# ምስጋና

የዚህን መጽሐፍ ረቂቅ ያዘጋጀሁት ኮምፒዩተር የመጠቀም ዕድል በሌለበት የእስር ቤት ቆይታዬ ነው። ለራሴ ደግሜ ለማንበብ የሚቸግረኝን የእጅ ጽሑፌን ሳይሰለች በኮምፒዩተር የተየበልኝ በና አብዱ ትልቅ ምስጋና ይገባዋል። ዚያድ አብዱሌ የአፋን ኦሮሞ የሆሄያት እና የሰዋሰው ግድፈቶችን ባያስተካክላቸው ኖሮ ይህ ጽሑፍ ለዚህ ባልበቃ ነበር። ከፍ ያለ ምስጋና ይድረሰው! በና እና ዚያድ በቁሮ ትግል ውስጥ ተሳታፊ እንደመሆናቸው የረሳሁትን አስታውሰው፣ የተሳሳትኩትን አርመው መጽሐፉ ከዳር እንዲደርስ አድርገዋል። ጽሑፉን በትንሽ በትንሹ በድብቅ አሾልከው ሲያስወጡ የነበሩ ለጉዳት ሊጋለጡ ስለሚችሉ፣ ስማቸውን መጥቀስ የማልፈልጋቸው ሰዎች ፈጣሪ ያክብርልኝ። ሬድዋን አማን ሾልኮ ሲወጣ የነበረው ጽሑፍ አንድ ላይ ተሰብስቦ እና ተቀናጅቶ በና እና ዚያድ ጋር እንዲደርስ ባያደርግ ረቂቁ ተበታትኖ ይቀር ነበር። የሬድዋን ድርሻ ይህ ብቻ አልነበረም። በዚያ አስቸጋሪ ጊዜ ቤተሰቤን ታድጎ፣ የሚያስፈልጋቸውን ሁሉ አሟልቶ በመንከባከብ ሊደርስብኝ ይችል የነበረውን ጫና እንዲቃለል ሰላደረገ ውለታው ተነግሮ አያልቅም። በትግሉ ውጣውረድ አንዴም ያልተለዩኝ የልብ ጉደኞቼና የትግል አጋሮቼ ኤሊያስ ኢብሳ እና መሀመድ አብዶሽ የሰኬቱ ሁሉ ባለደርሻ ሰለሆኑ ምሰጋናዬን በቃላቶች መግልጽ ያቅተኛል።

መጽሐፉን ከአፋን ኦሮሞ ወደ አማርኛ የተረጎመው ሁሴን ቱሉ እና ለሳምንታት መደበኛ ሥራዋን አቋርጣ የአርትዖት ሥራውን የሠራችው ማኀደር አካሉ ላቅ ያለ ምስጋና ይገባቸዋል። ኢብራሂም አብዱልዓዚዝ፣ ግዛው ለገሠ፣ አክመል ነጋሽ እና ሚካኤል ጨቡድ ማሞ ረቂቁን በማንበብ የማሻሻል ሥራ (proof read) በማከናወን ላደረጉት አገዛ ፈጣሪ ብድሩን ይክፈላቸው። ይሀ መጽሐፍ ታትሞ ለሕዝብ እንዲቀርብ ዘወትር ለወተወቱኝና ለህትመቱ አሰፈላጊውን የገንዘብ ድጋፍ ላደርጉ ሁሉ አላህ ባላቸው ላይ ይጨምርላቸው። በአጠቃላይ ይህን መጽሐፍ ለሕዝብ እንዳደርስ የረዱኝ ሰዎች ብዙ ናቸውና አንድ በአንድ ለመዘርዘር ስለማልችል ሁሉንም አመሰግናለሁ።

**ማውጫ**


| | |
|---|---|
| **መቅድም** | **1** |
| **ክፍል አንድ - ልጅነት** | 4 |
| 1.1. ውልደት | 4 |
| 1.2. የሰላሌው ተፈናቃይ፤ በአርሲ ቱጃር | 9 |
| 1.3. አመጸኛው አባ | 15 |
| 1.4. ጁሙጋ | 19 |
| 1.5. የሸጎዬ ምሽቶች | 21 |
| 1.6. ጁሙጋ እና የኦሮሞ ትግል | 25 |
| **ክፍል ሁለት - ከፖለቲካ ትውውቅ** | 27 |
| 2.1. ነገረ ኦሮሞ | 27 |
| 2.2. ኦነግን ለመጀመሪያ ጊዜ ያየሁት | 29 |
| 2.3. ሀምቢሳ እና ማንጁስ | 32 |
| 2.4. የአርባጉጉ ጦርነት | 34 |
| 2.5. የመጀመሪያዋ አመጽ | 37 |
| **ክፍል ሦስት - የሀገር ውሰጥ ስደት** | 42 |
| 3.1. አሰላ | 42 |
| 3.2. የፍቅር ወላፈን | 47 |
| 3.3. የመጀመሪያው እስር | 49 |
| 3.4. አዳማ፤ የከተማ አክቲቪስት | 50 |
| 3.5. ከአባዱላ ጋር በአንድ አዳራሽ | 54 |
| 3.6. «የኦነግ አባል እንድትሆኑ ተወሰኗል!» | 57 |
| **ትውሰታ በምስል** #1 | **61** |
| **ክፍል አራት - ውጭ ሀገር** | **65** |
| 4.1. ሲንጋፖርን ፍለጋ | 65 |
| 4.2. ሰሜኑን ብቻ ያየንበት የሀገርህን እወቅ ጉዞ | 69 |
| 4.3. ሕልም እና እንግሊዘኛ | 71 |
| 4.4. እውቀት እና ብልሀት ያበለፀጋት ሚጢጢ ሀገር | 73 |
| 4.5. የዩናይትድ ዎርልድ ኮሌጅ ተማሪ | 77 |
| 4.6. ዝንጉርጉሯ እሰያ | 81 |
| 4.7. ከተማሪነት ወደ ወጣት አመራርነት ጉዞ | 86 |

**ክፍል ስምስት - ዲያሰፓራ** 90
5.1. አሜሪካ 90
5.2. የጥቀር ሕዝቦች ታሪክ ጥናት እና የኦባማ ምርጫ 95
5.3. ሦሰቱ የሕንድ ዴሞክራሲ አባቶች 98
5.4. ወጣቶችን ማደራጀት 100
5.5. "Ethiopia Out of Oromia" 104
5.6. በኦሮሞ ጥናት ማህበር መድረክ ላይ 106
5.7. የኦነግ ትችት 112
5.8. ጋብቻ 120
**ትውስታ በምስል** #2 **125**
**ክፍል ስድስት - ዝግጅት** **131**
6.1. የሰሳማዊ ትግል ጥናት 131
6.2. ስትራቴጂ እቅደ ዝግጅት 143
6.3. የሀይማኖት ጉዳይ 151
6.4. ድምጻችን ይሰማ 158
6.5. የሀይማኖት እና የብሔር መብት ትግል፡ ተመጋጋቢ ወይስ ተገዳዳሪ? 163
6.6. የ 'Oromo First' ዘመቻ 170
6.7. OMN 179
6.8. ቃልን በተግባር 190
6.9. የትግል ወቅት ጉዞ፤ ገጠመኞች 198
**ክፍል ሰባት - ትግል እና ድል** 204
7.1. ሙከራ አንድ፡ #BoycottBedele 204
7.2. ቄሮ 208
7.3. የአንጃዎችን ጥቀት መቋቋም 210
7.4. ማስተር ፕላን 215
7.5. ፈተና 223
7.6. ታላቁ ሰልፍ 225
7.7. ማርሽ መቀየር 230
7.8. የኢሬቻ ፍጅት እና የአምሰት ቀናት ቁጣ ዘመቻ 233
7.9. ኮማንድ ፖስት ያላዳነው ውድቀት 238
7.10. የለውጡ ዋዜማ ድርድሮች 243
7.11. ልውጡን ማን ይምራው? 251
**ትውሰታ በምስል #3** 259

**ክፍል ስምንት - ለውጡን የማዳን ሙከራ** **264**
8.1. ጉዞ ወደ ሀገር ቤት 264

8.2. የሰሳም ጥረት ጅማሮ 272
8.3.የሶማሴ እና የኦሮሞ እርቅ 276
8.4.የብሔር ብሔረሰቦችን ትግል መደገፍ 283
8.5. ሰላም ለኦሮሚያ 287
8.6.የሰላም ጥረቱ ተግዳሮት 279
8.7.የኦሮሞ አመራር መማክርት 307
**ክፍል ዘጠኝ - የለውጡ መንሸራተት** **311**
9.1. የእኔ እና የመንግሥት ግንኙነት ከድጡ ወደ ማጡ 311
9.2.ጥቃት 316
9.3.ይፋዊ ልዩነት 320
9.4.ወደ ፓለቲካ ፓርቲ መቀላቀል 323
9.5.ሀገር አልባ 329
9.6.የኮሮና ቫይረስ እና ምርጫ 331
**ትውስታ በምሰል #4** **333**
**ክፍል አስር - ረጅሙ አረፍት** **345**
10.1. የሀጫሉ መገደል 345
10.2.እስር 353
10.3.ቃሊቲ 358
10.4.የፍርድ ቤት ሂደት 361
10.5.የረሃበ አድማ 365
10.6.የትግራይ ጦርነት 373
**ክፍል አስራ አንድ - ከእስር ቤት መልስ** 382
11.1 ከእስር መፈታት 382
11.2.ከተፈታሁ በኋላ 385
11.3.የሰላም ሰባኪ 389
11.4 ከዉጪ ማኅበረሰብ ጋር የተደረገ ውይይት 391
**ትውስታ በምሰል** #5 **396**
**እንደ መውጫ** 409

# መቅድም

የዚህ መጽሐፍ ረቂቅ የተጠነሰሰው እስር ቤት ውስጥ እንደመሆኑ ረገድ አንድጽፍ ያነሳሱኝ ሁለት ምክንያቶች ነበሩ። በመጀመሪያ ከዚያ ወህኒቤትበሕይወት እተርፋለሁ ብዬ ስላላሰብኩ፣ ከተሳተፍኩበት የትግል ጉዞ የማስታውሰውን ያክል ለቀጣዩ ትውልድ በጽሑፍ መዝገቤ ለማኖር ነው። ሁለተኛው ምክንያት ደግሞ አንዲት ቀን አንኳ የዓመት ያህል የምትረዝምበትን የእስር ቤት የቆይታ ጊዜ በሥራ በመጠመድ ለማሳጠር እና ለመቋቋም ነበር። ስለሆነም በታሰርኩ በጥቂት ቀናት ውስጥ ወረቀት እና እስክሪብቶ እንዲፈቀድልኝ የእስር ቤቱን ኃላፊዎች ጠየኩ። አምቢ ተባልኩ። እንደ ዕድል ሆኖ እነሱን ስጠይቃቸው የተመለከተ አንድ ፖሊስ በድብቅ አስገብቶልኝ መጻፍ ጀመርኩ። በምሥጢር ከሥር ከሥር ወደ ውጪ ማውጣትን ተያያዝኩት። ወደ ቃሊቲ እስር ቤት ከተወሰድን በኋላ ግን ወደ ውጪ ማስወጣት የተከለከለ ቢሆንም መጻፍ ስለተፈቀደ ያለሐሳብ ገፋሁበት። ከሥር ከሥር በድብቅ አያስወጣሁ ከእጅ ጽሑፍ ወደ ኮምፒዩተር ተቀየረ።

ከእስር እንደተፈታሁ መጽሐፉን ለማሳተም አስቤ ነበር። ነገር ግን አንባቢዎች በሰከነ መንፈስ እንዲመለከቱት ሰለፈለኩ፣ የተረጋጋ ጊዜ እሰኪመጣ መጠበቁን መረጥኩ። በተጨማሪም በወቅቱ ከነበረው የጦርነት ፖለቲካ አንጻር መጽሐፉ ውስጥ የማነሳቸው ጉዳዮች የበለጠ ውዝግብ እንዳይፈጥሩ ማቆየቱ አሰፈላጊ መስሎ ታየኝ። ብዙ ብጠብቅም፡ የተመኘሁት ዓይነት የተረጋጋ ጊዜ ሊመጣ አልቻለም። ሰዎችም በተለያየ ሁኔታና መንገድ አሳትመው አያሉ ስለወተወቱኝ አሁን ለማሳተም ወሰንኩ።

አስር ቤት ውሰጥ ዋቢ ማስረጃዎችን ማግኘት አስቸጋሪ ስለነበር፣በአእምሮዬ ጓዳ ተቀርጸው ከነበሩና ከትዝታ ማኅደሬ የተገኙትን ለማስፈር ተገደድኩ። ከእስር ከተፈታሁ በኋላ ያሉትን ማሰረጃዎች ከትውሰታዎቼ ጋር በማሰናሰል በተቻለ መጠን ለማስማማት ሞክሪያለሁ። እንዲሁም በተለያየ ወቅት አብረን የነበርን ሰዎችን በማጠያየቅ ጽሑፉን ለማዳበር ጥረት አድርጌያለሁ። በትግል ወቅት በጽሑፍ የያዝኳቸው ማሰታወሻዎች ስታሰር ከቤት ተወሰደው በመጥፋታቸው ልጠቀምባቸው አልቻልኩም። በዚሀ መጽሐፍ ውስጥ በመርሳትም ሆነ በስሕተት የፃፍኩት ነገር ካለ የምታስታውሱ ሰዎች እንደምታርሙኝ ተሰፋ አደርጋለሁ።

ፖለቲካ ብዙ ሰዎችን የሚያሳትፍ የጋራ ሥራ እንጂ፣ አንድ ሰው ብቻውን የሚያልፍበት ታሪክ ሰላልሆነ፣ እነዚያ ተሳታፊ ሰዎች ትላንት አብረው ያለፉባቸውን ክስተቶች በተመሳሳይ ሁኔታ ላያስታውሱ ይችላሉ። ሰለሆነም የአንድ ሰው ትውስታ ምሉዕ እና ሚዛናዊ ታሪክ ላይሆን ይችላል። በዚህ መሠረት፡ በመጽሐፉ ያሰፈርኳቸውን ሁነቶች ያሰታወስኩበትም ሆነ

የተገነዘብኩበት ሁኔታ ሙሉ በሙሉ ትክክል ነው የሚል እምነት የለኝም። ይልቁንም ክስተቶቹ እና ውሳኔዎቹ ብዙ ሰዎች እና ቡድኖች የተሳተፉባቸው ስለሆኑ፣ እኔ ካስታወስኩበት ወይም ከተረዳሁበት በተለየ መልኩ ሊያስታውሱ ወይም ሊረዷቸው ይችላሉ። እነዚያ ሰዎች አና ቡድኖች ትውስታቸውን እና ግንዛቤያቸውን ሰንደው ለሕዝቡ ካቀረቡ፣አንባቢዎች አመዛዝነው የተሻለ ግንዛቤ ሊጨብጡ ይችላሉ የሚል ተሰፋ አለኝ።

በመጽሐፉ ምዕራፎች ውስጥ የሰፈሩት ትንታኔዎች እና አመለካከቶች ኹነቶቹ በተፈጸሙበት ጊዜ የነበረኝን የፖለቲካ ግንዛቤ ያንጸባርቃሉ። ከዚያ ወዲህ ተጨማሪ መረጃዎችን በማግኘት፣ የፖለቲካው ሁኔታ በመቀየሩ፣ እንዲሁም በዕድሜ ከመብሰል ጋር ተያይዞ፣ የእኔም ሆነ የሌሎች ሰዎች እና ቡድኖች አመለካከት ሊለወጥ ይችላል። ሰለዚህ አንባቢያን፣ በመጽሐፉ የተገለጹትን ሐሳቦች እና ምልከታዎች ክስተቱ የተፈጸመበትን ጊዜ እና ሁናቴ ክግንዛቤ በማስገባት እንድታነቧቸው ከወዲሁ አደራ ለማለት አወዳለሁ።

መጽሐፉ በግለ ታሪክ (Memoir) መልክ የተዘጋጀ ነው። የወላጆቼን የጀርባ ታሪክ፣ አንዲሁም በልጅነቴ ወቅት በተወለድኩበት አካባቢ የነበሩ ፓለቲካዊ፣ ኢኮኖሚያዊ እና ማኅበራዊ ኹነቶች፣ ኋላ ላይ ላዳበርኩት የፖለቲካ አመለካከት ተጽዕኖ ስላላቸው፤ አንባቢው የወሰድኩትን አቋም እና ውሳኔዎቼን የበለጠ አንዲገነዘብ ይጠቅማል በሚል እሳቤ በመጽሐፉ የመጀመሪያ ክፍሎች ውሰጥ አጠር አድርጌ ለመዳሰስ መርጫለሁ። በቀጣይ ክፍሎች በሀገር ውስጥ አና በውጭ ሀገር በነበረኝ የትምሀርት እና የጉዞ ልምድ የቀሰምኳቸውን ግንዛቤዎች በማቅረብ በሂደት ላዳበርኩት የፖለቲካ አመለካከት ያበረከቱትን አሰተዋጽዖ ለመጠቆም ሞክሬያለሁ። የመጨረሻዎቹ ክፍሎች ወደ ቀጥታ የፖለቲካ ትግል ከገባሁ ጀምሮ ያደረኳቸው አንቅስቃሴዎች የሚቀርቡበት ነው። በመደምደሚያው ክፍል ያሳለፍኩትን የፖለቲካ ጉዞ መለስ ብዬ በመገምገም፣ በቀጣይ ሊከናወኑ ይገባሉ ብዬ ያሰብኳቸውን ሥራዎች አጠር አድርጌ ለመጠቆም የሞከርኩበት ነው።

መጽሐፉ መጀመሪያ በአፋን ኦሮሞ የተጻፈ ሰለሆነ፣ በአማርኛ ሲቀርብ ለአንባቢያን ግንዛቤ እንዲረዳ በማሰብ ከቃል በቃል ትርጉም (literal translation) ይልቅ ዐውዳዊ (contextual) ትርጉም መጠቀም ተመርጧል። የተወሰነው የአማርኛ አንባቢ የኦሮሞን ውስጣዊ ትርክት (narrative) በቅርበት ላይከታተል ስለሚችል፣ አንዳንድ ጉዳዮች ላይ የአማርኛው ቅጂ ከአፋን ኦሮሞው ዘርዘር ያለ ገለጻ ተጨምሮለታል።

ብዙዎቹ ክንዋኔዎች በውጭ ሀገር ሳለሁ የተፈፀሙ አንደመሆናቸው፣ አንዲሁም ከአንዳንድ ሁነቶች ይዘት አና ባሕርይ አንጻር፣ በመጽሐፉ ላይ ሁለቱም የኢትዮጵያ አና የጎርጎሮሳውያን የቀን አቆጣጠሮች አንደ አግባቡ ጥቅም ላይ ውለዋል። ሆኖም ብዥታን ለማስቀረት፣ በጎርጎሮሳውያን አቆጣጠር ለተቀመጡ ቀናት ብዙውን ጊዜ እንደተለመደው፣ አንደ አውሮፓውያን አቆጣጠር መጠቀሳቸውን ለመጠቆም "እ.አ.አ" የሚለውን በመጨመር ግልጽ ለማድረግ ተሞክሯል።

በመጽሐፉ ውሰጥ በአብዛኛው የሰዎችን ስም ላለመጥቀሰ መርጫለሁ። ግለሰቡ የተሳተፈበት ጉዳይ አስቀድሞ በሕዝብ የታወቀ ካልሆነ፣ ታሪኩ የግለሰቡን አዎንታዊ ገጽታ የሚያሳይ ካልሆነ፡ ስም ካልተጠቀሰ ከፍተኛ ክፍተት የሚፈጠር መስሎ ካልታየኝ በስተቀር ስሞችን ለለማካተት ወስኛለሁ። ይህን ያደረኩት በመጽሐፉ የተካተቱ ክሰተቶች ያለፉ ቢሆኑም

ውጤታቸው በዛሬው ፖለቲካ ላይም ተጽዕኖ ሊኖረው ስለሚችል እና ግለሰቦቹ አሁን ካሉበት የፖለቲካ አሰላለፍ አንጻር ለነቀፌታ እንዳያጋልጣቸው በመስጋት ነው። ሆኖም ግን ስሞቹን በማስታወሻ የመዘገብኳቸው ስለሆነ ወደፊት የዛሬው የፖለቲካ ትኩሳት ሲያልፍ እኔ ወይም ሌላ ጸሐፊ ይፋ እንደሚያደርጋቸው ተስፋ አደርጋለሁ።

# ክፍል አንድ - ልጅነት

## 1.1. ውልደት

በኦሮሞ ባሕል አንድ ሰው የትውልድ ሐረጉን ቢያንስ እስከ ሰባት መቁጠር ይጠበቅበታል። የኔም ጀዋር ሲራጅ ሙሐመድ ቱፋ ጂሎ ኦብሴ ጎዳና ኬቶ ቦነያ ቢላ እና ጋቲሮ… እያለ ይቀጥላል። ለነገሩ ከቅድመ አያት በኋላ ያሉትን ያወቅኩት አሁን በቅርብ ነው፣ እሱንም በልጄ አስገዳጅነት። የዘር ሐረጋችን በልጅነታችን እየተነገረን እንድንሸመድድ ይደረግ የነበረ ቢሆንም እኔ ግን ዘንግቼው ቆይቻለሁ።

እስር ቤት እያለሁ አንድ ቀን ልጄ ኦሮሞ ይሀን የዘር ሐረግ የመቁጠር ጉዳይ ሰምቶ ኖሯል፣ በሰልክ እያናገርኩት ድንገት ሲጠይቀኝ ከየት ላምጣው? “አላውቅም” ለማለት አፈርኩና በአፌ ላይ የመጡ ስሞችን ደረደርኩለት። «ድገምልኝ› ሲለኝ ደገምኩለት። የዘሙኑ ልጆች ነገር ሆኖ፣ ለካ ከአፌ ላይ እየለቀመ እናቱን ሲያጽፋት ነበር። መጀመሪያ የነገርኩትን እና ሁለተኛ የደገምኩትን አነጻጽሮ "አቦ! ስሕተት አለው" ብሎ ለሦስተኛ ጊዜ እንድደግምለት አፋጠጠኝ። ለሦስተኛ ጊዜ መያዝ አልፈለኩም። “እችኩላለሁ” በማለት ስልኩን ዘጋሁት። ወዲያውም አህቴ አጎታችንን አፈላልጋ የዘራችንን ሐረግ የስም ዝርዝር በአስቸኳይ እንድትጠይቀው ላኪት። እሷም ከእርሱ የተነገራትን ጽፋ አምጥታልኝ በሳምንታዊው የስልክ ቀጠሯችን ደግሜ ደጋግሜ በኩራት የዘራችንን ሐረግ ለልጄ ዘረዘርኩለት። እሱም ሸምድዶ በሳምንቱ ደገመልኝ።

የትውልድ ዘመኔን እና ትክክለኛውን የተወለድኩበትን ሰፍራ ያወቅኩት ወደ ሁለተኛ ደረጃ ት/ቤት ከመግባቴ ጥቂት ቀደም ብሎ ነው። የስምንተኛ ክፍል ብሔራዊ ፈተና (ሚኒስትሪ) ለመውሰድ እየተዘጋጀን በነበረበት ወቅት፣ ትምህርት ቤታችን የልደት ማስረጃ እንድናመጣ አዘዘን። ወደኋላ ላይ በማብራራው ምክንያት፣ ከሰምንተኛ ክፍል በፊት የነበሩ የትምህርት ማስረጃዎች ስላልነበሩኝ ማመሳከር አልቻልኩም። ለመንፈቅ ዓመት ዕረፍት ወደ እናቴ ዘመዶች ቀዬ ሄጄ አያቴ ሙሉ በዳኔን (የእናቴ እናት) ሳወራት የተወለድኩበት ቀን የግንቦት አቦ አንደ ነገ ሊውል በዋዜማው ሌሊቱን መሆኑን ነገረችኝ። አጎቴ ኃይሌ ቶላ ደግሞ ዘመኑ

በ1978 ዓ.ም መሆኑን አሳወቀኝ። በዚሀም መሠረት ከሁለቱ ያገኘሁትን መረጃ አገጣጥሜ ግንቦት 4/1978 ዓ.ምን የተወለድኩበት ቀን አድርጌ ትምሀርት ቤት አስመዘገብኩ።

የውጪ ትምሀርት ዕድል በማግኘቴ ወደ ሲንጋፖር ለመሄድ ፓሰፖርት ማውጣት ነበረብኝ። የትውልድ ቀኔ በጎርጎሮሳውያን አቆጣጠርም አብሮ መጻፍ አለበት ተባለ።ፎርም የሚያስሞላው ወጣት ልጅ ቀኑን፣ ወሩን፣ ዓመተ ምሕረቱንም ስምንት እንድጨምርበት በመከረኝ መሠረት፣

በፈረንጆች አቆጣጠር ሜይ 12 ቀን 1986 የትውልድ ቀኔ ሆኖ ተመዘገበልኝ። አሁን ሰዎች የሚያውቁትና በየዓመቱ የማኅበራዊ ሚዲያ ገጾች ላይ “Happy Birthday" እያሉ መልካም ምኞታቸውን የሚገልጹልኝ በዚሁ ዕለት ነው።

በነገራችን ላይ ሲንጋፖር እስክሄድ ድረስ እንደ አብዛኛው ገጠር ተወላጅ ኢትዮጵያዊ አንድም ቀን ልደቴን አክብሬ አላውቅም። አንድ ቀን ማለዳ ቁርሴን ልበላ ካፍቴሪያ ስገባ ጓደኞቼና መምህራኖቼ የመልካም ልደት ዜማ እያዜሙ ለልደቴ ያዘጋጁትን ኬክ አንድቆርስ ቢላዋ ሰጡኝ። 18ኛ ዓመት ልደቴ መሆኑ ነበር። አሁን ይህን መጽሐፍ ለማሳተም ስዘጋጅ 38ኛ ዓመት ልደቴን ያከበርኩ ቢሆንም፣ ውሰጤ ግን የዚያን እጥፍ ዓመታት የኖርኩ ያህል ይሰማኛል።

ልጅ እያለሁ የተወለድኩበት ቦታ፣ ያደኩበት የአርሲ ዞን ጎሎልቻ ወረዳ ይመስለኝ ነበር። አንድ ቀን ጎሎልቻ መወለዴን ለሰው ስናገር እናቴ ትሰማለች። ንግግሬን ወዲያው አቋርጣ በሰው ፊት ስሕተቴን ማረም አልመረጠችም። ታሪኬን ሳወጋው ከነበርኩት ሰው ጋር ከተለያየን በኋላ የተወለድኩበት ቦታ ጎሎልቻ ሳይሆን አስኮ ወረዳ፣ ዲማ ቀበሌ፣ ሰኞ ገበያ እንደሆነ ነገረችኝ። ያቺ ሰኞ ገበያ በስፋት «ጂኒ» ተብላ ትታወቃለች። እዚያ መወለዴ አዲስ ይሁንብኝ እንጂ ጂኒ ስለሚባለው ቦታ ቀድሞውንም አውቃለሁ። «ጂኒ» የሚለው መጠሪያ ለአካባቢው የተሰጠው ፏፏቴ ከሚያፈልቅ አንድ የዋሻ ሰም በመነሳት ነው።

በልጅነቴ ወደ እናቴ ቤተሰቦች ሰፈር ስንሄድ በዚሁ ፏፏቴ በኩል አናልፋለን። ፏፏቴው ጋር እንደደረስን ከሸለቆው በአንደኛው ጎን ቆመን ስንጣራ፤ ትንሽ ቆይቶ ድምጻችን በሌላኛው በኩል ይሰማል። ትዕይንቱ ሌላ ተመሳሳይ ድምፅ ያለው ሰው ከማዶ ሆኖ መልስ የሚሰጥ ይመስል ነበር።

ሁሌም ደስ ስለሚለን ደጋግመን እየተጣራን እንጫወታለን። ከማዶ ተመልሶ ሲያስተጋባ የሚሰማው ድምፅ «ጂኒ (ጋኔን) ነው» ተብሎ ይታመን ስለነበር «የጂኒ ዋሻ› ስያሜው ሆነ። ሰኞን ጠብቃ በምትውለው የገበያ ቦታ የተቆረቆረችው ትንሽዬ ከተማም ከዚሁ ፏፏቴ አጠገብ ስለነበረች «ጂኒ» ተባለች።

ጂኒ ከተማ ተወልጄ ከጥቂት ጊዜ በኋላ ወደ ጎሎልቻ ወረዳ፣ ጩሉል ጭርቅሳ ተወሰድኩ። የተወለድኩበት እና ቀጥሎ የተወሰድኩበት ስፍራዎች ጎን ለጎን ያሉ ወረዳዎች ቢሆኑም በጣም የተራራቀ የአየር ፀባይ አላቸው። የተወለድኩበት አካባቢ ለጥ ያለ ሜዳ፣ ሁሌም ዝናብ የማያጣው በጣም ብርዳማ (ደጋማ) ስፍራ ነው። በአካባቢው ገብስ፣ ስንዴ፣ ተልባ፣ ድንች፣ ባቄላ እና አተር በከፍተኛ ሁኔታ ይመረታል።

በተቃራኒው ያደኩበት የጎሎልቻ ወረዳ ቆላማ ነው። ከጂኒ ተነሰታችሁ በእግር ለሁለት ሰዓት ወደ ምሥራቅ አቅጣጫ ስትሄዱ ምድር ተሰነጠቀች ከሚያስብል ግዙፍ ገደል ጋር ትገጣጠማላችሁ። በገደሉ ጫፍ ላይ ቆማችሁ ቁልቁል ስትመለከቱ፣ የእርሻ ማሳ እና ቤቶች ከሩቁ ይታያሉ። ተራራውን ታከው ባሉ ቀጫጭን እና አስፈሪ መንገዶች ስትሄዱ ወደ ጎሎልቻ ወረዳ ትደርሳላችሁ። በየክረምቱ ሞልቶ ሰው የሚወሰደውን የደርባ ወንዝ እንደተሻገራችሁ ጩሉል ጭርቅሳ ቀበሌ እራሳችሁን ታገኛላችሁ። እዚሁ ጩሉል ጭርቅሳ ቀበሌ ውስጥ «ቡዮ» ተብላ የምትጠራው የአያቴ (የአባቴ አባት) ቀዬ አለች። ቡዮ ከላይ ተራራ፣ ከታች የደርባ ወንዝ፣ በግራ እና በቀኝ ትናንሽ ወንዞች በሚፈሱባቸው ሸለቆዎች ተከብባ ትንሽዬ ደሴት መሰላ ትታያለች። ትክክለኛ ሰሟ ቡዮ ቢሆንም፣ የቅርብና የሩቅ ዘመድ በአብዛኛው "የአባ ሲራጅ መንደር” እያለ ይጠራታል።

ወደ ቤተሰቦቼ ስሻገር አባቴ ሲራጅ ሙሐመድ ቱፋ ጂሎ ይባላል። አሁን በሕይወት የለም። እናቴ ሸምሲ ተላ ቡሊ ቡኔ ትባላለች። የትውልድ ሰሟ ፋንታዬ ነበር፡ ሸምሲ በኋላ የወጣላት ስም ነው። አሁን አዳማ እየኖረች ትገኛለች። አባቴ ጎሳው አርሲ ሲሆን፣ እናቴ ደግሞ ከቱለማ ጎሳ ናት። አባቴ የእስልምና እምነትን ሲከተል፣ እናቴ ከክርስቲያን ቤተሰብ ተወልዳ በኋላ ላይ እስልምናን ተቀብላለች። ወላጆቼ መጀመሪያ የተገናኙበት ሁኔታ፣ ኑሮ አመሠራረታቸው፣ ልጆች ያፈሩበት መንገድ ከኦሮሞ የትግል ታሪክ ጋር በእጅጉ የተቆራኘ፣ እንዲሁም በእኔ የፖለቲካ አመለካከት ላይም ተጽዕኖ ያሳደረ ሰለሆነ ትንሽ ዘርዘር አድርጌ ማቅረቡ የሚጠቅም ይመሰለኛል።

አባቴ በአርሲ ክፍለ ሀገር አርባጉጉ አውራጃ ጮሌ ወረዳ ከአባቱ ሙሐመድ ቱፋ እና ከእናቱ ወ/ሮ ሞሚና አደም ተወለደ። ጎሳው ግንዱ «ቢላ›› ከሚባል የአርሲ ጎሳ ይመዘዛል። በኦሮሞ የትውልድ ሐረግ መሰረት ኦሮሞ ሁለት ልጆች ነበሩት፣ ቦረና እና በሬንቱ። ቦረና ዘጠኝ፣ በሬንቱ አምስት ልጆች ወለዱ። አምስቱ የበሬንቱ ኦሮሞ ልጆች ከረዩ፣ መረዋ፣ ዱሙጋ፣ ሁምበና እና ቀሎ ይባላሉ። ዱሙጋ ደግሞ አርሲ፣ ሃዋሳ እና አሶሳ በሬንቱን አፈራ። አርሲ በተራው ሲኮ እና መንዶን ወለደ። ሲኮ አምስት ልጆች የነበሩት ሲሆን እነሱም ቡላላ፣ ዉጪሌ፣ ዋጂ፣ ጃዊ አና ኢላኒ ናቸው። የኔ ጎሳ ቢላ የሚባል ሲሆን የቡላላ ቅርንጫፍ ነው። ከዚሀ አንጻር የዘር ሐረጌ ጀዋር ሲራጅ ሙሐመድ ቱፋ ጂሎ «ቢላ›› ቡላላ ሲኮ አርሲ ዱሙጋ በሬንቶ ኦሮሞ ይሆናል ማለት ነው።

የአርሲ ዱሙጋ በሬንቶ ኦሮሞ ቅርንጫፍ ጎሳዎች በአብዛኛው በዋቤ ወንዝ ወዲያ እና ወዲህ የሚኖሩ ሲሆን፣ ከዋቤ ወዲያ ማዶ ያለው መሬታቸው ባሌ፣ ከወዲህ ያለው ደግሞ ዲደዓ በመባል ይጠራል። የመንዶ አርሲ ንዑስ ጎሳዎች በአብዛኛው በባሌ፣ ሲኮዎች ደግሞ ዲደዓ ይኖራሉ። እኔም ትውልዴ በአባቴ በኩል በጎሳ ከሲኮ አርሲ ቅርንጫፍ፣ በቀዬ ደግሞ ዲደዓ ነው። አያቴ ከተወለደበት የጮሌ ደጋማ ሰፍራ ለቆ ወደ ቆላማው ጎሎልቻ የሄደበት ምክንያት ከደረሰበት መገፋት ጋር ይያያዛል። ጣሊያን ኢትዮጵያን ለቅቃ ወጥታ የኃይለሥለሴ መንግሥት ወደ ዙፋኑ እንደተመለሰ፣ የፊውዳሉ ሥርዓት በአዲሰ መልክ መልሶ አንሰራራ። መንግሥት አዳዲስ ሰፋሪዎችን በማምጣት ከሀገሬው ላይ መሬት እየነጠቀ በመስጠቱ የመሬት እጥረት ተከሰተ። የአያቴ መሬት ተቆርሶ ሰለተወሰደበት ከእርቦና ሲሶ በሚተርፈው ምርት ቤተሰቡን ማሰተዳደር ተሳነው። ሰፋ ያለ መሬት ለማፈላለግ ከበረሃማው ጎሎልቻ ወረዳ ተሰድዶ ጬሉል ጬርቅሳ መንደር በሚገኝ ቡዮ የተባለ ቦታ ላይ ሰፈረ። ጠፍ የሆነ ለም መሬት ቀናውና የተቀሩ ቤተሰቦቹንም አምጥቶ የራሳቸውን ሰፈር መሠረቱ።

አባቴን አባዬ እያልን እንጠራዋለን። ጮሌ ተወልዶ ከአባ (ከአያቴ) ጋር ወደ ጎሎልቻ ሄደ። እድሜው ከፍ ሲል መድረሳ (የእስልምና ሀይማኖታዊ ትምህርት ቤት) እዚያው እንዲገባ ተደረገ። በመማር ላይ እያለ ራቅ ባለ የወረዳው አካባቢ ዘመናዊ ትምሀርት ቤት ሲከፈት ሄዶ ተመዘገበ። ትምሀርት ቤቱ አራተኛ ክፍል ላይ ስለሚያቆም፣ ከዚያ በላይ ለመማር ወደ ሌላ ስፍራ መሄድ ነበረበት። በተጨማሪም አንድ ሰው ትምህርት ለመመዝገብ “ሀይማኖቱን እና ስሙን መቀየር አለበት” ስለተባለ አባቱ (አያቴ ) አሻፈረኝ ብለው፣ ዘመናዊ ትምህርቱን አቋርጦ ሀይማኖታዊ ትምህርት እንዲቀጥል ወደ ሐረርጌ ላኩት።

1 በኃይለሥላሴ ዘመነ መንግሥት የኦሮሞ ወይም የውስሊም ስም ያላቸው ዜጎች ትምህርት ለመመዝገብ ስማቸውን እንዲቀይሩ የሚገደዱባቸው ሁኔታዎች በስፋት ነበሩ።

በዚያ ዘመን ወጣቶች ከአርሲ፣ባሌ፣ወሎ እና ጂማ ሀይማኖታዊ ትምህርት ለመከታተል ስመጥር ሼይኾች ወደሚገኙበት ሐረርጌ ይጎርፉ ነበር። እነዚህ ወጣቶች ትምህርታቸውን ተከታትለው ሲመለሱ የወጡበትን ማኅበረሰብ እንዲያስተምሩ ይደረጋሉ። ተሰፋ እንደተደረገውም ከእነዚህ ወጣቶች ውስጥ የተወሰኑት ሀይማኖታዊ ትምህርታቸውን በደንብ ቀስመው በመመለስ ማኅረሰባቸውን ማገልገል ቻሉ። ሌሎቹ ሐረርጌ በምትታወቅበት ንግድ እና ማኅበራዊ ኑሮ ተማርከው፣ ንግድ ውስጥ ገብተው፡ ጎጆ ቀልሰው እና ልጆች ወልደው እዚያው ቀሩ።

አባቴ ሀይማኖታዊ ትምህርቱን ካጋመሰ በኋላ የልብስ ስፌት ጥበብን ተማረ። እንደሱ የቁርኣን ትምህርት ካቋረጡ ደረሶች ጋር በመሆን ሐረርጌ እና አርሲ ድንበር ላይ በምትገኘው ዱሙጋ የተባለች ትንሽዬ ከተማ በመክተም ልብሰ ስፌት እና ንግድ ሥራ ላይ ተሰማራ። ወደ ሐረርጌ፣ ባሌ አልፎም ኦጋዴን ድረስ መነገድ በጀመረበት ከዕለታት በአንዱ ቀን ቤተሰብ ጥየቃ ወደ አባቱ ቀዬ ሲመለስ ወጥመድ ተዘጋጅቶ ጠበቀው።

አባቱ የቁርኣን ትምህርቱን አንደተወ ሲሰሙ፣ እሱን ወደ ቀዬው የሚመልሱበትን ዘዴ ያውጠነጥኑ ጀመር። በዚህም መሠረት በጠና አንደታመሙና ሊሞቱ እያጣጣሩ መሆኑን ለአባቴ መልዕክት ላኩበት። አባቴም በድንጋጤ አየከነፈ ከቀዬው ተመለሰ። ሀገር ሰላም ብሎ ሮጦ ቤት ሲገባ ፣ አያቴ የሀገር ሽማግሌዎችን ሰብስበው ጠበቁት። የተሰባሰቡት ሽማግሌዎች አባቴ እግር ላይ ወድቀው መፈናፈኛ አሳጡት። አባቴ እየተካሄደ ያለው ነገር አልገባውም። እሱ "አባቴ ሳይሞት ደርሼ ዓይኑን ልየው" ብሎ ከመጨነቅ ውጪ የተደገሰለትን አልተረዳም ነበር።

እንደ አካባቢው ባሕል አንድ ወጣት በአካልም ሆነ በአእምሮ ተረጋግቶ አንዲቀመጥ ከተፈለገ ሚሰት ይዳራል። "ለትዳር የደረሰን ወጣት ማሰሪያው ሚሰት ነው" የሚባለውም ለዚህ ነው። አያቴም በዚሁ ዘዴ በመጠቀም ለሀይማኖት ትምህርት ሐረርጌ የሄደውን እና ትምህርቱን ከዳር ሳያደርስ ወደ ንግድ ገብቶ ሰው ሀገር የቀረውን አባቴን ወደ ቀዬው መለሱት። ዘመድ አዝማድ እግሩ ላይ ወድቆ ስለለመነው አባቴ የአያቴን እቅድ አሻፈረኝ የሚልበት ዕድል አልነበረውም።

ለአባቴ የታሰበችው ኮረዳ ከአካባቢው ባሕል አና ልማድ ጋር የምትጣጣም አልነበረችም፣፡ ጎሳዋ አርሲ አይደለም። ቤተሰቦቿ በአካባቢው ገና አዲስ የሰፈሩ እንግዶች ሲሆኑ ሀይማኖታቸውም እስልምና አልነበረም። በአካባቢው የሚኖሩ ክርስቲያኖች ቢኖሩም፣ ከዚያ በፊት የሀይማኖት ድንበር ተሻግሮ ጋብቻ መፈጸም ያልተለመደ አዲስ ክስተት ነበር።

አያቴ ለልጁ ያሰባት ኮረዳ ፋንታዬ ቶላ ትባላለች። የትውልድ ሀረጓ በአባቷ በኩል ቶላ ቡሊ ቡኔ ቆሪቻ ነሞ ሳኖኦ ሄበኖ ባቡ-ጉምቢቹ ኦበ ዳጪ ቱለማ በረና ኦሮሞ ነው። በእናቷ ደግሞ ሙሉ በዳኔ ቱፋ ኢርኮ ዳዉ አቸን- አቢቹ ኢላሞ ዶዮ ጂዳ ገላን ዳጪ ቱለማ በረና ኦሮሞ ይሆናል። ከሸዋ ክፍለ ሀገር፣ ሰላሌ አውራጃ አቢቹ ወረዳ ዴኮ ከሚባል አከባቢ ተፈናቅለው ወደ አርሲ እንደመጡ ይናገራሉ። የቶላ ቡሊ ታላቅ ወንድም ገመቹ የቤተሰቡ አንጋፋ አና አሥተዳዳሪ ነበር። ገመቹ ጣሊያን ኢትዮጵያን በወረረችበት ዘመን አምጸው ለአምስት ዓመታት ከተዋጉት አርበኞች ውስጥ አንዱ ሲሆን፣ አጎቱን ጨምሮ ብዙ ሰዎች በዚያ ጦርነት ተሰውተዋል።

በጣሊያን ላይ የተደረገው አመጽ በአብዛኛው መሀል ኦሮሚያ/ሸዋ ውስጥ የተካሄደ ነው። አያቴ ሲናገር እንደሰማሁት፣ የአጼ ኃይለሥላሴ ፊውዳላዊ ሥርዓት የሀገሬውን ሕዝብ መሬት ቀምቶ ጭሰኛ ስላደረገው፡ ጣሊያን መጀመሪያ ወደ ኢትዮጵያ ሲመጣ፣ የዚያ አካባቢ ኦሮሞዎች እንደበጎ ለውጥ ወሰዱት። ብዙም ሳይቆይ ጣሊያኖች ከንጉሱ ባለሟሎች የተረከቡትን መሬት

«ባንዳ›› ሆነው ላገለገሏቸው ብቻ መርጠው አከፋፈሉ። በተጨማሪም አምጸው ጫካ የገቡ የንጉሥ ባለሥልጣናት በአብዛኛው በዚሁ አካባቢ ይንቀሳቀሱ ስለነበር፣ "ለእነሱ እርዳታ ታደርጋላችሁ" በሚል ጥርጣሬ ጣሊያን ሕዝቡን ማንገላታት ጀመረ። በዚህም ምክንያት ቀድሞ በጣሊያን የተደሰተው ሕዝብ አኩርፎ አመጸ። እንደ ገረሱ ዱኪ ያሉ የነፃነት ታጋዮች ብዙ ሺህ ጦር አደራጅተው ከኋላቸው በማሰለፍ እና በመዋጋት ታላቅ ዝናን ተቀዳጁ።

## ፲፪.የሰላሌው ተፈናቃይ፤ በአርሲ ቱጃር

ጣሊያን አመጹን ለማጥፋት በሕዝቡ ላይ አሠቃቂ ዕልቂት ፈጸመ። ለአምስት ዓመታት ከተደረገ ውጊያ በኋላ ጣሊያን ከሀገር ሲወጣ፣ አጼ ኃይለሥላሴ ከተሰደዱበት እንግሊዝ ተመልሰው መንበረ ሥልጣኑን ዳግም ተቆናጠጡ። የንጉሡ መመለስ ለገመቹ ቡሊ እና ከእርሱ ጋር ጣሊያን ላይ አምጸው ለተፋለሙ አርበኞች ጥሩ ነገር ይዞ የመጣ አልነበረም። ለሀገራቸው ለዋሉት ውለታ ዕጣቸው ሽልማት እና ክብር መሆን ሲገባው፣ በደል ተፈጸመባቸው። ንጉሡ ወደ ሀገር ተመልሰው ብዙም ሳይቆዩ "መሬቱ ለዘመናዊ እርሻ ይፈለጋል" በሚል ሰበብ ለጋሻ ጃግሬዎቻቸው እና ለባለሀብቶች ታደለ።

አስገራሚው ነገር መሬት ከተሰጣቸው ውስጥ አብዛኛዎቹ ፋሺስት ጣሊያን ሀገርን በወረራ ስትይዝ፣ሀገር ጥለው የሸሹት ናቸው። በኦሮሚያ አንዳንድ ቦታዎች አሁንም ድረስ "የስደተኛ ሰፈር "ተብለው የሚጠሩ አካባቢዎች አሉ። እነዚህ ለጣሊያን በባንዳነት አድረው፣ ወራሪዋን ሲያገለግሉ ቆይተው መሬት የታደላቸው ሰዎች ሰፈሮች ናቸው። በሀገራቸው ውስጥ ከወራሪዋ ጣሊያን ጋር ተናንቀው ለነጻነት መሥዋዕትነት የከፈሉት ግን ውለታቸው ተጨማሪ የእርሻ መሬት ማግኘት ሳይሆን ያላቸውንም መነጠቅ ሆነ። ከአባቶቻቸው የወረሱትን መሬት በደም እና በአጥንታቸው ከጠላት ሲከላከሉ እንዳልቆዩ፣ ተፈናቅለው በገዛ መሬታቸው ላይ ለጭሰኝነት ተዳረጉ። ከእርቦ አና ሢሶ የተረፈችው ምርት ቤተሰባቸውን ለመመገብ አልበቃችም። ሮሮው ከቀን ቀን እየበረታባቸው ሲመጣ እና ይደርስባቸው የነበረውን መከራ መሸከም ሲያቅታቸው ከአካባቢያቸው ለመሰደድ ተገደዱ።

በጣሊያን ዘመን ገመቹ ቡሊ ሐጂ ቃሲም ከሚባሉ የአርሲ ሰው ጋር ተዋወቀ። መሬቱን ሲነጠቅ አርሲ ሄዶ ሐጂ ቃሲምን ሲያማክራቸው በአርሲ በቂ ጠፍ መሬት ሰላለ መጥቶ እንዲያርስ ጋበዙት። ገመቹም ወደ ሸዋ ተመልሶ ቤተሰቡን በማስከተል ወደ አርሲ ተሰደደ። ለወትሮውም በእግር ተጉዞ አርሲ ለመድረስ ረጅም ጊዜ ይፈጃል። ጉዞው አረጋውያን፣ ነፍሰጡር ሴቶች፣ ሕጻናት እና የቤት እንስሳትን ይዘው ሲሆን ደግሞ በእጥፍ ይጨምራል። ከእንስሳቶቹ መሀል ገሚሱ ጉዞ ላይ አለቁ። መንገድ ላይ ደክመው የሞቱ ሕጻናትም እንደነበሩ ይነገራል። ከዚያ አስቸጋሪ የስደት ጉዞ በኋላ፣ አርሲ ደርሰው አሰኮና ጉና ወረዳ ድንበር አቅራቢያ ዲማ የተባለ አካባቢ ደረሱ።

አርሲዎች ቃል በገቡት መሠረት እነገመቹን መሬት ሰጥተው አሰፈሯቸው። ገመቹና ቤተሰቡ ከአካባቢው ማኅበረሰብ ጋር በፍጥነት ጠንካራ ትስስር መሠረቱ። በዚያን ጊዜ እነሱ የሰፈሩበት አካባቢ የአርሲ ጎሳ ኦሮሞዎች እና "ቡልጌ/መንዜ" በመባል የሚታወቁ የአማራ ማኅበረሰብ ክፍሎች ነበሩ። አማራዎች መስፈር የጀመሩት የምኒሊክ ጦር በአካባቢው ከደረሰበት ጊዜ ጀምሮ ነው። ከዚያ በኃላ በታው እንደ መንዝ፣ ምንጃር እና ቡልጋ ላሉ የሸዋ አካባቢዎች ካለው ቅርበት የተነሳ ብዙ አማራዎች ወደተለያዩ የአርሲ ዞን ወረዳዎች ፈልሰዋል። በዚህም ምክንያት በአካባቢው ያሉ የአማራ ማኅበረሰብ "ቡልጌ ወይም መንዜ "ተብለው ይጠራሉ።

ከሰላሌ የመጡ ኦሮሞዎች፣ በአርሲ ኦሮሞዎች እና በቡልጌ አማራዎች መካከል ሰፈሩ። እነሱ ወደ አካባቢው ከመድረሳቸው በፊት የቡልጌ አማራዎች እና የአርሲ ኦሮሞዎች እንደ ዘይት እና ውኃ ብዙም ሳይቀላቀሉ ይኖሩ ነበር ይባላል። አማራዎች ለእርሻ አመቺ የሆነው ተራራማ መሬት በመንግሥት ተሰጥቷቸው በእርሻ ሲተዳደሩ፤ አርሲዎች ቆላማ እና ወይናደጋማ የሆነውን መሬት ይዘው በእርሻ እና ከብት ማርባት ሥራ ይኖሩ ነበር። በሁለቱ መሀል በስንደዶ የተሸፈነ ለማረስም ሆነ ለእንስሳት ግጦሽ ብዙ አመቺ ያልሆነ ሰፊ ሜዳ ነበር። ከሰላሌ የመጡት ኦሮሞዎች እዚህ መሬት ላይ ሰፈሩ። ገመቹ እና ወንድሞቹ ይህንን ስንደዶ በበሬ እና በእጃቸው በመታገዝ ነቅለው ጋይ ከምረው በማቃጠል ገብስ፣ ስንዴ እና ባቄላ ዘርተው ሀገር "አጃዒብ" ያስባለ ምርት መሰብሰብ ጀመሩ። ገመቹም ትልቅ ባለሀብት ለመሆን በቃ፣ በአጭር ጊዜም ከፍተኛ ምርትና የከብት ባለቤትነት ስመጥር ገበሬ ሆነ።

በአርሲ ኦሮሞዎች ባሕል ሠላሳ ጊደሮች በአንድ ጊዜ የተወለዱለት ሰው ባለጸጋ ሀብታም ተብሎ ይሞገሳል። እዚሀ ደረጃ የደረሰ ገበሬ፣ የሀብቱን መጠን ለማሳየት ኪላ መግባት (kiila lixuu) የተባለ ሥርዓት ያከናውናል። ኪላ ሊጡ ማለት ከብቶቹ ከመብዛታቸው የተነሳ ሠላሳ ጊደሮች በአንድ ጊዜ የተወለዱለት ሰው ትልቅ ጉድጓድ ተቆፍሮ በእንገር ( ገና በወለደች የጊደር ወተት) ከተሞላ በኋላ ሀብታሙን ሰው እዚያ ውስጥ የመባረክ ሥርዓት ነው። በዚህ ሥርዓት ውሰጥ ያለፈ ሰው "እከሌ ኪላ የገባ የናጠጠ ሀብታም ነው" ተብሉ ይነገርለታል። በዚህ ሁኔታ የቡሊ ቡኔ ልጆች ከስላሌ ተሰደው፣ ቤተሰባቸው ላይ የደረሰውን ከፍተኛ በደል ተቋቁመው፣ በመጨረሻ ግን የተደላደለ አዲስ ሕይወት በአዲሰ አካባቢ መመሥረት ቻሉ።

ከላይ እንደጠቀስኩት፣ በዚያ አካባቢ የአርሲ ኦሮሞዎች ብቻ ሳይሆኑ የአማራ ወገኖችም በብዛት ይኖሩ ነበር። ሁለቱ ማኅበረሰቦች የምኒሊክ ጦር ያንን ቦታ በኃይል ካስገበረበት ጊዜ ጀምሮ አብረው የኖሩ ቢሆንም፣ በአሰፋፈርም ሆነ በማኅበራዊ ኑሮ ብዙም ሳይቀላቀሉ ጎን ለጎን ሲኖሩ ቆይተዋል። ለዚሀ መራራቅ አንዱ ምክንያት የሀይማኖት ልዩነት ነው። አርሲዎች የእስልምና፤ ቡልጌዎች የኦርቶዶክስ ሀይማኖት ተከታዮች ናቸው። ነገር ግን ለዚያ ማኅበራዊ መራራቅ ሀይማኖት ብቸኛው ምክንያት አልነበረም።

በምኒሊክ ወረራ ጊዜ አሠቃቂ ጭፍጨፋ ከተካሄደባቸው ቦታዎች አርሲ ዋነኛው እንደነበር ታሪክ በስፋት ያትታል። በጦርነቱ ምክንያት የተፈናቀለው የአርሲ ኦሮሞ ገሚሱ ወደ ደጋማ፤ የተቀረው ወደ ቆላማ ቦታዎች በመሰደድ ሰፍሯል። በጦርነቱ ወቅትም ሆነ ከዚያ በኋላ የመጡ አማራዎች ሜዳማ አካባቢዎች ላይ ሰፈሩ። ጦርነቱን ተከትሎ የተመሠረተው መንግሥታዊ አሥተዳደር ግን ብሔር ተኮር መድሎዎችን የሚፈጽም በመሆኑ፣ በጦርነቱ የተፈጠረው ጠባሳ እንዳይሽር አድርጎ ለማኅበራዊ መቀራረብ እንቅፋት ሆነ።

ከስላሌ የመጡት የእናቴ ወገኖች ያረፉት በአሰፋፈርም፣ በማኅበራዊ ሁኔታም በሁለቱ መካከል ነበር።ሁለቱም ወገኖች የማይጠቀሙትን ስንደዷማ መሬት ከመያዝ ባለፈ፣ከአርሲ ኦሮሞዎች ጋር ቋንቋ እና ባሕል፣ ከአማራ ቡልጌዎች ጋር ደግሞ ሀይማኖት ሰለሚጋሩ በሁለቱም በኩል ትስስር መፍጠር ቻሉ። በዚህ ሁኔታ ውስጥ እያሉ የቶላ የበኩር ልጅ ፋንታዬ ታማ በሕይወት እና በሞት መካከል ሆና፣ አጎቷ ገመቹ ሞራ አንብቦ ስለታየው2 አዮ ሞሚና የሚባሉ የጸሎት ሰውጋር እንድትወሰድ አዘዘ።

2 ሞራ ማየት በኦሮሞ ባሕል ውስጥ እንስሳት ሲታረዱ ሞራቸውን ማንባብ ሰዎች ስለገጠማቸው የጤና እክል፣ የቀጣዩ አዝመራ የዝናብ ሁኔታ ወዘተ መተንበይ የተለመደ ነው። ሞራውን የሚያነቡት ተሰጥዖ እና እውቀት ያላቸው ሰዎች ናቸዉ።

አዮ ሞሚና ታዋቂ ባለውቃቢ (ayyaantuu) ሲሆኑ "ፈጣሪን በመለመን ከተለያዩ ችግሮች ይፈውሳሉ" ተብሎ በአካባቢው ማኅበረሰብ ሰለሚታመን፣ የሁሉም ሀይማኖት እና ብሔር አባላት ወደ እሳቸው የጸሎት ስፍራ ይጎርፉ ነበር። አዮ ሞሚና የዘር ሐረጋቸው ከወሎ የእስልምና እምነት ዐዋቂዎች (ዓሊሞች) ቀዬ እንደሆነ ይነገራል። በአጼ ዮሐንስ ዘመነ-መንግሥት ወሎ ውሰጥ ይካሄድ በነበረ የብሔር እና የሀይማኖት ጭቆና፣ በብዛት ወደ ሐረርጌ ከተሰደዱ የሀይማኖት ምሁራን እና ቤተሰቦቻቸው መሀል አንዷ ናቸው ይባላል።

የትውልድ ስማቸው ኡበሺ ኡመር ሲሆን ሞሚና የሚለው ስም ሐረርጌ ውስጥ እንደተሰጣቸው ይነገራል። በጨርጨር (ምዕራብ ሐረርጌ) አካባቢ ሼኽ አሊ ጃሚ የተባሉ ዓሊም ሲካድሙ (ሲያገለግሉ) ቆይተው ሼኹ በሞት አፋፍ ላይ ሆነው ሲያጣጥሩ፣ እሙት ሞሚና ከሰጡት አገልግሎት በመነሳት "ከራማ"ውን ሰጥተዋቸው "ወደ አርሲ ሂጂና ሕዝቡን አገልግዪ " ብለው እንደሸኛቸው በአካባቢው ይታመናል። እሙት ሞሚናም የተወሰነ ቡድን አስከትለው፣ የአርሲ ዞን አሰኮ ወረዳን አቆራርጠው፣ መርቲ እና ጉና ወረዳዎች ውስጥ መስጂድ ቀልሰው ሰፈሩ። በጉና ወረዳ መስጂድ የተሰራበት ቦታ ገነቴ ሲባል በመርቲ ወረዳ ደግሞ ፈረቀሳ ተብሎ ይታወቃል። የአዮ ሞሚና ሙስሊም መሆን የሁሉም ሀይማኖት ተከታዮች ወደ እሳቸው ዘንድ ከመሄድ አላገዳቸውም። አዮ ሞሚና በ1929 ዓ.ም ሲያርፉ ልጆቻቸው የፈረቀሳን እና የጉናን "ከራማ" ወርሰው የሕይወት ዘይቤያቸውን ቀጠሉበት።3

ፋንታዬ ቶላ በጣም ታማ ሌላ ቦታ መዳን ሲያቅታት ወደ ፈረቀሳ ወስደዋት ከበሽታዋ አገገመች። ከተሻለት በኋላ ስላሰለሟት ስሟ ከፋንታዬ ወደ ሽምሲ ተቀየረ። በወቅቱ ሙሐመድ ቱፋ ከነገመቹ ቡሊ ጋር የጠበቀ ወዳጅነት ፈጥረዋል። የሀይማኖት ትምህርት (ቁርኣን) ትቶ ወደ ንግድ የገባውን ልጃቸውን ወደ ቀዬው የሚመልሱበትን መላ እያወጡ እያወረዱ ቆይተው፣የቶላ ቡሊ ልጅ መስለሟን ሲሰሙ እሷን ሊያጬለት ወሰኑ። ከላይ እንደገለጽኩት፣ «ታምሜያለሁ፣ በነፍሴ ድረስ» ብለው ልጃቸውን ወደቀዬው ከመለሱት በኋላ፣ በሀገር ሽማግሌ አስገድደው ሽምሲን እንዲያገባት አደረጉ።

እናቴ ዘምዘም የተባለች የመጀመሪያ ልጅ ወለደች፣ በዓመቱ ሌላ ሴት ልጅ ደገመች። ሁለት ሴቶች ተከታትለው መወለዳቸውን ቀልባቸው አልወደደውም። የሲራጅ አባትም ከሲራጅ በሰተቀር ሌሎች ልጆቻቸው ሴቶች ስለሆኑ፣ ወንድ የልጅ ልጅ ለማግኘት ታለቅ ጉጉት ነበራቸው። ተፈላጊውን ወንድ ልጅ ለማግኘትም አባቴ ሌላ ሚስት በእናቴ ላይ ደርቦ አግብቶ ቢሞክርም አዲሷም ሚስቱ ሴት ወለደች። እናቴ አሁንም ሦሰተኛ ሴት ልጅ ወለደች፣ አባቴ ተጨማሪ ቢያገባም ውጤቱ ያው ሆነ። ይባስ ብሎ እናቴ አራተኛ ሴት ልጅ ደገመች። በዚህ "እድለቢሥነቷ" ያዘነችው እናቴ በአካባቢው ባሕል መሠረት ለሼኽ ሁሴን ተሳለች። "ፈጣሪ ሆይ፣ ቀጥሎ የምወልደውን ልጅ ወንድ አድርግልኝ፤ ወንድ ልጅ ካልሆነ ግን አምጥቼ በቀዬህ (ድሬ ሼኽ ሁሴን) እጥላለሁ" ብላ በዛቻ ተማጸነች። ሼኽ ሁሴን በ13ኛው ክፍለ ዘመን ባሌ ውስጥ ይኖሩ የነበሩ ታዋቂ የእስልምና ወልይ ናቸው። እርሳቸው በኖሩበት ቦታ ከበርካታ ዞኖች የተውጣጣ ሕዝብ አሁንም ድረስ ለጸሎት ወደ ሙዳ ይሄዳል።

እናቴ ነፍሰጡር ሆና ከሼኽ ሁሴን ዚያራ የሚመለስ አንድ ሰው ጎራ ብሎ በሆዷ ያዘለችው ፅንስ

3 Geda, Gemechu Jemal. The Faraqasa Indigeneous pilgrimage center. History and Ritual Practices,2007.

ወንድ መሆኑን በሕልሙ እንዳየ ነገራት። ለሚወለደውም ልጅ ከምንም ምግብ በፊት "ይህን ጀዋረ አጉርሺው" በማለት ከድሬ ሼኽ ሁሴን ይዞት የመጣውን ቋጠሮ ሰጣት። የልጁንም ስም ሙሐመድ ጅዋር ብዬ ሰይሜዋለሁ አላት። ጀዋረ ማለት ወደ ሼኽ ሁሴን ለሙዳ (መንፈሳዊ ጉዞ) የሚሄዱ ሰዎች ይዘው የሚመጡት ጥቁር አፈር ወይም አመድ ቢሆን ሕመምተኛን ለመፈወስ የሚበላ እና የሚቀባ ነው። በኦርቶዶክስ ክርስትና «እምነት» ከሚባለው የሚቀባ ነገር ጋር ተመሳሳይ ነው።

እንደተባለውም እናቴ አምስተኛ ላይ ወንድ ልጅ ወለደች። ያንን ጀዋረ አጎረሱኝ፡ ስሜንም ሙሐመድ ጀዋር ብለው ሰየሙኝ። ትምህርት ቤት ስመዘገብ መምህራኖቹ ሙሐመድን ጀዋር በሚለው አሳጠሩት። እናቴ ከእኔ በኋላ ሁለት ሴቶችን ብትወልድም ወንድ ልጅ ግን መድገም አልቻለችም። አባቴ ግን እናቴ እኔን ነፍሰጡር ሆና ካገባት ሚስቱ አሚን የተባለ ሌላ ወንድ ልጅ ወለደ። እኔም ወንድሙን አስከትሎ የመጣ ገዳም ('ዳ' ጠብቆ) ልጅ ተባልኩ።

ዕድሜዬ ለትምህርት ባይደርሰም ታላላቆቼ ት/ቤት ሲገቡ ከእነሱ ላለመነጠል ስል አልቅሼ ሳልመዘገብ ት/ቤት ገባሁ። አስተማሪዎቹ የሚሰጠውን ትምህርት በደንብ እንደምረዳ ስላስተዋሉ፣ እንድቀጥልበት ተፈቀደልኝ። ከጥቂት ጊዜያት በኋላ የደርግ መንግሥት ወድቆ ት/ቤት ሲዘጋ አያቴ ጋር ሄጄ የሀይማኖት ትምህርት (መድረሳ) መማር ጀመርኩ። ሎዲ ወይም ሉሂ (ሉህ) በሚባል ከእንጨት የተጠረበ ዝርግ ጣውላ ላይ በጥላሸት በመጻፍ እንማር ነበር።

ጠዋት ምግብ መብላት ምላስ እንዲተሳሰር በማድረግ የቁርአን ንባብ ላይ ያስቸግራል ሰለሚባል ባዶ ሆዳችንን ወደ መድረሳ እንሄዳለን። በወቅቱ ቁርሴን ሳልበላ ወደ ቁርአን ቤት መሄድ በጣም ያናድደኝ ስለነበር፣ ሲነጋጋ ከአያቴ ቤት በመነሳት የቡዮን ወንዝ ተሻግሬ፣ በለስ ከቀናኝ ዘይቱን፣ ኮክ፣ አጋም፣ ቡሩሪ እና ዶቅማ የመሳሰሉትን ፍሬዎች ለቅሜ በልቼ እንዳይታወቅብኝ አፌን ተጉመጥሙጬ እና አደራርቄ ምንም እንዳልቀመስኩ ሆኜ ከመድረሳው እሰየማለሁ።

በወቅቱ ለወጉ ያሀል ሼኻ ጋር ትቀራላችሁ ብንባልም የሚያስሰተምሩን ግን ደረሶቹ ናቸው። ሼኹ ደረሶችን ያስቀራሉ፡ ደረሶቹ ደግሞ እኛን። ደረሶቹ ያነበቡትን ሸምድደው፣ በማግሰቱ መጽሐፉን ዘግተው ከእንደበታቸው ማንበብ ያቃታቸውን ተማሪዎች በአርጩሜ ይገርፋሉ።

እኔ የተሰጠንን ትምህርት በመሸምደድ ላይ ችግር አልነበረብኝም፣ ከሚያሰተምረን ደረሳ ጋርም ሰለምግባባ ብዙ ጊዜ አልገረፍም።

አንድ ቀን ግን ከእኛ ጋር የምትቀራ ልጅ ደረሳው ተማሪዎቹን ሊቀጣበት ያዘጋጀውን አርጩሜ እኔ የተቀመጥኩበት ስጋጃ (ምንጣፍ) ሥር ደብቃው ሲፈለግ እኔ ሥር ተገኘ። ደረሳው እኔ የደበቅኩት መስሎት በልጆቹ ፊት ሲገርፈኝ የሚያርፍብኝን የዱላ ናዳ መቋቋም አቃተኝ። በመሀል ጎንበስ ብዬ መሬቱን ስመለከት፣ አንድ ድንጋይ አየሁና አንስቼ ይቀጠቅጠኝ በነበረ ደረሳ ጭንቅላት ላይ ለቀኩት። ከመቅፅበት ከግንባሩ ደም ሲፈስ ሳይ ደንግጬ በሩጫ ከግቢው ወጣሁ ጥፋት ሰርቼ ወደ ቤት መመለስ ሰለፈራሁ ከገበያተኞች ጋር ወደ እናቴ ቤተሰቦች ቀዬ ለመሄድ የዲማን ዳገት ተያያዝኩት።

እነሱ ጋር ትንሽ እንደከረምኩ አባቴ ሊፈልገኝ መጣ። ወደ ቆላ ተመልሼ ሼኹ ጋር መቅራት እንደፈራሁ ስለገባው "የሚፈለገው መማሩ ሰለሆነ እዚያው እናንተው ጋር (የቄስ ት/ቤት) አስገቡት" አላቸው። ወዲያውም ከአክስቶቼ እና ከአጎቶቼ ልጆጭ ጋር የቄሰ ትምህርት አስጀመሩኝ። ከደረሳው የሸሸሁት ግርፊያ ግን የኔታ ጋርም አልቀረልኝም። ከዚህኛው

የምሸሽበት እንደሌለ ስለተረዳሁ ከየኔታ ጋር መወዳጀትን እንደ ስልት በመጠቀም ከመገረፍ አመለጥኩ።

የኔታ ከሌሎች ልጆች ጋር የሚያስተምሩንን በደንብ ከማጥናት ባለፈ፣ ሌሎች ንባቦችን እንዲያውሱኝና በትርፍ ጊዜያቸውም እንዲያስጠኑኝ አግባባኋቸው። መጀመሪያ ይህን ያደረኩት በጉብዝናዬ የኔታን በማስደሰት ከግርፊያ ለማምለጥ ነበር። በሂደት ግን ትምህርቱን እየወደድኩት መጣሁ። የቄስ ትምህርት ቤት መግባቴ በአጭር ጊዜ የአማርኛ ፊደል መጻፍ እና ማንበብ ከማስቻል አልፎ በአብዛኛው አማርኛ ብቻ ከሚናገሩ ልጆች ጋር መዋሌ ቋንቋውን በደንብ ማውራት እንድችል አገዘኝ። በሚዲያ ስናገር ብዙ ሰዎችን የሚያስገርመው የአማርኛ ቋንቋ ችሎታዬ መሠረትም ያ በልጅነቴ ከመድረሳ ሸሽቼ የተጋፈጥኩት የቄስ ትምህርት ቤት ነው።

በ1986 ዓ.ም ሀገር ተረጋግቶ ትምህርት ቤት ሲከፈት ወደ መደበኛ ትምህርት ተመለስኩ። ቁቤን በኦነግ ወታደሮች፣ የአማርኛ ፊደልን ቄስ ትምህርት ቤት በመማሬ የንባብ ችሎታዬ ጥሩ ሆኖ ተገኘ። በዚህም ክፍሎችን በመዝለል (ደብል በመምታት) ያባከንኩትን ዓመታት አካካስኩ።

የእናቴ ዘመዶች ጋር ለቄስ ትምህርት በቆየሁበት ጊዜና ከዚያ ወዲህም ስመላለስ፣ የሰላሌ/የቱለማ ኦሮሞን ባሕል ለመረዳት ዕድል ሰጥቶኛል። የኦርቶዶክስ ክርስትና ሁለት ትውልድ ቢያልፈውም፣ ነባሩን የኦሮሞ ሀይማኖት አልተዉም። ከክርስትና ጋር ቀላቅለው ያመልካሉ። ሴቶቹ የአቴቴ፤ ወንዶቹ ደግሞ በረንቲቻን የመሳሰሉ የአምልኮ ሥርዓቶችን ቀጥለውበት ነበር። በአቴቴ ዕለት ቄጤማ ተጎዝጉዞ፣እጣን ተጨሶ፣በቅቤ የተጥለቀለቀ ቂንጬ ቀርቦ፣ አያቴ ሙሉ በዳኔ ጨሌዋን አጥልቃ፣በቤተሰቡ ሴቶች ተከባ ፈጣሪን ትለምናለች። እኛ ወንዶቹ ደግሞ ጸሎቱ አልቆ ቂንጬው አሰኪሰጠን ሰፍ ብለን እንጠብቃለን። እናቴ እሰልምናን ብትቀበልም ከእናቷ የወረሰችውን የአቴቴ ሥርዓት እስካሁንም ቀጥላበታለች። አያቴ ጠዋት ጠዋት በሌሊት ተነሰታ ማርያምንም፣ የአያቶቿን አምላክም አየለመነች ትጸልያለች። አማርኛ ሰለማትችል በረጅሙ "እግዚኦ" ካለች በኋላ ዝርዝር ጸሎቷን በአፋን ኦሮሞ ትቀጥልበታለች።4

በረንቲቻ በዓመት አንዴ የሚከበር ሲሆን፣ በግ ታርዶ፣ ጠላና ድፎ ዳቦ ተዘጋጅቶ፣ ቤተሰብ በትልቅ ዛፍ (አድባር) ሥር ተሰብሰቦ አያታችን ፈጣሪን ይለምናል። ከተዘጋጀው ምግብ እና መጠጥ ሁሉ ላለፉት ቤተሰቦች ነፍስ ወርወር ካደርገ በኋላ ዳቦውን “በስመዓብ” ብሎ ይቆርስና ያከፋፍላል። እስካሁን በጣም የሚገርመኝ የበረንቲቻ ዕለት ጠዋት ከብቶች በጠዋት ከበረት ተለቀው ወደ ሜዳ ሄደው ይግጣሉ። ነገር ግን እንደወትሮው እረኞች አያግዷቸውም። አድርሰዋቸው ወደ አድባሩ ቦታ ይሄዳሉ። ፀሐይ ሞቅ ብላ ቤተሰብ ተሰብስቦ የበረንቲቻው ሥርዓት ሊጀመር ሲል፣ ከብቶቹ በማንም ሳይነዱ መጥተው በአድባሩ ዙሪያ ይተኛሉ። እንዴት ሊመጡ እንደቻሉ አያቴን ሰጠይቅ፣ "የበረንቲቻ መንፈስ” እንደሳባቸው ይነግረኝ ነበር።

የክርስትና በዓላትን ሲያከብሩም ከነባሩ አምልኳቸው ጋር ደባልቀው ነው። ለምሳሌ ደመራን

4 ወደ ኋላ ላይ የኦርቶዶክሰ እምነት ተከታይ የሆኑ ኦሮሞዎች በቋንቋቸው እንዲገለገሉ ሲደረግ የነበረውን ትግል የደገፍኩበት እንዱ ምክንያት አያቴ አማርኛ ባለመቻሏ በኑዛዜ ወቅት የሚደርስባትን መሳቀቅ ስለማውቅ ነበር፡፡ ኑዛዜ በቄሱ እና በተናዛዥ መካከል ብቻ ሊሆን የሚገባው ምሥጢራዊ ተግባር ሆኖ ሳለ፣ አያቴና ሌሎች አማርኛ የማይችሉ ሰዎች በአስተርጓሚ መናዘዝ ግድ ሆነባቸው፡፡ ቤተክርስቲያን በቋንቋቸው ማገልገሏ ይህን ችግር ለመፍታት በጣም አሰፈላጊ ነው፡፡

እና መስቀልን ከኢሬቻ ጋር ቀላቅለው ያከብራሉ። ገብርዔል ሲነግስ የቀይ ቡሃ፤ ማርያም ስትነግስ ደግሞ የጥቁር ቡሃ በግ ይታረዳል። ቤተክርስቲያኑን ገመቹ ቡሊ እና ጓደኞቹ ስላሰሩት[5] ነው መሰለኝ የዓመቱ ጊዮርጊስ ከጥምቀት ባልተናነሰ በሬዎች ታርደው በድምቀት ይከበራል። እነዚህ በዓላት ሲከበሩ እንዲሁም የማኅበር ጽዋ ሲጠጣ በቤት ውስጥ የሚደረገው ጸሎት ጊዮርጊስንም፤ የእናት የአባታቸውንም አምላክ አከታትሎ በመለምን ይካሄዳል። ስለትም ቢሆን ለማርያም፤ ለሃደ አበዪም (Haadha Abbayyii) እኩል ይሳላሉ።

ይሀ ነባሩን የኦሮሞ አምልኮ ኋላ ከተቀበሉት ሃይምኖት ጋር ቀላቅሎ ማካሄድ በክርስቲያን ዘመዶቼ ብቻ የተገደበ ሳይሆን በሙስሊሞቹም የተለመደ ነበር። ለምሳሌ የእስልምና ከሆኑት ሰላት እና ጾም በተጓዳኝ የዋቄፈና የሆነው የቡነ ቀላ ሥነ-ሥርዓት ይከናወናል። በቡነ ቀላ ወቅት ጀንፈል ቡና ተፈልቶ በነጠረ ቅቤ ተቀቅሎ በቆሪ ይቀርብና፣ አያቴ እየመረቀን ቅቤውን ግንባራችን ላይ እየቀባ ቡናውን ያጎርሰናል። በምርቃቱ ውስጥ አላህንም የአባቶቹን ከራማም እያከታተለ ይለምንልናል። ለነገሩ በድሬ ሼኽ ሁሴንም ሆነ በፈረቀሳ (አዩ ሞሚና) የሚከናወኑ የጸሎት ክንዋኔዎች እስልምናን እና ዋቄፈናን ያካተቱ ናቸው።

የነብዩ ሙሐመድ ልደት በዓል የሆነው መውሊድ ሲከበርም ቢሆን የሚዘመረው መንዙማ ከቁርኣን እና ከሐዲስ ስንኞች በተጨማሪ የጎሳዎችን አያና (መንፈስ) ማሞገሰን ያካትታል። ከመውሊድ በዓል ትዝ የሚለኝ ማታ እራት ሲቀርብ ለልጆች ለብቻቸው ገንፎ በጥልቅ ቆሪ ይሰጣል። በዕድሜ ከፍ፣ በጉልበትም ፈርጠም ያሉት ቆሪውን አንስተው ጨለም ወዳለ ቦታ በመውሰድ አንድንበላ ይጋብዙናል። ማንኪያ ሰለማይዳረሰ በእጃችን መብላት ነበረብንና እጃችንን ሰንሰድ ትላልቆቹ በጥፍራቸው ይቧጭሩናል። እጃችንን አውጥተን ሕመሙን አስታግሰን መልሰን ስንሰድ ገንፎው አልቋል። በኋለ እንደተረዳሁት ልጆች ለዚህ የገንፎ ሽሚያ ሲሉ መውሊድ ሲቃረብ ጥፍራቸውን ያሰድጉ ነበር።

5 በሸዋ አካባቢ ኦሮሞ ውሰጥ ሀብት የቀናው ሰው ቤተክርስቲያን ማሰራት የክብር ምልክት ነው። ከዚህ በተጨማሪም አያቶቼ አርሲ ከመድረሳቸው በፊት ቤተክርስቲያን ሰርተው የነበሩ አማሮች፣ አዲስ መጪዎቹን አድሏዊ እና ክብር በሚነሳ መልኩ ያሰተናግዷቸው ሰለነበር፣ በሰፈሩበት ተደላድለው ሀብት ከአፈሩ (ጠብቆ) በኂላ ወደ ሸዋ ተመልሰው ታቦት እና ቄሰ በማምጣት ጊዮርጊስ ቤተክርስቲያን ከፍ ያለ ኮረብታ ላይ አሰሩ።

# 1.3. አመጸኛው አባ

አባቴ ከታሰረ በኋላ በሁለቱ አያቶቼ ቤት መካከል እየተመላለስኩ መኖር ጀምርኩ። ለነገሩ ከዚያ በፊትም ቢሆን ብዙ ጊዜዬን የምኖረው እነሱ ጋር ነበር። አያቶቼ ጋር መኖሬ ስለኦሮሞ ሕዝብ ባሕል ያለኝ ግንዛቤ እንዲዳብር ረድቶኛል። የአባቴ አባት የሆኑትን ሙሐመድ ቱፋን አባ ብለን እንጠራቸዋለን፤ በጓደኞቻቸው ዘንድ ማሞ በመባል ይታወቃሉ፤ የአካባቢው ሰው አባሲራጅ ይላቸዋል። አባ እና ጓደኛቹ በእኔ ዕድሜ ያሉ ልጆችን እንደ ዕድሜያቸው እና ተሰጥዖዋቸው በመገምገም ከሰፈር ሽማግሌዎች ሥር መደቡን።

ምደባው ሁለት ዓላማዎች ሲኖሩት፣ ቀዳሚው እንድንላላክላቸው ቢሆንም፣ ዋናው ግን በእነሱ ምክር ታንጸን ባሕሪያችንን እንድናርቅና ክህሎታችንን እንድናዳብር ነበር። ለምሳሌ ከአፈር እና ከጭቃ ቁስ መሥራት የሚችሉ ልጆች የአጅ ሥራ ባለሞያ የሆነ ሽማግሌ ጋር እንዲውሉ ይደረጋል። እፅዋት የመንከባከብ ዝንባሌ ያላቸው ልጆች ደግሞ የአትክልት እና ፍራፍሬ ዝርያ በመትከል የሚታወቁ ሽማግሌ ጋር ይመበሉ። እኔን ከመጀመሪያውም የመናገር ተሰጥዖ አለው ብለው ስላመኑ «ደኔ›› በመናገር የሚታወቁ አንድ ሽማግሌ ጋር መደቡኝ።

ሽማግሌዎች ደኔ በሚያወሩበት ወቅት ቁጭ ብለን እንድናዳምጥ ይደረጋል። ንግግሩ ካለቀ በኋላ በቦታው ከተወራው ነገር ይጠይቁናል። ለምሳሌ በዚያ ንግግር ውስጥ ምሳሌያዊ አነጋገር ከተነገረ ማን እንደተናገረው እንጠየቃለን። አያቴ ከሌሎች ሽማግሌዎች ንግግር እንድማር አመቻቹልኝ እንጂ፣ እሳቸው ግን ብዙም ንግግር የሚወዱ ሰው አልነበሩም። በደኔ ሥርዓት ወቅትም ማዳመጥ እንጂ መናገር አይችሉም። ጠንካራ እና ምግባረ ቀና ገበሬ ስለነበሩ፣ ካረጁ በኋላ እንኳን ቀኑን ሙሉ የሚውሉት ቡና ማሳ ውስጥ ነው ፤በጣም ቁጡ ስለሆኑ ንግግር ይሸሻሉ።

የአባ ንግግሮች እና ድርጊቶች እስካሁንም ይገርሙኛል። አንዱ በዱዓ (ጸሎት) ላይ የነበራቸው አቋም ነው። ሁሌ ጠዋት ጠዋት ከአንድ የዋርካ ግንድ ሥር ቁጭ ብለው ማሳውን ቁልቁል እያማተሩ፣ ትንሽዬ ጫት ለኢጀ - በና (ዓይን መግለጫ) የመያዝ ልምድ ነበራቸው፤ ለወጉ እንጂ ብዙ አይቅሙም። የእሳቸው ሱስ ድቅቅ ብሎ ተፈጭቶ በአፍንጫ የሚሳብ ሱረት እና ትምባሆ ናቸው። የጎረቤት ሰዎችና አላፊ መንገደኞች ወደ አባ ሲራጅ ጫያ (ጥላ) ጎራ ብለው ቡና መጠጣት የዘወትር ልማዳቸው ነበር።

በባሕሉ ቡና ተፈልቶ ሊቀዳ ሲል ቡና የምታፈላዋ ሴት «ከአጀባ› በማለት ከሽማግሌዎች አንዱ ዱአ እንዲያደርጉ ትጋብዛለች። እንግዳ ካለ በወጉ መሠረት ባለቤቱ ዱዓ አያደርግም። ታዲያ ከአባ ሲራጅ ጫያ ሥር ለጠዋት ቡና የታደመ ሰው ዱዓ ሲያደርግ ካስረዘመ አባ ቶሎ ያስቆሙታል። «የጠዋት ጸሎት አጭር መሆን አለበት፤ ፈጣሪ ሆይ፤ በሰላም ያሳደርከኝ በሰላም

6 ''ደኔ'' ማለት ሰው ሲጣላ፣ ሲጋባ እና ሲሞት ሽማግሌዎች በሁለት ወገን ተቀምጠው እየተቀባበሉ የሚናገሩበት ሥርዓት ነው። ወደ ምዕራብ አርሲ አካባቢ «ኮቱዱፌ» ተብሎም ይታወቃል።

አውለኝ፤ ከተባለ በቂ ነ ው›› በማለት የጠዋት ምክርና ተግሳጽ መስጠት ይጀምራሉ። «ሰው የሚችለውን ፈጽሞ፣ ላልቻለው ነው ፈጣሪን መለመን ያለበት ፈጣሪ ሙሉና ጤነኛ አካላት ሰጥቶሃል፤ የምታይበትን ዓይኖች፣ የምትራመድበትን እግሮችና የምትቆፍርበትን እጆች ችሮሃል። በተሰጠህ ሠርተህበት፣ ባልቻልከው ፈጣሪን ትለምናለህ» በማለት ምክራቸውን ይቀጥላሉ። ከዋርካው ጥላ ዝቅ ብሎ ካለው ማሳ ቁልቁል በጣታቸው እየጠቆሙ «ለምሳሌ ፈጣሪ ያንን መሬት ፈጥሮ እሷ ላይ አሰፈረኝ። እኔ ደግሞ መሬቱን አርሼ ከዘራሁ በኋላ፣ ፈጣሪ ሆይ፤ ዝናቡን አዝንብልኝ ብዬ እጸልያለሁ እንጂ፣ ያልተነካ ባዶ መሬት ይዞ ፈጣሪን መለመን አይሆንም። ማረስ እና መዝራት የእኔ ኃላፊነት ሲሆን፣ ማዝነብ ደግሞ የፈጣሪ ድርሻ ነው» በማለት ቡናቸውን ተጎንጭተው፣ ምክራቸውን ለማሳረግ ጉሮሮዋቸውን ይስላሉ። «የእኔን ድርሻ ተወጥቼ ፈጣሪ ዝናብ እንዲያዘንብልኝ እና የዘራሁትን እንዲያበቅልልኝ እለምናለሁ። ቀኑን ሙሉ ጫት እያላመጡና ባዶ መሬት ወደታች እያዩ ፈጣሪን መለመን መሬቱን በማሳ አይሞላውም፤ ከድህነትም አያወጣም›› በማለት ምክራቸውን ይደመድማሉ።

ይህ የአያቴ አቋም እና አነጋገር ረጅም ጸሎት ማድረግ የሚወዱ ሼኾች እና ሽማግሌዎችን ማስቀየሙ አልቀረም። ሲናገሩ «የአርሲን ሥርዓት (adaba Arsii) የሚጥስ ሰው ተብለው ይወቀሱ ነበር። የአርሲ ማኅበረሰብ በተለይ ደገኛው በጣም ወግ አጥባቂ ነው። ከደጋ የሚመጡ ዘመዶቻችን «ነገሮችን አቅልሎ መናገር ከኖሌ ሰዎች ጋር ባለው ግንኙነት እና ጉርብትና ያዳበረው ነው› እያሉ አባን ያሟቸዋል። በእውነቱ ብዙ ጊዜ ደቦ የሚጠራሩት ከኖሌ ገበሬዎች ጋር ነበር፣ ከሚሰቶቻቸው መካከል አንዷ ከኖሌ ጎሳ ናት።

አባ የሆነ ነገር ታዝበው ካልተመቻቸው ወዲያው በቀጥታ እና በግልጽ ይናገራሉ። አንድ ቀን አዮ ዜይኒ (ሚስታቸው) ገን ፎ በትልቅ ቆሪ (የገንፎ ማቅረቢያ) አዘጋጅታ ማንኪያ ይዘን በቆሪው ዙሪያ ለመብላት ታደምን። ከመካከላችን አንድ ጎረምሳ ገንፎውን በማንኪያው በዛ አድርጎ ሊጎርስ ወደ አፉ ሲያስጠጋ፣ አባ የልጁን እጅ አፈፍ አድርገው ይዘው «ይሄን የደሀ ጭንቅላት የሚያክል ወዴት ልትወስደው ነው» ብለው ልጁን ኩም አደረጉት። ልጁም በኀፍረት ተሸማቆ ማዕዱን ትቶ ወጣ፡ በማግሰቱም የሰው ዓይን ማየት አፍሮ በማለዳ ከአካባቢው ጠፋ።

አያቴ ብዙ ሚስቶች በማግባት ይታወቃሉ፡ እሳቸው ባያምኑም እስከ 17 ሚሰቶች እንዳገቡ ይታማል። ብዙ ማግባት ብቻ ሳይሆን፣ የሚያገቡበትና የሚፈቱበት ታሪኮችም የሀገሬው መተረቻ ነበሩ። በአንድ ወቅት እንዲህ ሆነ ተብሎ ይነገራል፤

አባ አጎት የሚሆኑለት የሆነ ጎረምሳ አንዲትን ኮረዳ አይቶ ወደዳትና «ቤተሰቦቿን ጠይቅልኝ» ብሎ ሽምግልና ላካቸው አሉ። አባ ሽምግልና ሲሄዱ በልጅቷ ውበት ይማረካሉ። ወደ ቤታቸው ሲመለሱ ላኪውን ልጅ ጠርተው፣ «ልጅቷ አትሆንህም » ይሉታል። ልጁም «አጎቴ አትሆንህም ካለ ትቅር፤» ብሎ ተዋት። ከጥቂት ሳምንታት በኋላ አባ ሽማግሌዎችን ወደ ልጅቷ ቤተሰቦች ልከው ለራሳቸው አጯት። ልጁ ይሀን ሲሰማ በመናደድ «እኔ አይቼ ጠይቅልኝ ብዬ ብልክህ አትሆንህም ብለኸኝ፤እንዴት ለራስሀ ታጫታለህ?›› ብሎ ይጠይቃል። አያቴም ቀበል አድርገው «ላንተ አትሆንህም አልኩ እንጂ፣ ለእኔ አትሆንም ብያለሁ እንዴ?» በማለት ጥያቄውን በጥያቄ መልሰው ልጅቷን አገቧት ይባላል። የኋላ-ኋላ አባ ጎረምሳውን ሌላ ልጃገረድ ፈልገው በመዳርና ጥሎሹን በመክፈል ክሰውታል።

አባ ከማርጀታቸውበፊት ለንግድ እስከ ኦጋዴን እና በረና ድረሰ ይጓዙ ነበር። ለንግድ በሚጓዙበት

ሰዓት ከሚሰቶቻቸው መካከል ልጅ እግሯን አስከትለው የመጓዝ ልምድ ነበራቸው። አንዴ እንዲሁ ወጣት ሚስታቸውን ይዘው ሲጓዙ ይመሽባቸውና፣ ወደ ገደብ (ምዕራብ አርሲ) አካባቢ የሰው ቤት ውለታ ጠይቀው አደሩ። የቤቱ አባወራ «ልጅቷ ምንህ ናት?›› ብሎ አባን ይጠይቃቸዋል። አባም ሰውዬው ልጅቷን እንደከጀላት አውቀው፣ «እህቴ ናት›› ይላሉ። ሰውዬው በተራው «ዳርልኝ›› ሲላቸው፣ አባም በመስማማት፣ሠንጋ ፈረሰ እና ጠመንጃ በጥሎሽ መልክ ተቀብለው፣ሚስታቸውን «እኔ የሆነ ቦታ ደርሼ አስከምመለስ እዚሁ ጠብቂኝ›› ብለዋት ሄዱ ይባላል። ይህ ታሪክ እውነት ይሁን ውሸት የሚያውቁት ፈጣሪና አባ ብቻ ናቸው። ታሪኩን ዘመድ አዝማድ በሹክሹክታ የሚያወራው ቢሆንም፣ በማስረጃ የሚታወቀው ነገር፣ አንደኛዋ ሚስታቸው ለንግድ አብራቸው ወጥታ አለመመለሷ ብቻ ነው።

አባ ከእናቴ ቤተሰቦች ጋር የተለየ ፍቅር ነበራቸው ትስስራቸው ገና ልጆቻቸው ከመጋባታቸውም በፊት የተጅመረ ነው። ክርስቲያን እና ሙስሊም የሆኑት የሁለቱ ወገን ቤተሰቦች፣ልዩነቶቻቸውን በማቻቻልና በማክበር የተዋጣላቸው ነበሩ።

በክርስቲያኖቹ ወገን ድግስ ሲኖር ሙስሊሞች ጠጅ እና ጠላ ሰለማይጠጡ ቃሪቦ እና ብርዝ ይዘጋጅላቸዋል።

አንድ ቀን አባ የእናቴን ቤተሰቦች ሊጠይቁ ይሄዳሉ። ምሽት ላይ ሁለቱ አያቶቼ (ሙሐመድ ቱፋ እና ቶላ ቡሊ) በቤተሰብ መሀል ተከበውና ጎን ለጎን ተቀምጠው እሳት እየሞቁ እየተጫዋወቱ ሳለ፣ ክርስቲያኗ አያቴ ሙሉ በዳኔ ለጨዋታ ማዋዣ የሚጠጣ ነገር አመጣችላቸው። ለሙሐመድ ቃሪቦ፣ ለቶላ ደግሞ ጠላ ሰጠችው። እንደሚታወቀው ጠላ አልኮል ሲኖረው፡ ቃሪቦ ከአልኮል ነጻ ነው። ለዚህም ይመስላል ቃሪቦን «የእሰላም ጠላ» እያሉ ይጠሩታል። በመሀከል ጠላ አየጠጣ ያለው ቶላ ተረጋግቶ እየተጫወተ፣ ቃሪቦ የተሰጠው አያቴ ሙሐመድ ግን ሞቅ እያለው መጣ። ቶላ ነገሩ ግራ ገብቶት ሁኔታውን ልብ ብሎ ሲመለከት፣ ሚስቱ የእሱን መጠጫ እጇ ላይ እንዳለ እየሞላችለት፣ የሙሐመድን ግን ወደ ጓዳ ወሰዳ ሞልታ ታመጣለች። ቶላ ሁኔታውን ተጠራጥሮ «ሙሉ እሰቲ የኔንም አንደ ሙሐመድ ከጋኑ ቅጂልኝ፡ እዚህ ውጪ ስትቀጂልኝ እየነፈሰበት ነው መሰለኝ››  በማለት እሱ ጠላ አየጠጣ ሞቅታው የባለቃሪቦው ሙሐመድ የሆነበትን ምክንያት ማወቁን ገለጸላት።

አባ የትኛውንም በደል በኃይል በመመከት ያምኑ ነበር። በየዓመቱ ግብር ላለመክፈል ከአሥተዳደርና የሰፈር ሚሊሻ ጋር «መሬቱን የፈጠረው አላህ፤ አርሼ ያመረትኩት እኔ፡ ታዲያ መንግሥት ምርቴን ከእኔ ጋር የሚካፈለው ምን አሰተዋጽዖ ስላደረገ ነው ?›› በማለት ተጨቃጭቀው ተቃውሞ ያስነሳሉ። በዚህም ምክንያት ብዙ ጊዜ የአሥተዳደሩ ሰዎች አባብለው እና ከመጀመሪያው የግብር ተመን ቀንሰው ያሰተናግዷቸዋል። ለዚህም ይመሰለኛል በአንድ ወቅት አሜሪካ እያለሁ በVOA (የአሜሪካ ድምፅ ሬዲዮ)  ስለ ሰላማዊ ትግል ስናገር ሰምተው፣ ስደውልላቸው «ምነው ፈረንጅ ልብህን ሰልቦ ሳምባ ብቻ ተወልህ እንዴ? » በማለት በወቅቱ የማቀነቅነውን ሰላማዊ ትግል አንደ ፍርሀት ቆጥረው በምፀት አጣጥለውብኛል።

አባ ስላለፈ ታሪክ ማውራት እምብዛም አይወዱም። እርሱና ቤተሰቡ ያሳለፉትን ታሪክ ሲናገሩ ገጥሞን አያውቅም። ስለ አባ የሕይወት ጉዞና ታሪክ የምንሰማው ከንደኞቻቸው እና ከዘመዶቻቸው ነበር። አንዴ እስከ ሰባት ያለውን የዘር ሐርጋችንን እንዲነግሩኝ ስጠይቃቸው «ምን ያደርግልኸል? ያሸለቡትን ሽማግሌዎች አፅም ከመቃብር ልታወጣ ነው?» በማለት እንደዋዛ ቀልደውብኝ አለፉት። ከእርሳቸው ይልቅ በይሱ የምትባል አክስታችን እስከ አሥር ያለውን የዘር ሐረጋችንን ታስቆጥረን ነበር።

አባታችን ልጅ እያለን ስለሞተ፣ አያቴ በልጅነቴ ላይ ተጽዕኖ ካሳደሩ ብዙ ሰዎች አንዱ ናቸው። አያቴ ዕድሜያቸውን ነግረውኝ አያውቁም፤ ሰጠይቃቸው «ምነው? የሒሳብ ትምህርት ፈተና ላይ ይመጣል እንዴ? ነው ወይስ ሐሰን ዓብደላ (የአካባቢው ቡና ነጋዴ) ጋር ወስደህ ወደ ብር ልትመነዝረው አሰብክ? ለመንግሥት ተናግረህ ግብር ልታሰጨምርብኝ እንዳይሆን?›› እያሉ አከታትለው ጥያቄዬን በጥያቄ እየመለሱ ነገሩን ያድበሰብሱታል። ጓደኞቻቸው እንደሚናገሩት ከሆነ፣ ጣሊያን ሀገር ሲቆጣጠር አባ አግብተው ወልደዋል። ይህ ማለት በ2004 ዓ.ም ከዚህ ዓለም በሞት ሲለዩ መቶ ዓመት አልፏቸዋል ማለት ነው።

# 1.4. ጹሙጋ

ቀድም ብዩቆ እንደገለጽኩት፣ አባቴ ከደረሳነት ሲመለስ በሐረርጌ እና አርሲ አዋሳኝ ጹሙጋ በምትባል ትንሽዬ ከተማ ኑሮውን መሥርቶ በንግድ እና ልብሰ ሰፌት መተዳደር ጀምረ። በኋላ ቤተሰቡን ለመጠየቅ ወደ ሰኞ ገበያ ሲመለስ እናቴን ድረውት፣ መጀመሪያ አስኮ ወረዳ የሰኞ ገበያ (ጂኒ) ኖሩ፡ ቆይቶ ወደ ጎሉልቻ ወረዳ፣ ጨሉል ጭርቅሳ ገቡ፣ በኋላም ወደ ጽሙጋ ተመልሰን መኖር ጀመርን። ጹሙጋ ራሴን አውቄ የልጅነት ትዝታ ውሰጤ ያኖረች እና የፖለቲካ ተሳትፎም የጀመርኩበት አካባቢ ነች። ሰለዚህ ከተማዬ (hometown) ብይ የምጠራው ጹሙጋን ነው።

የጹሙጋ ከተማ በ1950ዎቹ ዓ.ም የተቆረቆረች ሰትሆን የአጼ ኃይለሥላሴ ሥርዓት "ጠቅል ተፈረ" ብሎ ሰየማት። የከተማዋ ነዋሪዎች በ1967 ዓ.ም ባደረጉት ተቃውሞ ስሟን ወደ ጹሙጋ ማሰመለሰ ችለዋል። ሆኖም የደርግ ሰዎች "Dh'ን በአማርኛ መጻፍ ሰለማይችሉ "ጥሙጋ' በማለት ይጽፉ ነበር። አሁንም ብዙ ካርታዎች ላይ የሚታየው ይኸው አጻጻፍ ነው። እዚያ በነበርኩበት ዘመን ጹሙጋ በጎሎልቻ ወረዳ ሥር ትተዳደራለች። ውጪ ሀገር ሄጄ ስመለስ ግን በአካባቢዋ ካሉ ቀበሌዎች ጋር ሽነን ኮሉ የተባለ አዲሰ ወረዳ ተዋቅሮ ጹሙጋም ዋና ከተማዋ ሆነች። የመጠጥ ውኃ ገብቶላት እንደድሮው በአህያ ከወንዝ ከመጨን ተገላግላ ጠበቀችኝ። የተሻለ መንገድም ሰለተሰራላት በበቅሎ ለቅቄያት ወጥቼ በመኪና ተመለሰኩባት።

ጹሙጋ ስያሜዋን ያገኘችው የኦሮሞ የልጅ ለልጅ ከሆነው ከጹሙጋ በሬንቶ ኦሮሞ ነው ይባላል። ስለውልደቴ ባወጋሁበት ምዕራፍ ውስጥ አንደተገለጸው ኦሮሞ ሁለት ልጆች ነበሩት፣ በረና አና በሬንቱ። በሬንቱ ኦሮሞ አምስት ልጆች ወለደ፣ እነሱም ከረዩ፡ መረዋ፡ ጹሙጋ፣ ሁምበና እና ቀሎ ይባላሉ። ጹሙጋ በሬንቶ ኦሮሞ ደግሞ አርሲ፣ ሃዋሳ እና አሰሳ የተባሉ ልጆች አፈራ። ታሪክ ዐዋቂ የአካባቢያችን የሀገር ሽማግሌዎች አንደሚሉት እኔ ያደኩባት ከተማ የተሰየመችው የነ አርሲ አባት በሆነው በጹሙጋ በሬንቶ ኦሮሞ ነው። ምክንያቱን ሲያሰረዱም የጹሙጋ በሬንቶ ቀብር በከተማዋ አፋፍ ሪቡ ተራራ ላይ ሰለሚገኝ ሲሆን፣ ቦታውም የጹሙጋ ወንዝ መነሻ ነው ይባላል።

ሽማግሌዎች እንደሚሉት ከሆነ ጹሙጋ ዋና ከተማው ለሆነችለት ለአዲሱ የሽነን ኮሉ ወረዳ ስያሜ የተሰጠው ከሦስት ምክንያቶች በመነሳት ነው። እነሱም ወረዳውን ከሚያቋርጡ አምሰት ወንዞች፣ በአካባቢው ከሚገኙ አምስት ተራሮች እና ወረዳው የጹሙጋ በሬንቶ አናት (የአምሰቱ መካነ-መቃብር መገኛ በመሆኑ ነው ይላሉ።

አምሰቱ ወንዞች ኤጀርሳ (የአርሲ አና የምዕራብ ሐረርጌ /የጨርጨር ወረዳ ድንበር ሆኖ የሚያገለግለው) ፣ በቀቅሳ፡ ጹሙጋ፤፣ ኮሉ እና ደርባ ናቸው። ያደኩት እነዚህን ወንዞች እያቋረጥኩ፣ገላዬን እየታጠብኩባቸው እና በወንዞቹ የለመለመውን የመሰኖ ሽንኮራ አየበላሁ ነው። አምሰቱ ተራራዎች ደግሞ ከከተማዋ በሰተምዕራብ ራቅ ብለው ያሉና ከደጋማው አርሲ

የሚመጡ ወንዞች የሚፈሱባቸው ሰንሰለታማ ተራሮች ናቸው። ስማቸውም ኮሉ፡ ዊጣ፣ ጃዊ፣ ጃኖ እና ሶምቦ ይባላሉ። ልጅ ሆነን ከቀትር በኋላ ከሩቅ ስናያቸው ጥላቸው አምስት ጎን ለጎን የቆሙ ሰዎች ይመስሉን ነበር። የበሬንቱ ኦሮሞ ሚስት አምስት ወንድ ልጆች ስለነበራት Haadha Shanan (የአምስቱ እናት) ተብላ ትታወቃለች። ቀብሯ ጴሙጋ በልዓ በሚባል የገጠር ቀበሌ የሚገኝ ሲሆን፣ እስካሁንም የቀብር ድንጋዩ (Koobbii/tombstone) ባለበት ቦታ ባሕላዊ ክንዋኔ ይፈጸማል።

## 1.5. የሸጎዬ ምሽቶች

ጹሙጋ ውስጥ ብዙ ጎሳዎች አሉ። በጥንት ዘመን ኢቱዎች በምሥራቅ በኩል፣ አርሲ ደግሞ የደጋውን አጎራባች ይዘው ይኖሩ ነበር። አፍረን ቀሎ በኋላ የመጡ ቢሆንም በባሕል እና በማኅበራዊ ሕይወት የበላይነትን ተቀዳጅተዋል። በእኛ ጊዜ ከየትኛውም ጎሳ የተወለደ ማንኛውም ሰው የንግግር ዘይቤዉ የአፍረን ቀሎ ሆኗል። ኢቱ እና አርሲ በወግ አጥባቂነት (conservation) ይታወቃሉ። ጹሙጋ ግን ባሕሏ እንደ ምሥራቅ ሐረርጌ ለቀቅ ያለ (Liberal) ከመሆኑ የተነሳ "ትንሿ ድሬ ደዋ" ናት ማለት ይቻላል።

እንዚህን ሦስት ጎሳዎች ጨምሮ በአካባቢው የቱለማ ኦሮሞዎች እና ጥቂት አማራዎች አሉ። ቀደም ብሎ መጥቶ ሀገሩን ሰለወደደው እዚያ የቀረ ዶ/ር ወልደአብ የሚባለ ኤርትራዊ ብቻ ነበር። በሀይማኖት ረገድ አብዛኛው ሕዝብ ሙሰሊም ሲሆን፣ ጥቂት ክርሰቲያኖችም ይገኛሉ። በአጠቃላይ ጹሙጋ የበርካታ ነገዶች፣ ብሔሮች እና ሀይማኖቶች ከተማ ናት። በባሕል እና በቋንዳ በኩል ግን ከምሥራቅ ሐረርጌ ተቆርጣ ኢቱ እና አርሲ መካከል የሰፈረች ትመስላለች።

ይህ የምሥራቅ ሐረርጌ ባሕል ከተማውን ብቻ ሳይሆን ገጠሩንም ተቆጣጥሮ ነበር። ብዙ ጊዜ እሸት ለመብላት ወደ ገጠር ስሄድ በገጠር ያሉ የባሕል ኹነቶችን የመጎብኘት ዕድል አጋጥሞኛል። ከነዚህም አንዱ የሸጎይ (ሙሲና) ባሕል ሲሆን፣ ሰርግ (አሩዝ) ሲቃረብ ወጣት ወንዶች እና ልጃገረዶች ሌሊት ወደ ጫካ ሄደው ይጫወታሉ። በጫካው መሀል ለጥ ያለ ሜዳ ፈልገው በተፈጥሮ ድምጻቸው እየተቀባበሉ ይዘምራሉ። የሚጫወቷቸው የሸጎዬ ዓይነቶች ደዳይሳ፣ ሁሩምሱ፣ ኦኮይና፣ ገዲ ደዋ፣ ጂይሳ፣ ረገዳ፣ ወዘተ በመባል ይታወቃሉ።

የወጣት ልጃገረዶች እና ጎረምሶች በምሽት ወጥቶ መዝፈን የሚታወቅ ቢሆንም በግለጽ ግን አይፈቀድም። ስለዚህ ላለመጋለጥ ሲባል ምሽት ከሰፈር ራቅ ተብሎ ይጨፈራል። ይህም ርቀት "ሽማግሌዎችን በእንቅልፍ ሰዓት ላለመረበሽ" የሚደረግ ጥረት አካል ነው ይባላል።

እኩያማቾች የሆኑ ልጃገረዶች እና ጎረምሶች የሚጫወቱበትን ቀን፣ ቦታ አና ሰዓት ይቀጣጠራሉ። ምሽት ላይ ሴቷ ልጅ ቤተሰቦቿን እራት አብልታ ካስተኛች በኋላ ከእናቷ ጀርባ ትተኛለች። ወላጆቿ መተኛታቸውን ሰትገነዘብ፣ ቀሰ ብላ ትነሳና ማታውኑ አንዳይጮኽ ብላ በውኃ ያራሰችውን በር ከፍታ ወጥታ ከሌሎች ሴት ጓደኛቿ ጋር ትቀላቀላለች። እናቷ ለወጉ ያህል ዓይኖቿን ታዞራለች እንጂ ምሥጢሩን ታውቃለች። ይልቁንም ወደ ሸጎዬ ከሚሄዱ ወጣቶች መካከል ለአንዱ ዘመድ አደራ ትሰጣለች።

ወጣቱ የሴቷን ደኅንነት እና ሥነ-ምግባር የመጠበቁን ኃላፊነት ይወሰዳል። በዚህም ምክንያት የሸጎዬ ቦታ አንዲት ልጃገረድ እና አንድ ወጣት የፍቅር ዘፈኖችን አብረው ቢዘፍኑም እዚያ ያለፈ ፆታዊ ግንኙነት አይታሰብም። በሌላ ቦታም ቢሆን አንድ ወጣት ካላገባች ሴት ጋር ከተኛ እንደ ነውር የሚቆጠር ከባድ ጥፋት ነው። ይሀን የፈጸመ በሸለምጥማጥ ቆዳ ተጠቅልሉ ከጎሳው እና ከሀገሩ አንዲወገድ ይደረጋል። ሸለምጥማጥ በመጥፎ ጠረን የሚታወቅ እንሰሳ ነው። በእኛ ዘመን ጫካ ሄዶ ሸጎዬ የመጫወት ባሕል እየተዳከመ መጥቶ በዳንስ ተተካ። በጹሙጋ

ከተማ የሰርግ ሥነ-ሥርዓትን በዳንሰ ያደምቁ ነበር። እንደቀድሞ በተፈጥሮ ድምፅ ከመዝፈን ይልቅ በቴፕ ካሴት በታውን እየተነጠቀ መጣ። ወጣት ወንዶች እና ሴቶች በተፈጥሮ ድምጻቸው ሲጫወቱ ወዲያውኑ ግጥሞችን በመፍጠር ይወዳደሱ ነበር። እሁን ያ ሁሉ ቀርቶ ከቴፕ ተቀነባብሮ በሚሰማ ዘፈን ተለወጠ፤ ከቤት ርቆ ወደ ጫካ ከመሄድ ይልቅ ከተማ ውሰጥ ቤት ዘግቶ መጨፈር ሆነ።

በእኔ ዘመን የዳንስ ጭፈራው በአብዛኛው ሸጎዬ ሆኖ ቢቀጥልም፣ ቴፕ እና ካሴት መሰፋፋቱ የሌሎች የኦሮሚያ ዞኖች እንዲሁም የአማርኛ፣ የትግርኛ እና የጉራግኛ የባሕል ውዝዋዜዎች እንዲለመዱ ዕድል ፈጥሯል። አንዳንዴ ሌሊቱ ተጋምሶ ምርቃናው ሲደራ የማይክል ጃክሰን "ዲሰኮ" ይከፈታል። በአንዲት በቆርቆሮ የተሸፈነች ትንሽዬ ክፍል ውሰጥ ብዙ ሰዎች ከአፍ እስከ ገደፉ ሞልተው ሲጨፍሩ የሚንጠፈጠፈው ላብ ጣሪያውን ነክቶ እየተመለሰ እንደዝናብ መልሶ ያበሰብሳል።

በወቅቱ ይህ የቴፕ ዳንስ ወደ ገጠርም መሰፋፋት ጀምሯል። እኔም ገጠር ሰርግ ሲኖር ቴፕ እና ካሴቶችን ከከተማ ወሰጄ በማከራየት ለደብተር መግዣ ገቢ አገኝበት ነበር። ሻርፕ (Sharp) የተባለውን የእህቴን ባል ቴፕ ሪክርደር፣ ከብዙ ካሴቶች ጋር ይዤ ወደገጠር ሳቀና፣ መሸከሙ ስለሚከብደኝ ሰርጉ ላይ ከልጃገርዶች ጋር መጨፈር ለሚፈልጉ ዕድሜያቸው ከፍ ላለ ጎረምሶች ተሸክመውልኝ እንዲሄዱ አግባባለሁ። ሰርጉ ቦታም ልጃገረዶች ቴፑን ሃሙራ የሚባለውን የጥፍር ቀለም በመቀባት ያሰምሩታል። የምርቃና ደረጃውን የሚመጥን ካሴት እየቀያየርኩ ሳሰጨፍር አድሬ፣ ክፍያዬን ወሰጄ ወደከተማ እመለሳለሁ።

በአካባቢያችን ብዙ የሰርግ ልማዶች ነበሩ። ከእነዚሀ ውሰጥ በጣም የማታወቁት ከጳ (መሪ)፣ ጨብሳ እና ቡታ ናቸው። ከሁሉም በክብር የሚታየው ወንዱ የልጅቷን ቤተሰብ ለምኖ አጭቶ የሚያገባው ነው። አንድ ወጣት ለማግባት ዝግጁ ሲሆን ልቡ የከጀላትን አይቶ ለአባቱ ይናገራል። አባትየውም ሽማግሌ መርጦ ወደ ልጅቷ ቤተሰቦች ይልካል። እነሱም ልጅቷ ከዚህ በፊት ካልታጨች "ተወያይተን እናሳውቃችኋለን" በማለት ለሌላ ጊዜ ይቀጥሯቸዋል። በዚያ ቀጠሮ ልጁ ጥሩ አማች እንደሚሆናቸው ካመኑ «ይሁን» ይላሉ።

በመቀጠል የጉዱንፋ ሥነ-ሥርዓት ይከተላል። ይህም በልጁ ወገን ያሉት ሽማግሌዎች እንደ ትምባሆ ስኳር፡ ጀንፈል ቡና ወዘተ ይዘው በመሄድ ለሴቷ ወገን የሚሰጡበት ነው። የልጃገረዷ ወላጆች ቋጠሮውን ከፈቱ ልጅቷ ታጭታለች ማለት ነው። ከዚያም ልጁ ለአማቾቹ ጥሎሽ ይጥላል። ጥሎሹ እንደሌሎች አካባቢዎች ለአማቾቹ ገንዘብ ወይም ከብት ከመስጠት ይልቅ በሥራ ማገዝ ነው። ልጁ ደቦ ጠርቶ በቡና ቆፋሮ፣ እህል በማጨድ እና ቤት በመሥራት ያግዛል። ይህ ለአማቾች የሚሰጥ ነጻ አገልግሎት እነሱን ከመጥቀም ይልቅ ለልጁ ሠራተኛ መሆኑን ለመገምገም የሚከናወን ነው።

ደቦ የጠራ ሰው በምላሹ ለጠራቸው ሰዎች ሄዶ መሥራት አለበት። ብዙ ሰዎችን ደቦ መጥራት ቻለ ማለት ከዚሀ በፊት ሌሎችን አግዟል ወይም ወደፊት አፀፋውን እንደሚመልስ ይታመናል። ወጣት ሙሽሮች ለአማቾች ደቦ በሚጠሩት የሰዎች ብዛት ይፎካከራሉ። «የእከሌ አማች ለጠራው ደቦ ማሳው አልበቃ አለ» ተብሎ ይዘመርለታል። በዚህ መንገድ ልጅቷን አግብቶ ወደ ቤቱ ከማሰገባቱ በፊት ቢያንሰ ለሁለት ዓመታት ያገለግላል። በዚህ ጊዜ ውሰጥ ለአማቾቹ ብቻ ሳይሆን ለራሱም በትጋት መሥራት አለበት። ቢያንስ አራሽ በሬ እና ሦሰት ጎተራ እንዲኖረው ይጠበቃል። ምክንያቱም አንዱ በድንገት ቢሞት፣ ሥራው እንዳይቆም ዋሰትና ለማግኘት ነው።

መሬቱ በረሃ ከሆነ ሁለት ጎተራ በቆሎ እና ሁለት ጉድጓድ ማሽላ፣ ደጋ ከሆነ እኩል መጠን ያለው ስንዴ እና ገብስ ያስፈልገዋል።

በዚህ መልኩ ለአማቾቹ ደቦ እየጠራ እና ምርቱንም ማሳየት ሲጀምር "ልጁ ትጉህ ነው!" ተብሎ የሰርግ ቀጠሮ ይያዝለታል። እሱም አዲስ ቤት ሠርቶ ለሰርጉ ይሰናዳል። ለሰርጉ አንድ ወር ሲቀረው ልጃገረዶች እና ጎረምሶች ሽጎዬውን ይጀምራሉ። በሰርጉ ቀን በወጣት ጭፈራ ታጅቦ፣ ለልጅቷ ኒካህ አሰሮ ወደ ቤት ይዟት ይገባል።

ሴት ልጅን ለምኖ ማግባት እንደዚህ ዓይነት ውጣ ውረድ ስላለው አንዳንድ ወጣቶች በጨብሳ እና ቡታ ማግባትን ይመርጣሉ። እኛ ጋር ከቡታ በላይ ጨብሳ ይከናወናል። ጨብሳ የድንገቴ ጋብቻ ሲሆን፣ ሴትን ልጅ ወዲያውኑ ለምኖ የማግባት ሂደት ነው። ልጁ በማለዳ ጓደኞቹን ይዞ የልጅቷ ወላጆች ቀዬ በማድፈጥ ከአንቅልፍ እስኪነቁ ድረስ ይጠባበቃል። ሴቶቹ አመድ ለመድፋት በሩን ከፍተው ሲወጡ፣ ካደፈጡበት ዘለው በመነሳት አለንጋ ወደ ፊት ወርውረው ገብተው ይቀመጣሉ። የልጅቷ አባት ነገሩ ስለሚገባቸው ለጎረቤት ሽማግሌዎች ይናገራሉ።

ሽማግሌዎቹ በተራቸው ወጣቶቹ ያለ ግብዣ ለምን የሰው ቤት ዘው ብለው እንደገቡ ይጠይቃሉ። የሚፈልጓትን ሴት ልጅ ስም እንደተናገሩ ሽማግሌዎቹ ጉዳዩን አጣርተው ለልጅቷ አባት ይናገራሉ። እሱም ልጅቷ እጮኛ እንዳላት እና መስጠት እንደማይችል ገልፆ እንዲሄዱ ይጠይቃል። «እጮኛ አላት» የሚለው ብዙ ጊዜ ውሸት ነው። ይህንን ስለሚያውቁ ወጣቶቹ አይወጡም። በዚህ ጊዜ የልጁ አባት ሽማግሌዎችን ይልካል። የገዘ ልጁን ጥሉሽ ጥሎ በወግ በማዕረግ ሊያጋባው አቅዶ ባለበት፣ያለፍቃዱ ጨብሳ ሄዶ እንዳዋረደው በቁጣ ይናገራል። ይህ እውነት ወይም ማስመሰልም ሊሆን ይችላል። ሽማግሌዎቹም የልጅቷ ወላጆች ዘንድ ሄደው ይቀመጣሉ። ከብዙ ምልጃ እና ክርክር በኋላ እሺ ከተባሉ፣ አንድም በዚያው ቀን ፈጣን ሰርግ ተካሂዶ ልጅቷን ይዘው ይገባሉ። አለበለዚያ የጥቂት ሳምንታት አጭር ቀጠሮ ያስይዛሉ።

አንድ ወጣት በጨብሳ ለማግባት የሚገደድባቸው የተለያዩ ምክንያቶች ሊኖሩ ይችላሉ። አንደኛው ምክንያት በሁለቱም በኩል ያሉት ቤተሰቦች ቂም ኮተያያዙ፣ ልጁ ደሀ ከሆነና የልጅቷ ወላጆች ሀብታም ሆነው በወጉ ከጠየኩኝ አይሰጡኝም ብሎ የሠጋ እንደሆነ ነው። ከዚህ ውጪ በገንዘብ ከእሱ ሻል ያለ ሰው ልጅቷን ለመጠየቅ ማቀዱን ከሰማ ሳይቀደም ለመቅደም ነው። ያጫት ልጅ ሌላ ሰው አፍቅራ አብራው ከኮበለለች፣ አሊያም ከተጠለፈች ሞራሉን ለመጠበቅ በእልህ ተነሳስቶ ወደ ጨብሳ ያመራል።

በሌላ በኩል ጨብሳም አይሳካልኝም ብሉ የሠጋ ወጣት ቡታን እንደ አማራጭ ይወሰዳል። ሌላ ሰው ቀድሞ ካጫት ኮረዳ ከባድ ፍቅር ከያዘው፡ ልጅቷ ላይ ጠለፋ (ቡታ) ሊፈጽም ይችላል። ወኃ ቀድታ፣ እንጨት ሰብራ ወይም ገበያ ሄዳ ሰትመለስ ጓደኞቹን አደራጅቶ በግዳጅ ይዟት ከተሰወረ በኋላ የሀገር ሽማግሌ ልኮ በመታረቅ ኒካህ ያሥራል።

ከቅርብ ዓመታት ወዲህ ግን የኃይል ጠለፋ በአብዛኛው ቀርቶ በሐሰተኛው ተተክቷል። ይህም ወንዱ እና ሴቷ ከተዋደዱ በኃላ ወላጆቿ ይሁን እንደማይሉ ከጠረጠሩ የውሸት ጠለፋ በስምምነት ያዘጋጃሉ። በተቀጣጠሩበት ቦታና ሰዓት ተገናኝተው ይዟት ይሄዳል። ከዚያም በእውነት እንደጠለፋት አሰመሰሎ ሽማግሌ ልኮ ይጨርሳል። ምንም አንኳን ልጁ እና ልጅቷ ተዋደው ለመጋባት ቢሰማሙም፡ ወደ ቤቱ መግባትን እንደ ውርደት ይቆጥረዋል። ስለዚህ የውሸት ጠለፋ የሚቀነባበረው የሴቷን ስም እና የወላጆቿን ክብር ለመጠበቅ ሲባል ነው።

የገጠር ሰርግ ሲኖር ሁሌም አልቅሼ ከእናቴ ጋር እሄዳለሁ። ብዙ አሥቂኝ ትዝታዎችም አሉኝ።

ሙሽሪትን ወደ ቤት ይዘው በሚገቡበት ወቅት ሲጨፈር ይታደራል። ሽማግሌዎች በአንድ ቤት ውስጥ ዱዓ ያደርጋሉ፣ ወንዶች እና ሴቶች ከሙሽሮቹ ጋር በሌላ ቤት ይጨዋወታሉ። በሁለተኛው ቀን እራት ከተበላ በኋላ የልጁ ሚዜዎች ሁሉንም ሰው ሙሽሮቹ ካሉበት ቤት በማባረር ሽማግሌዎች ወዳሉበት ቤት ወይም ወደ ጎረቤት ይወስዷቸዋል። ይህም ሙሽሮቹ የመጀመሪያቸውን የግብረ ሥጋ ግንኙነት እንዲፈጽሙ ነፃነት (privacy) ለመስጠት ነው።

ምሽቱ ሙሽሪት ልጃገረድ ሰለመሆኗ ለሚነሳው ጥያቄና ሀሜት፡ ሙሽራው ይችላል ወይ? ለሚለው ግምት መልስ የሚገኝበት ስለሆነ ሚዜዎች ምሥጢሩን ለመጠበቅ፡ ሌሎቹ ደግሞ ቀድሞ ለማወቅ ይፋጠጣሉ። ስለዚህ ሚዜዎቹ ቤቱን እና አካባቢውን አስሰው ያገኙትን ሰው ሁሉ በአለንጋ እየገረፉ ያባርራሉ። ምሥጢሩን ለማወቅ የሚፈልጉ ሰዎች እንደ እኛ ያሉ ልጆችን ይጠቀማሉ። ትንንሾች ስለሆን የቤቱ ግድግዳ ላይ ከተጋደመ ሳር ወይም በቡና ጀኒያ መሀል ይደብቁናል። ድምጻችንን አጥፍተን ከሚዜዎቹ ፍተሻ ካመለጥን በሙሽሮቹ የጫጉላ ክፍል ውስጥ የሆነውን እና የሰማነውን ሁሉ ላሰማሩን ትልልቅ ሰዎች እንተርካለን። ተደብቀን ከተገኘን ግን የዕድሜ ልክ ጠባሳ የሚያስቀር የአለንጋ ግርፋት ያጠብቀናል። እኔ በማሰታወስ ችሎታዬና የተከሰተውን አጣፍጬ በመተረክ ሰለምታወቅ፣ ብዙ ጊዜ ለዚህ ተልዕኮ እመረጣለሁ። በተደጋጋሚ አሰኪበቃኝ ድረሰ በአለንጋ ተገርፈያለሁ።

## 1.6. ጺሙጋ እና የኦሮሞ ትግል

ወደ ፖለቲካው ሰንመልስ፣ ጺሙጋ ለወታደራዊ ሰልት የምትፈለግ ሰትራቴጂካዊ ሰፍራ ናት። በዚህም የተነሳ የአካባቢው ሕዝብ ከአያቶቻችን አንስቶ እስከ እኛ ዘመን ድረስ መራራ የትግል እና የመከራ ጊዜያትን አሳልፏል። ጺሙጋ ምዕራብ ሐረርጌ፣ አርሲ እና ባሌ መካከል ሰለምትገኝ ለሦስቱ ዞኖች ግንኙነት ወሳኝ ማዕከል ተደርጋ ትታያለች። በ1960ዎቹ የኃይለሥላሴ ጦር እዚያ ቦታ ካምፕ በማሠራት የባሌ ሕዝብ አመጽ ወደ ሐረርጌ እና አርሲ እንዳይዛመት ከፍተኛ አሰሳ እና ክትትል ሲያደርግ ነበር ይባላል።

የንጉሡ መንግሥት ያንን አካባቢ በጥርጣሬ ለመመልከት በቂ ምክንያቶች ነበሩት። ለምሳሌ ዕውቁ ታጋይ ጃራ አባገዳ ለትጥቅ ትግል ወደ ባሌ ሲያመራ፣ እዚሁ ጺሙጋ አካባቢ ቆይቶ ከባሌ ከመጡ ገበያተኞች ጋር ተደባልቆ እና ነጋዴ መስሎ የዋቤ ወንዝን በመሻገር ከነዋቆ ጉቱ ጋር ተቀላቅሏል። ብዙ የአካባቢው ተወላጆች ወደ ባሌ ሄደው ሶውራ በሚባለው ጦርነት ተሳትፈዋል፣ ተመልሰውም ትግሉን ወደ አርሲ እና ሐረርጌ ለማሰፋፋት ሞክረዋል በሚል ሰበብ መንግሥት በሕዝቡ ላይ ከፍተኛ ጉዳት አድርሷል።

ጀኔራል ታደሠ ብሩ ገለምሶ በቁም አስር ላይ በነበረበት ወቅት፣ የጺሙጋ አካባቢ ሰዎች በድብቅ ሄደው ሲያገኙት እንደነበር አሁንም በሕይወት ያሉ የአካባቢው ተወላጆች አማኝነት ይሰጣሉ። በመጨረሻ ከቁም እስር ሲለቀቅም፣ ከእነ ኮሎኔል ኃይሉ ረጋሳ ጋር በዚሁ አካባቢ የትጥቅ ትግል ለመጀመር ከመጡ በኋላ፣ ከፓለቲካ አመራሩ ጋር ለመወያየት ወደ መሀል ሀገር ተጉዘዋል። ከጥቂት ዓመታት በኋላ የኦነግ የትጥቅ ትግል ሲጀመርም እንዲሁ፣ ለውጊያ ያመቻሉ ተብለው ከተለይ ቦታዎች ውሰጥ ከጺሙጋ የሁለት ሰዓት የእግር ጉዞ ላይ የሚገኘው የቱምቱ ፉርዳ በረሃ አንዱ ነው።

ከቱምቱ ፉርዳ ጀምሮ በዳሮ ቢሊቃ አድርጎ እስከ ጋራ ሙለታ እና ጎቤሌ ወንዝ ድረሰ ያለው የመሬት አቀማመጥ፣ እንዲሁም የሕዝቡ አሰፋፈር ለትግሉ የተመቸ ነበር። አብዛኛዎቹ የኦነግ አመራሮች ከፊንፊኔ ወደ ሐረርጌ ሲሄዱ በአዋሽ መንገድ ያለውን ፍተሻ ለማምለጥ ሲሉ በአርሲ አድርገው በእኛ አካባቢ ያልፉ ነበር። በዚሁ የአካባቢው ጂኦግራፊያዊ ተፈላጊነት የተነሳ ኦነግ የሕዝቡን ንቃተ-ኅሊና ለማጎልበት እና ለማደራጀት በከፍተኛ ትኩረት ሠርቷል ። ከቀደምቶች የኦነግ አመራሮች አንዱ የነበረው ጀማል ሮበሌ (ጉተማ ሐዋሰ) የአካባቢው ተወላጅ በመሆኑ፣ የወረዳውን ሕዝብ በደንብ በማንቃት እና በማደራጀት ለኦነግ እንቅሰቃሴ አመቺ ሁኔታ ፈጥሯል። ከዚያ ወዲህም አካባቢው ብዙ የኦነግ አመራሮች እና የጦር አዛዦችን አፍርቷል።

ይህንን የኦነግ እንቅሰቃሴ ለመበቀል የደርግ መንግሥት በአካባቢው ሕዝብ ላይ ከፍተኛ ጉዳት አደረሰ። በቀይ ሽብር ዘመን ደርግ በአንድ ቀን ውስጥ ብቻ አካባቢዋ አሏት የሚባሉ ጉምቱ ሰዎችን፣ትልልቅ ባለሀብቶችን፡ ታዋቂ የሀገር ሽማግሌዎችን እና የሀይማኖት አባቶችን ሰብስቦ በሦስቱ የከተማው መግቢያዎች ላይ ገድሎ በመጣል ሬሳቸው ለቀናት እንዳይነሳ አድርጓል።

በሕወሓት/ኢሕአዴግ የመጀመሪያዎቹ ዓመታት ለቀይ ሽብር ክስ ማሰረጃ ሲሰበስብ፣ በወቅቱ የተረሸኑ ሰዎች አፅም ፖሊስ ጣቢያ ጀርባ ከነበረ ገደል ተፈልጎ ሲወጣ በዓይኔ አይቻለሁ።

የደርግ ጭፍጨፋ የአካባቢውን ሕዝብ ሆድ ሰላስባሰው፡ በ197070ዎቹ የነበሩ አብዛኞቹ የአካባቢው ወጣቶች ወደ ትጥቅ ትግል እንዲገቡ በር ከፍቷል። ከእነሱ ውስጥ የተወሰኑት በጊዜ ሂደት ዝነኛ የኦነግ ጦር አመራር መሆን ችለዋል። በልጅነታችን ሰማቸው ሲወደሰ ከምንሰማቸው የአካባቢው ተወላጅ የኦነግ አመራሮች ውስጥ ቦባሳ ገዳ፣ እሰሊ ኦርሞ፡ አብደታ ሐጂ ቡና፣ ኢብሳ ሰባ እና ጎቶምሳ ገናን አሰታውሳለሁ። የእኛ ትውልድም እንደእነሱ ለመሆን ከልጅነታችን ጀምሮ ምኞት አደረብን።

በሕወሓት/ኢሕአዴግ ዘመንም በአካባቢው ሕዝብ ላይ የሚደርሰው መከራ አላባራም። ደርግ እንደወደቀ ኦነግ አካባቢውን ተቆጣጥሮ ማሥተዳደር ጀመረ። በሽግግር ቻርተሩ ሰምምነት መሠረት የኦሮሞ ነጻነት ሠራዊት ጦር በብዙ ቦታዎች ካምፕ ሲገባ፣ በእኛ አካባቢ የነበረው ግን በአብዛኛው ካምፕ ሳይገባ ሰለቀረ፣ ኦነግ ከቻርተሩ ሲወጣ ትልቅ ጦርነት ተደረገ። በዚህም የተነሳ ከፍተኛ የሰለማዊ ሰዎች ዕልቂት በሌላ ዙር ተፈጸመ። ከኦነግ የፖለቲካ ቢሮ አመራሮች አንዱ የሆነው ነዲ ገመዳ ከአዲስ አበባ ወጥቶ ወደ ሐረርጌ ለማለፍ ሲሞክር እዚሁ ጶሙጋ በዴዩ የተባለ መንደር ከተያዘ በኋላ እስከዛሬ ደብዛው አልተገኘም።

አባቴ የኦነግ ተዋጊ ባይሆንም የረጅም ጊዜ የቡድኑ ጎቡዕ ደጋፊ ነበር። ከደርግ ውድቀት በኃላ ኦነግ አካባቢውን ማሥተዳደር ሲጀምር፣ አባቴ እና ጓደኞቹ ሕዝብ የማሰተባበር እና አሥተዳደራዊ መዋቅር የመዘርጋት ሥራ ላይ ተሰማሩ። በጎቡዕ ሲያደርግ የነበረው ደጋፍ ገሃድ በመውጣቱ ኦነግ ከቻርተሩ ወጥቶ ሕወሓት/ኢሕአዴግ አካባቢውን መልሶ ሲቆጣጠር፣ ችግር ውስጥ ገባ። አካባቢው እንደ አዲስ የጦር አውድማ ሆነ። የኢሕአዴግ ኃይል በኦሕዴድ እየታገዘ ደጋማውን አርሲ፣ ሐረርጌ እንዲሁም የባሌን በረሃ ለመሻገር ወደ አካባቢያችን ተንቀሳቀሰ። ሕዝቡ እና የኦሮሞ ነጻነት ሠራዊት አላሳልፍ ብለው ለወራት የዘለቀ ጦርነት አካሄዱ። የኦሮሞ ነጻነት ሠራዊት ወደ ካምፕ እንዲገባ ሲደረግ በእኛ አካባቢ ሰፍሮ የነበረው ጦር አሻፈረኝ ብሎ ውጪ መቆየቱ ለመልሶ መከለከል ጦርነቱ ድርሻ ነበረው። ከብዙ ዕልቂት በኋለ የሕወሓት/ኢሕኣዴግ ጦር በከባድ መሣሪያ ታግዞ የጉጉን ተራሮች አልፎ ገባ። የኦነግ ጦርም ከተማዎችን ለቅቆ ወደ ቀድሞው አማጺነት ተመለሰ።

ሕወሓት/ኢሕአዴግ አካባቢውን ከተቆጣጠረ በኋላ የኦነግ አባላት እና ደጋፊዎች ብሎ የጠረጠራቸውን በሙሉ ማደን ጀመረ፡ አባቴንም ይዘውት ወደ ሌላ ቦታ ወሰዱት። ከወራቶች በኋለ ወደ ቀዬው ሲመለሰ መታመሙን እና ሰውነቱ ክፉኛ መጎሳቆሉን ሰማሁ። በወቅቱ የእናቴ ዘመዶች ጋር ሰለነበርኩ ሳለየው፡ እሱም ካጋጠመው ሕመም ሳያገግም፣ በ1986ዓ.ም በሞት ተለየን። አባቴ ሲሞት ሁለት ሚሰቶች ነበሩት። ብቸኛው የቤተሰቡ የገቢ ምንጭ ሰለነበረ ያፈራው ንብረትም የእሱን መታሰር እና ማለፍ ተከትሎ እንደጉም ተነነ፡ ቤተሰባችንም ተበተነ። ልጆቹም ተከፋፍለን በየዘመዶቻችን ቤት በጥገኝነት መኖር ጀመርን።

# ክፍል ሁለት - ከፖለቲካ ትውውቅ

## 2.1. ነገረ ኦሮሞ

እስከማስታውሰው ድረስ «ኦሮሞ›› የሚለውን ቃል ለመጀመሪያ ጊዜ የሰማሁት፣ አንድ ቀን ከእናቴ ጋር ወደ እሷ ቤተሰቦች እየሄድን የእንጨት ጥላ ሥር አረፍ ባልንበት አጋጣሚ ነበር። በአካባቢው ኦሮሞዎች ሲገናኙ ከስማቸው በመቀጠል ጎሳቸውን በመጠያየቅ የበለጠ ለመተዋወቅ ይሞክራሉ።

እዚያ አረፍ ባልንበት ቦታ ትውውቅ ሲካሄድ፣ አንዱ ጋዱላ (የኢቱ ኦሮሞ አንዱ ንዑስ ጎሳ)፣ ሌላው ቤጎ (አርሲ) ፣ አንዷ ሜታ (ከአፍረን ቀሎ) ብለው ራሳቸውን አስተዋወቁ። እናቴ ደግሞ ጎሳዋ ኦሮሞ እንደሆነ ተናገረች። በወቅቱ እናቴ የተናገረችው የጎሳ ስም ግልጽ አልሆነልኝም። ኦሮሞ ስለሚባል ጎሳ ከዚያ በፊት ሰምቼ አላውቅም፣ እኔ የእናቴ ቤተሰቦች ጎሳ ሰላሌ እንደሆነ ነበር የማውቀው። አርሲ፣ ኢቱም ሆነ አማራው የሚጠራቸው ሰላሌ እያለ ነው። እናቴ ጎሳዋ ኦሮሞ እንደሆነ ስትናገር እንደ መንገደኛ «አንቺ ሴት እኛ ሁላችንም ኦሮሞ ነን፤ የጠየቅንሽ ጎሳሽን ነው›› አሏት። እናቴም «አቢቹ›› መሆኗን ገለጸችላቸው።

ዘግይቼ እንደተረዳሁት ሰላሌ የአካባቢ እንጂ የጎሳ ስም አይደለም። በወቅቱ ሰላሌዎች ብቻ ሳይሆኑ በአካባቢው የሚኖሩ ሌሎች የኦሮሞ ማኅበረሰቦችም የሚጠሩት በትክክለኛው የጎሳ ስማቸው እንዳልሆነ ተረዳሁ። ለምሳሌ ከምሥራቅ ሐረርጌ መጥተው አካባቢው ላይ የሰፈሩ ኦሮሞዎች በአጠቃላይ «ኖሌ›› በሚል ስም ይታወቁ ነበር።«ኖሌ›› የአንድ ንዑስ ጎሳ ስም ሆኖ እያለ፣ በእኛ አካባቢ የምሥራቅ ሐረርጌ ኦሮሞዎች በሙሉ (ለምሳሌ አላ፣ ኦቦራ፣ ሜታ፣ጃርሶ አና የመሳሰሉት ንዑስ ጎሳዎች) በአንድ ላይ ኖሌ ተብለው ይጠራሉ። ሁሉም የምሰራቅ ሐረርጌ ጎሳዎች ኖሌ የተባለበት ታሪካዊ ምክንያት እንዳለም ተረዳሁ። ነገሩ ወዲህ ነው። ከረጅም ዓመታት በፊት ምሥራቅ ሐረርጌ አካባቢ ድርቅ ተከስቶ፣ ብዙ ሕዝብ ወደ ጨርጨር (ምዕራብ ሐረርጌ) እና አርሲ ድንበር ተሰድዶ ይኖር ነበር። ጨርጨር የኢቱ ኦሮሞ የሚኖርበት ሲሆን ከአሲሷ ጋር በድንበር ይዋሰናል። ጨርጨር እና አርሲ በሚዋሰኑበት እንደ ዳሮ ለቡ፣ አሰኮ፣ አንጫር እና ጎሎልቻ ያሉ ወረዳዎች የአርሲ አና የኢቱ ጎሳዎች ተቀላቅለው በመሰፈር ጋብቻ ተሳሰረው ኖረዋል። እንግዲሀ ቀድሞ እዚያ በነበሩት የኢቱና የአርሲ ጎሳዎች ኖሌ ተብሎ የሚጠራው፣ በዚያ የድርቅ ዘመን ከምሥራቅ ሐረርጌ ተሰዶ ወደ ጨርጨር እና አርሲ

የመጣው ማኅበረሰብ ነው። ከምሥራቅ ሐረርጌ ከመጡት መካከል ቀድሞ የደረሰው የኖሌ7 ንዑስ ጎሳ ስለነበር ህገሬው ከኋላ የመጡትን በሙሉ በዚያው ሰም መጥራት ጀመረ። በዚህም መሠረት የምሥራቅ ሐረርጌ የአነጋገር ዘዬ (dialect) ያለው ሰው ማለትም አንዳንድ ቃሎቶች ላይ 'kha' (khana) ፣ eeysa (kheeysa/keeysa) የሚጠቀም በሙሉ «ኖሌ» ተብሎ ይጠራል።

ከዚህ ታሪክ ጋር የተያያዘ ቀልድም አለ። የምሥራቅ ሐረርጌ ተፈናቃዮች ጨርጨር እንደደረሱ ወደ አርሲ አሻግረው ሲመለከቱ ከጉጉ ተራሮች ቁልቁል የሚፈስ ነጭ ነገር ይመለከታሉ። «ያ ነጭ ነገር ምንድነው?» ብለው ያስተናግዷቸውን የኢቱ ጎሳ ሰዎች ሲጠይቁ «ከጋራ ላይ የሚፈስ ወተት ነው» ብለው መለሱላቸው። ተፈናቃዮቹም «ወተት ከጋራ ላይ ወደሚፈስበት ሀብታም ሀገር እንሄዳለን» ብለው ጨርጨርን ተሻግረው ወደ አርሲ ዘለቁ። በዚህ ሁኔታ ኢቱ ስደተኞቹን ሸንግሎ ወደ አርሲ ላካቸው በማለት የሦስቱ ጎሳ ሽማግሌዎች እርስ በእርስ ይተራረባሉ። እውነታው ግን በክረምት ጊዜ ደጋማው አርሲ ክፍተኛ ዝናብ ስለሚያገኝ ወንዞች ሞልተው በጉጉ ተራራ ላይ ብዙ ፏፏቴዎችን ይፈጥራሉ። ከሩቅ ሲታይ የምርም ወደ ታች የሚፈስ ወተት እንጂ ውኃ አይመስልም።

በሌላ በኩል በአካባቢው በሚገኙ የአርሲ ጎሳዎች የሚከበሩት አውሊያ ሼኽ ሁሴን ሲሆኑ፣ ከምስራቅ ሐረርጌ በመጡት ዘንድ ሼኽ አባድር ይወሳሉ። ከዚህ የተነሳ ከምሰራቅ ሐረርጌ የሚመጡ ኦሮሞዎች ኖሌ ከሚለው መጠሪያ በተጨማሪ «የአባድር ሰዎች/Warra Abaadir/» በመባልም ይታወቃሉ። ይህንን ስያሜ ያገኙት በታዋቂው የሐረር አውሊያ ሼክ አባድር (Sheikh Abaadir Umar Al-Rida) ሰበብ እንደሆነ ይነገራል። እንደ ሼኽ ሁሴን ሁሉ ሼኽ አባድርም ታለቅ ዓሊም እና አውሊያ ነበሩ። ከሐረሪ ማኅበረሰብ በተጨማሪ በምስራቅ ሐረርጌ ኦሮሞዎች እና ሶማሌዎች ዘንድ ታለቅ ተሰሚነት እና አክብሮት አላቸው። በመንዙማ ውስጥም ይወደሳሉ። በአካባቢያችን የሚገኙ የምሰራቅ ሐረርጌ ኦሮሞዎች በወዳጃ ወቅት ሼኽ አባድር እና ሰይድ አቢዮን ያወድሱ ነበር።

7 ኖሌ የትውልድ ሐረጉ ከደጋ ቀሎ በሬንቶ ኦሮሞ ነው። ባለፉት ምዕራፎች እንደተገለጸጠው በትውልድ ሐረግ ተዋረድ መሰረት ኦሮሞ ሁለት ልጆች ነበሩት፣ ቦረና እና በረንቱ፡ በሬንቱ በበኩሉ እምሰት የወለደ ሲሆን እንዱ ቀሎ ነው። ቀሎ እራት ልጆች ሲኖሩት እነሱም አላ፣ ደጋ፣ ኦበራ እና ባቢሌ ናቸው። ደጋ በተራው ሦሰት ልጆች የወለደ ሲሆን ኖሌ፣ ጃርሶ እና ሁሜ ሲባሉ ከእነሱ በተዋረድ የመጡ ንዑሰ ጎሳዎች ቀደምት ቀዬኣቸው ከሶማሌ ክልል አዋሳኝ እንሰቶ ያሉ የምሰራቅ ሐረርጌ ወረዳዎች ናቸው። በ20ኛው ክፍለ ዘመን መጀመሪያ እጋማሽ በአካባቢያቸው በተፈጠረ ድርቅ ሳቢያ አሁን ምዕራብ ሐረርጌ በሚባለው የኢቱ ሙረዋ በሬንቶ እና የእርሲ ጁሙጋ በሬንቶ ንዑሰ ጎሳዎች ቀዬ መተው በመሰፈር አሁንም በብዛት ይኖራሉ።

8 ሰይድ አቢዮ በምሥራቅ ኦሮሚያ ሕዝብ ዘንድ የሚወደሱ ዓሊም ናቸው። የዘር ሐረጋቸው ኬንያ ከሚኖሩ እና ዋታ ከሚባል የኦሮሞ ጎሳ እንደሆነ፣ የተወለዱትም በነጌሌ ቦረና መሆኑ ይነገራል። ሰይድ አቢዮ በጅማ፣ ኢሉ አባቦር እና ባሌ እሰልምናን ሲያተምሩ ከቆዩ በኋላ በ1950ዎቹ መጀመሪያ ላይ ወደ ሐረርጌ ተሻገሩ። በአሰተምሯቸውም ስማቸው እየገነ በመሄዱ፣ በተለያዩ ወረዳዎች የእምልኮ ሰፍራ አቋቁመው ሺዎች ይጎርፉባቸው ጀመር። ይህ ሁኔታ ያሳሰበው የአጼ ኃይለሥላሴ መንግሥች የጸጥታ ሥጋት ናቸው በሚል ሰበብ ይዞ ዕድሜ ልክ ከፈረደባቸው በኋላ በግዞት ወደ ጎጃም ወሰዳቸው። በአብዮቱ ወቅት ተለቀው አዲሰ አበባ መኖር ሲጀምሩ ሕዝቡ ልክ እንደበፊቱ ይጎርፍባቸው ሰለጀመረ፣ አዲሱ የደርግ መንግሥትም እንደ ሥጋት ቆጥሯቸው በ1977፣ እኔ ካደኩባት ጁሙጋ 20 ኪሜ ርቀት ላይ በምትገኘው ሚጨታ ከተማ አምጥቶ እንደረሻናቸው አብዱረሺድ አብዱረህማን/ አባ ኡርጂ 'Raammisoo' በተሰኘው መጽሐፋ ውሰጥ አስፍሯል። ሰይድ አቢዮን እኔ ከመወለዴ በፊት ቢገድሉትም፣ ተከታዮቻቸው ተሰብሰበው ድቤ እየመቱ እና ሰማቸውን እያወደሱ ሲያመልኩ በልጅነቴ አይቻለሁ፡

## 2.2. ኦነግን ለመጀመሪያ ጊዜ ያየሁት

ቀደም ብዬ እንደጠቀሰኩት ነባሩ የአካባቢው ሰው የእናቴን ቤተሰቦች የሚጠራቸው ሰላሌ እያለ ነበር። ሰላሌ የመጡበት አካባቢ መጠሪያ ቢሆንም የተወሰደው እንደጎሳ ሰም ነው። የሰላሌ ኦሮሞዎች ትክክለኛው የጎሳ ሰም ቱለማ ነው። ሰላሌ ከሰሜን ሸዋ የመጡ ኦሮሞዎች ብቻ ሳይሆን ክርስቲያን ሆኖ አፋን ኦሮሞ የሚናገር በሙሉ ይጠራበታል። ለምሳሌ ከወለጋ እና ኢሉ አባ ቦራ የመጡ መምህራንም ሰላሌ ተብለው ይጠሩ ነበር። አብዛኛው የአካባቢው ማኅበረሰብ ሰላሌ፣ኖሌ፣ አርሲ፣ኢቱ በሚል የጎሳ እና የአካባቢ ስሞች ስለሚታወቅ፣ «ኦሮሞ› የሚለው ቃል እነዚህን ሁሉ ያቀፈ ወጥ የብሔር ስም እንደሆነ መረዳት የጀመርኩት ኦነግ ወደ አካባቢያችን በግልጽ የመጣ ጊዜ ነው።

ኦሮሞ የሚለውን ቃል እናቴ ጎሳዋን ስትናገር ለመጀመሪያ ጊዜ ከሰማሁ በኋላ ቃሉን ለሁለተኛ ጊዜ የሰማሁት የኦነግ ወታደሮችን በድንገት ያየሁ ዕለት ነበር። አጋጣሚው "ለገ ኩሊ"ተብሎ በሚጠራውና በቀቅሳ ወንዝ ውሰጥ ወዳለው የመንግሥት የቡና እርሻ መኪና ተንጠልጥለን ከመሄዳችን ጋር ይገናኛል። በወቅቱ ሁለት ዓይነት መኪናዎች በዱሙጋ በኩል ይመላለሱ ነበር። አንዱ «ትሬንታ ለማ› እያልን የምንጠራው የጭነት መኪና ነበር፡ለማ አሽከርካሪው ሲሆን መኪናውም በዚያው ሰያሜ ተጠራ። ሁለተኛው መኪና የመንግሥትን የቡና አርሻ መሬት የሚያርስ እንዲሁም ለጭነትም ጭምር ይጠቀሙበት የነበረ ትራክተር ነው።

የዱሙጋ ሕጻናት እነዚህ መኪናዎች ወደ ከተማችን ሲመጡ ከኋላ እየሮጥን በመንጠልጠል አሰከቻልነው እንሄዳለን። ብዙ ጊዜ ከከተማዋ ማዶ ባለው ቂልጡ ካራ ተራራ ዳገት ስንደርሰ እጃችን ይዝላል። ከዚያም እንወርድና እንደ አንኮይ፣ ሮቃና ዶቅማ ያሉ ፍራፍሬዎችን ለቅመን እየበላን እሰከ ዱሙጋ ወንዝ እንጓዛለን። ላብ ያጠመቀውን ሰውነታችንን ታጥበን፡ በለሰ ከቀናን የሰው ማሳ ውስጥ ተደብቀን ገብተን ሙዝ አና ሸንኮራ በልተን ስንጠግብ ወደ ቤት እንመለሳለን።

አንድ ቀን ከተንጠለጠልንበት ትራክተር ወርደን ፍራፍሬ ለመልቀም ወደ ጥሻ ስንገባ፣ ረጅም ጸጉር ያላቸው እና መሣሪያ ያነገቱ ሰዎች ጥላ ሥር ቁጭ ብለው ፍራፍሬ ሲበሉ አየናቸው። ከመደንገጣችን የተነሳ ሰውነታችን ተርበተበተ፡ እነሱ ግን በዝምታ ተመለከቱን። ከእኛ መሀል ጠና ያለና ሲያወራ የሚንተባተብ ሰቡሬ(አብዱልሰቡር) የምንለው ልጅ እነዛ ሰዎች «ኦሮሞ ናቸው፡ ሰው አይነኩም'!›» ብሎ አደፋፍሮ እነርሱ ጋር ወሰደን። የማን ልጆች እንደሆንን ጠይቀው፣ «የኦሮሞ ጦር» መሆናቸውን ከነገሩን በኃላ እንዳየናቸው ለማንም እንዳንናገር አሰጠንቅቀው ሸኙን።

ይሀ ክስተት ከዚያ በፊት ተመሳሳይ ሰዎች ማየቴን አሰታወሰኝ። አንድ ቀን ሼኻ (የአባቴ ጓደኛ) ማሳ ውሰጥ ዘይቱን አና ኮክ ለመልቀም ስሄድ ድምፅ ሰምቼ ወደ አቅጣጫው ሳመራ የቆምኩበት ከሙዝ ግንድ የወዳደቀ ቅጠል አንሸራቶኝ የሆነ ጉድጓድ ውሰጥ ወደቅሁ። የወደቅሁበት ገደል የምድር ሥር ቤት ሲሆን፣ ከአሥር በላይ ሰዎች ልብሰ አየሰፉ፡ አባቴ መሀከላቸው

ባለ መቀመጫ ላይ ተፈናጦ ልብስ ይቀዳል። ልክ ሰውድቅ አባቴ ደንግጬ እንዳልጮህ ዘሎ አፌን ይዞ ልጁ እንደሆንኩ ነግሮ አረጋጋቸው። እኔንም ያየሁትን ነገር ለማንም እንዳልናገር አስማለኝ፤ ከረሜላና ናና የምገዛበትን ሃምሳ ሳንቲም ሰጥቶ ለቀቀኝ። በኋላ እንደተረዳሁት፣ አባቴ እና አብረውት የነበሩት ሰዎች ቱምቱ ፉርዳ ተብሎ በሚጠራው አካባቢ ላለው የኦሮሞ ነጻነት ጦር ልብሰ እና የትጥቅ ቀበቶ ሲሰፉላቸው ነበር።

አብረውት የነበሩት ወጣቶች የኦነግ ወታደሮች ሲሆኑ፣ አባቴ ልብሰ ስፌት ያሰተምራቸው እንደነበር ከዓመታት በኋላ ከእነሱ ውሰጥ አንዱን አግኝቼዉ አጫውቶኛል።

የኦነግን ወታደሮች በዚህ መልኩ ቀደም ብዬ ማየቴ በኋላ ላይ በይፋ ሲመጡ እንድቀርባቸው አደፋፈረኝ። ቁቤ አፋን ኦሮሞን በአጭር ጊዜ ውስጥ በለገ ደርባ የሸንኮራ ማሳ ውሰጥ አሰተማሩኝ።ከቻርተሩ ተገፍተው ከወጡ ከጥቂት ዓመታት በኋላም አንዳንዴ የፍየል እረኛ ሌላ ጊዜ ደግሞ ዘመድ ጠያቂ መስዬ የከተማ እና የገጠር ሕዋስ መካከል መልዕክት እንዳመላልስ ይልኩኝ ጀመር።

አንድ ቀን መልዕክት እንዳደረሰኩ በወያኔ እና በኦሮሞ ነጻነት ሠራዊት መካከል በተደረገ ጦርነት የተወረወረ የቦንብ ፍንጣሪ አቆሰለኝ። መልዕክት የያዘው ወረቀት መንገድ ላይ የምበላው ጭቡጦ በማሰመሰል በእንጀራ ተጠቅልሎ ተሰጠኝ። እኔም ይዤ ደርባ ወንዝ ሰደርሰ፣ መንገድ ላይ መስኖ ውስጥ ይሠራ የነበረ ሽማግሌ አገኘሁ። ከመንገድ ዘወር ካደረገኝ በኋላ ለሁለት የኦሮሞ ነጻነት ሠራዊት ወታደሮች አሰረከበኝ። ከዚያም ከሁለቱ ወታደሮች ሴቷ የተቀበለችኝን ጭብጦ ከፈታች በኋላ በፌስታል የተጠቀለለውን ደብዳቤ ማንበብ ጀመረች። ወንዱ ወታደር ትንሽ ፈንጠር ብሎ ከወገቡ በላይ ልብሱን አውልቆ ገላውን እየታጠበ ነበር። በድንገጤ «እንዳትንቀሳቀስ › የሚል ድምፅ ተሰማ። ቀና ብይ ስመለከት ወታደሮች ከሸለቆው ወዲህ እና ወዲያ መሣሪያ ደግነውብናል። ገላውን እየታጠበ የነበረውም ልጅ እንደታዘዘው በድንጋጤ እጁን ከፍ አደረገ። ሴቷም አንድ እጇን ወደ ላይ አነሳች። በዚህ ጊዜ መጀመሪያ በወንዙ አፋፍ ላይ ድንጋይና እንጨት ተገን አደርገው መሣሪያ የደገኑብን ወታደሮች ከተገናቸው ወጥተው ወደ ወንዙ ቁልቁል መምጣት ጀመሩ።

በዚህ መሀል በድንገት የተኩሰ እሩምታ ከአጠገቤ ተሰማ። ለካ ሴቷ ወታደር አንድ እጇን አንሳች እንጂ ሌላኛው ጉልበቷ ላይ ከነበረ መሣሪያ አልተነሳም። እጅ ያሰጡ መሰሏቸው ወደእኛ ለመምጣት ከተገናቸው የለቀቁቱ የሕወሓት ወታደሮች ወደ ኋላ ዘለው መሬት ይዘው ተኩሰ ከፈቱ። ውኃ ውስጥ ቆሞ እጁን ያነሳውም ልጅ መሣሪያውን ዘሎ አነሳና ሁለቱም እየተኮሱ ማፈግፈግ ጀመሩ፡ እኔም ተከተልኳቸው። ወንዝ ውሰጥ ትንሽ አንደሮጥን በመውደቄ ልጁ መሬት ላይ ሲጎተትኝ ቆይቶ የሆነ ጥሻ ውሰጥ ወሽቆኝ ተፈተለከ።

ከዚያ በኋላ የሆነውን በትክክል አላስታውሰም፡ ቅዠት ከሚመስል እንቅልፍ ስነቃ ሰዎች

በጎንና ጎን ይዘዉኝ ይሄዳሉ። መሬት ላይ በእግሬ አቆማለሁ ስል እግሬን ያመኛል፡ ዝቅ ብዬ ስመለከት በደም ተጨማልቂያለሁ። የዘንጋዳ ማሳ ውሰጥ ካለች አንዲት ጎጆ አድርሰው ደሜን አጥበው፣ ቁስሌን የደቀቀ ኪኒን ነስንሰውበት አሠሩልኝ። በማግስቱ ወደ አያቴ ዘንድ ለመሄድ ሰነሳ «ምናልባት የመንግሥት ሰዎች እዚያም ሊፈልጉሀ ይችላሉ» በሚል ከመሄድ ከለከሉኝ። ለተወሰኑ ቀናት ከአንዱ ማሳ ወደ ሌላው እያሸጋገሩ ከደበቁኝ በኋላ ቁስሌ ሲሽር ወደ ዱሙጋ ለመመለስ ወሰንኩ። ቁሰሉም ከጉልበቴ በታች መጠነኛ ጭረት አንጂ የከፋ ሰላልነበረ ቶሎ ዳነ።

ያክሙኝን ሰዎች ምን እንደሆንኩ ስጠይቅ «የቦምብ ወይም የጥይት ፍንጣሪ ጫር አድርጎሀ ነው። ፈጣሪ ነው ያወጣሀ› አሉኝ። ማክሰኛ የኡንኬc ገበያ ሰላለ ከዱሙጋ የመጡ ገበያተኞችን ተከትዬ ወደ ቤቴ ገባሁ። ቤተሰቦቼ የተከሰተውን አልሰሙም። እንደወትሮው ገጠር ዘመዶቹ ጋር እሸት ስበላ ቆይቼ የመጣሁ መሰላቸው። እንደዛሬው ስልክ በየሰፈሩ አለመኖሩ በጀኝ።

# 2.3 ሀምቢሳ እና ማንጁስ

የልጅነት ጊዜዬን ያሳለፍኩት የፖለቲካ ውዥንብር በሀገራችን እና በአካባቢያችን ላይ ከፍተኛ ጉዳት አያደረሰ ባለበት ወቅት ነው። ኦነግ በአካባቢው ለረጅም ጊዜ መሽጎ ቆይቷል። ደርግ ወድቆ ኦነግ አካባቢውን ማሥተዳደር ሲጀምር በሕዝቡ ዘንድ ተቀባይነት ለማግኘት ብዙ አልተቸገረም። አንደኛ ያሉ ሕጻናት ካልሆኑ በስተቀር ትላልቆቹ ቀድሞውኑ የድርጅቱን ዓላማ ያውቃሉ። ለረጅም ዓመታት በኅቡዕ ሲደራጅ የነበረው ሕዋስ ግልጽ ሆኖ ሥራ ጀመረ። ቀደም ብሎ ከዱሙጋ ጠፍተው ድርጅቱን የተቀላቀሉ ወጣት ወንዶች እና ሴቶች ትጥቅ አንግበው፡ ጎፈሬ አጎፍረው ሲመለሱ በደስታ እና በአግራሞት ሰሜት እየተመለከትን ሥር ሥራቸው እንሮጣለን።

በአካባቢው ከሚንቀሳቀሱ የኦነግ ወታደሮች ውስጥ ሦሰቱ በኋለ ላዳበርኩት የፖለቲካ ንቃት ትልቅ ሚና ነበራቸው። ከእነሱ ውስጥ አንዱ ሀምቢሳ ሰሌ ነው። ሀምቢሳ የኦሮሞ ነጻነት ሠራዊት የአካባቢው ክፍለ ጦር አዛዥ ነበር። ትውልዱ ምሥራቅ ሐረርጌ ሲሆን፣ በጣም መልከ-መልካምና ሕጻናትን አብዝቶ የሚወድ ነበር። ከአካባቢያችን ርቆ በተመለሰ ቁጥር ቁቤ የሰፈረበት መጽሔት ይዞልን እየመጣ ማንበብ እንድንለማመድ ያደርጋል። ሀምቢሳ ከገበሬው ጋር መሬት ይቆፍራል፣ ሽማግሌዎች የተሰባሰቡበት ጥላ ሥር እየሄደ ሰለ አካባቢው ታሪክ ጠይቆ ይረዳል፣ ለቅሶ ይደርሳል፣ የታመመ ሰው መኖሩን ከሰማ በየቤቱ እየዞረ ይጠይቃል። በሽር የሚባል ሾፌር በሚነዳው የእርሱ መኪና ጭኖን ለመኪና የነበረንን ጉጉት ያሰታግስልናል። በዚሀም የተነሳ የአካባቢው ማኅበረሰብ የሱን አመራር በጣም ያደንቅ ነበር።

ኦነግ ከሕወሓት? ጋር ጦርነት ሲጀመር ማዕከላዊ ዕዙን(central command) ከዱመጋ አሥር ኪሎ ሜትር ወደምትርቀው ቱሉ ጢሉ አደረገ። እኛም ከእናቶች ጋር ምግብ ለማድረስ ስንሄድ ሀምቢሳን እናየዋለን። ወላጅ እናቱ አንዴ ልታየው መጥታ ጎረቤታችን አርፋ እንደነበር አሰታውሳለሁ። በኋለ ስሰማ እናቱ ሀምቢሳን ጨምሮ ሰድሰት ልጆቿን ለኦነግ አበርክታ ስድስቱም ተሰውተውባታል። ሀምቢሳ ወያኔ ዱሙጋን ከተቆጣጠረ በኋላ አሰኮ መጨረሻው ሲዋጋ ቆይቶ በምዕራብ ሐረርጌ ዳሮ ለቡ ወረዳ ሀሮ አዲ የተባለ ቦታ ላይ አንደተሰዋ አብረውት ከነበሩ ሰዎች ሰምቻለሁ። ልክ አንደ እኔ በሀምቢሳ የጀግንነት ገድል ያልተቀረፀ የአካባቢው ሕፃን እና ወጣት ያለ አይመሰለኝም፤ ሳድግ እንደሱ መሆን የሁልጊዜም ምኞቴ ነበር።

ወላቡ የተባለ ሌላኛው የኦሮሞ ነጻነት ሠራዊት አባል ከሕወሓት ጋር በተደረገ ጦርነች ዱሙጋ ት/ቤት ግቢ ውስጥ ተሰዋ። ሬሳውን ቀድሞ ያየው ከእኛ ተለቅ ያለ ልጅ ጠርቶን እዚያው ግቢ ውስጥ ጉድጓድ ቆፍረን ቀበርነው። የሰው ሬሳ ለመጀመሪያ ጊዜ ሰላየሁ መሰለኝ፣ የወላቡ ፊትና ጎፈሬ እስካሁንም ከዓይነ-ኅሊናዬ አልጠፋም። ያኔ መቃብሩ ላይ የተከልነው ዋርካ ዛሬ

9 በወቅቱ ከኦነግ ሠራዊት ጋር መሣሪያ ይታኮሱ የነበሩት የሕወሓት ወታደሮች ናቸው። ነገር ግን አካባቢውን የሚያውቁት የኦሕዴድ ካድሬዎች ቦታዎችን በመጠቆምና የሕወሓቶችን የቋንቋ ክፍተት በመሸፈን አብረዋቸው ይንቀሳቀሱ ነበር።

አድጎ ትልቅ ጥላ ሆኗል። ከዉጪ ተመልሼ ዱሙጋ ሰሄድ <<እንደዚሀ ዋርካ እኛ ቄሮዎችም በእነ ወላቡ ደም ላይ ሰለበቀልን፣ የእነሱ መሥዋዕትነት ከንቱ አልቀረም፡ እኛም ቃላችንን አላጠፍንም፤ ትግሉንም እዚሀ አድርሰነዋል › በማለት ሊቀበለኝ ለተሰበሰበ ሕዝብ የወላቡን ታሪክ ገልጫለሁ።

የወያኔ ጦር ዱመጋ በነበረበት ወቅት አማርኛ መናገር ሰለምችል አልፎ አልፎ በአሰተርትጓሚነት አገለግላቸው ነበር። እነሱ እየሰጡኝ እኔ ለጓደኛቼ ከማከፋፍለው ኮሾሮ ይልቅ ከወታደሮቹ የምሰማቸው ታሪኮች ይማርኩኛል። ብዙዎቹ ወታደሮች ገርና ለጋ ወጣቶች ነበሩ። ከእነሱ አንዱ ማንጁስ  ይባላል። ከልጁ ጋር በጣም ሰለተቀራረብን ወደ እኛ አካባቢ ወታደር ሆኖ እንዴት እንደመጣ ነገረኝ። የመጀመሪያ ደረጃ ተማሪ እያለ አንድ ቀን የደርግ ጦር መጥቶ የቤተሰቡን ቤት አቃጠለ። አባቱን ገደሉት፡ ቤተሰባቸውም ተበተነ። በማግስቱ የሕወሓት ወታደሮች ደርሰው ይዘውት ሄዱ። መጀመሪያ ሲላክላቸው ቆይቶ ጉልበቱ ሲጠና ውትድርና ሰልጥኖ ወደ ጦሩ ተቀላቀለ። ደርግ ወድቆ ወያኔ ሥልጣን ሲረከብ ኦነግን ለመዋጋት ተሰማርቶ ሰፈራችን መጥቶ ተገናኘን።

ይሀንን ታሪክ ከከተማው ጠረፍ ኮረብታ ላይ በነበረው ካምፓቸው ሲነግረኝ ሁለት እርስ በእርሳቸው የሚጋጩ ነገሮች መሳ ለመሳ እየተከሰቱ ነበር። በአንድ በኩል ማንጁስ የቤተሰቡን ታሪክ ሲነግረኝ እንባውን መቆጣጠር አቅቶት መላልሶ ይጠርጋል። በሌላ በኩል በወያኔ ጦር ተይዘው የታሰሩ የኦሮሞ ገበሬዎች ዘብ ሆኖ መሣሪያውን ይዞ ይጠብቃል። ይሀ ሁኔታ ብዙ ጥያቄዎች ፈጠረብኝ። ቤተሰቡ ላይ በደረሰ በደል ተገፍቶ ወደ ትግል የገባ ሰዉ፡ አሁን ከቀዬው በሺህ ኪሎ ሜትሮች ርቀት ተጉዞ መጥቶ በሰፈሬ ያሉ ምስኪን ገበሬዎችን አስሮ ማሰቃየቱ ምን ይባላል? ትላንት ጭቆናን ተጠይፎ ያመፀ ሰሜት ዛሬ ሌሎችን ወደ መጨቆን እንዴት ሊሸጋገር ቻለ? የልጁን ሰብዓዊ ባሕርይ በጣም እወደው ነበር። የቤተሰቡን ታሪክ ነግሮኝ ሲያለቅስ እንባዬን አብሬው አፍስሻለሁ። ቆየት ብዬ ደግሞ እዛው ጋር ቁሰላቸው ገና ያልጠገገ ኦሮሞዎች እጃቸው የፊጥኝ ታስሮ መጥተው በአንድ ትንሽዬ ክፍል ውሰጥ ታጉረው ማንጁስ ክላሽ አንግቶ ሲጠብቃቸው ሰመለከት ውስጤ በንዴት ክፉኛ ተንገበገበ። መለሰ ብዬ ሳሰበው ይሀ አጋጣሚ ብሔርተኝነት ገና ከጠዋቱ ውስጤ እንዲያቆጠቁጥ ካሰቻሉ ክስተቶች አንዱ ይመስለኛል።

## 2.4 የአርባጉጉ ጦርነት

ከኦነግ እንቅሰቃሴ በተጨማሪ «የአርባጉጉ ጦርነች» ተብሎ የሚታወሰውና በአማራ እና በኦሮሞ መካከል የተከሰተው ግጭት በልጅነቴ ለብሔር ጉዳይ ቅርብ እንደሆነ ያደረገ ክሰተት ነው። ሰለዚህ ግጭት ለመጀመሪያ ጊዜ የሰማሁት ሰዎች «ቢያ ዱባ» ከሚባል ቦታ ተሰደው ወደ ዱሙጋ በመጡበት ጊዜ ነበር። «ቢያ ዱባ» የሚባሉት ከዱሙጋ ባሻገር በኩሉ ተራራ ጀርባ ያሉ የአሰኮ (አርሲ) አና አንጫር (ምዕራብ ሐረርጌ) ወረዳዎች ናቸው። ከቤተሰቦቻቸው ጋር ተሰደው የመጡ የእኛ እኩዮች ዘመዶቻቸው እንዴት እንደተገደሉ ይነግሩን ገቡ። በተለይ ሐሰን የተባለ ልጅ ታላቅ ወንድሙ በጥይት ተደብድቦ «ውኃ.. ውኃ» እያለ ሲማጸን ውኃ ሰጥቶት ወዲያው እንደሞተበት ተርኮልን ሲያበቃ ለቆሰለ ሰው ውኃ መስጠት ነፍሰን ከማዳን ይልቅ፣ መግደል እንደሚችል ዘግይቶ ከሰዎች መሰማቱን በቁጭት አየተብሰከሰከ አወጋን።

ወደ ኋለ ላይ የእናቴን ቤተሰቦች ለመጠየቅ ደጋ ስሄድ እዚያም ጦርነት ተካሂዶ እንደነበር ተረዳሁ። እዚያው እያለሁ ጦርነቱ ለሁለተኛ ጊዜ ሊጀመር መሆኑ ሰለተሰማ፣ ከአማራዎች ጋር ጎረቤት የሆኑት የእናቴ ቤተሰቦች ለሕይወቴ ሠግተው እዚያው ወረዳ ዋጫሌ የተባለ መንደር ወደሚኖሩ የአርሲ ዘመዶቻችን ቀዬ ሰደዱኝ። በቦታው ዳካ በሚባል አዛዥ የሚመራውን የኦሮሞ ነጻነት ሠራዊት አየሁ። ኦነግ ቻርተሩን ከፈረመ በኋላ ጦሩ ወደ ካምፕ እንዲገባ ሲባል ዳካ አምቢ በማለቱ ከድርጅቱ ጋር ተጣልቶ የተወሰኑ ወታደሮችን ይዞ ወደዚያ አካባቢ እንደመጣ ይነገራል።

ያኔ ይዞኝ የሄደው አያቴ ቶላ ቡሊ በዕለቱ ከዳካ ጋር የነበራቸውን የቃላት ልውውጥ ሁሌ ያነሳል። ሙሐመድ ጂማ (የአህቴ ባል) ሰለሽማግሌው ማንነት ለዳካ ከነገረው በኋላ ዳካ አያቴን በሰሙ ጠርቶ «ቶላ ቡሊ፣ እየተጣሉ ያሉትን አማራ እና አርሲ አንተ አሰታርቃቸው» አለው። አያቴም «እኔ ደካማው ገበሬ ይኸን የሚያክል ጦርነት አንዴት ማሰታረቅ ይቻለኛል? እናንተ ፖለቲካ የምታውቁ ሰዎች ብታስታርቋቸው አይሻልም?» ብሎ መለሰለት። ዳካም ቀጠለና «ቶላ ቡሊ፣ በሁለቱ መሀከል በመግባት ማሰታረቅ የምትችልበት ዕድሉ አለህ። አማራ ሲያጋጥምህ ማተብህን ታሳያለህ፡ አርሲ መንገድ ላይ ሲያስቆምሀ ጎሰሀን ትቆጥርለታለሀ» አለው። የወታደሩ አባባል ሰላሌዎች ከአርሲ ጋር በብሔር፣ ከአማራ ጋር በሀይማኖት ትሰሰር ስላላቸው ሁለቱን ማኀበረሰቦች ለማሰታረቅ እንደሚቻላቸው ለመግለጽ ነው።

በአሜሪካ የዩኒቨርሲቲ ተማሪ ሆኜ በልጅነቴ ሰላየሁት የአርባጉጉ ጦርነት ጥናት የማድረግ ዕድል አጋጥሞኛል። የልጅነት ትውሰታዬ ከመሆኑም በተጨማሪ፣ ለረጅም ጊዜ ኦነግን እና የኦሮሞን ትግል ለማጠልሸት በሚሠሩ ፕሮፓጋንዳዎች ውሰጥ ዋነኛና ተጠቃሽ ተደርጎ ሰለሚነሳ፣ በጥናቱ የተረዳሁትን ፍሬ ነገር ትንሽ ዘርዘር አድርጌ መግለጹ አስፈላጊ ነው ብቆ አምናለሁ።

በአጠቃላይ ጦርነቱ የተደረገው በሰባት ወረዳዎች ነው። አምሰቱ አርሲ ዞን ሲሆኑ፣ ሁለቱ ደግሞ

ምዕራብ ሐረርጌ ናቸው። አምሰቱ የአርሲ ወረዳዎች መርቲ፣ ጮሌ፣ ጉና፣ አሰኮ እና ጎሎልቻ ሲሆኑ፡ ዳሮ ለቡ እና ጉባ ቆሪቻ ምዕራብ ሐረርጌ ሥር ይገኛሉ። ቀደም ብሎ አንደተጠቀሰው በአካባቢው የተለያዩ የኦሮም ጎሳዎች እና አማራዎች ይኖራሉ። የአርሲ ኦሮሞ ጎሳዎች እና ኢቱ ቀደምት ነዋሪዎች ሲሆኑ፡ ቱለማ እና አፍረን ቀሉ (ኖሌ) ዘግየት ብለው የመጡ ናቸው።

በአካባቢው ቁጥራቸው ከፍ ያለ የአማራ ብሔር ተወላጆች የሚኖሩ ሲሆን፣ መጀመሪያ የአጼ ሚኒሊክን ጦር ተከትለው የሰፈሩት እና ኋላ ላይ የመጡት አንድ ላይ ሲደመሩ ብዛታቸው ከፍ ያለ ነው። የአርባጉጉ ጦርነት እነዚህን የማኅበረሰብ ቡድኖች ያሳተፈ ነበር። አርሲ እና ኢቱ በሚኒሊክ ጦር ሲሸነፉ ወደ ተራራ እና ቆላማ አካባቢ በመሸሻቸው፣ ሜዳማውን የደጋ መሬት አማራው መጥቶ ሰፈረበት። ሰላሌዎቹ ሲደርሱ አማራ እና አርሲ የማይጠቀሙውን ሰንደዴማ መሬት አርሰው ለመኖር በመካከሉ ሰፈሩ። አማራ አና ሰላሌ በእርሻ ሲተዳደሩ፣ ኢቱ እና አርሲ በእርሻ እና ከብት ማርባት ተሰማርተዋል።

ኃላ ላይ የመጡት አፍረን ቀሎዎች በበኩላቸው አማራ፣ አርሲ፣ ኢቱ እንዲሁም ቱለማዎች የማይጠቀሙበትን የወንዝ ዳርቻ አካባቢ በመውሰድ መስኖ ማልማት ጀመሩ። እነሱ ከመድረሳቸው በፊት የመስኖ እርሻ አምብዛም አይታወቅም ነበር። አትክልት እና ፍራፍሬ አምርተው በጥቂት ጊዜ ውስጥ ተሳካላቸው። በኃይለሥለሴ ዘመን አብላጫው ምርታቸው በአርቦ እና ሚሰ፣ አንዲሁም በግብር መልክ ለባላባት እና ለመንግሥት ሰለሚገበር፣ ሕይወታቸው ላይ ትልቅ ለውጥ ሳያመጣ ቆይቷል። በዚሁ ሁኔታ እያሉ አብዮቱ ሲፈነዳ ደርግ «መሬት ለአራሹ(› ብሉ አወጀ። የአፍረን ቀሉ ገበሬዎችም አርቦ እና ሚሰ ቀርቶላቸው የመሰኖ መሬት የግላቸው ሆነ። እንደ ቡና፣ ጫት፣ አትክልት እና ፍርፍሬ ያሉ የገበያ ምርቶችን (cash crops) በሰፋት በማምረት በአጭር ጊዜ ውስጥ ባለጸጋ መሆን ጀመሩ።

ይህ ሁኔታ በፊት መሬት ያከራዩዋቸው በነበሩ ሰዎች መንደር የተበለጥን መንፈስ መፍጠሩ አልቀረም። ደርግ ሊወድቅ ጫፍ ላይ ሲደርስ፡ ይሀ የተበለጥን መንፈሰ ወደ እሰጣ-ገባ ተሻጋገረ። በተለይ ብሔራዊ ዘመቻ ዘምተው የነበሩ የአማራ ሚሊሻዎች ደርግ እየተዳከመ መሆኑን ሰለተረዱ፣ ከአባቶቻቸው ተወሰዶ «ለኖሌ « የተሰጠውን ርሰት ለማሰመለስ ዛቻና ማሰፈራራት ጀመሩ። የገዙትን ጠመንጃ እና የውትድርና ሙያ ተማምነው ኖሌዎችን መተናኮሱን ተያያዙት። የደርግ መንግሥት እየተዳከመ በመጣ ቁጥር ውጥረቱ እየጨመረ ሄደ። «ኖሌ « እና «አማራ « የጎሪጥ በሚተያዩበት በዚሀ ወቅት አርሲ፡ ቱለማ እና ኢቱ በዝምታ መመልከትን መረጡ። ምክንያቱም በአንድ በኩል ጠንካራ አካባቢ ዘለል የኦሮሞ ብሔርተኝነት አልነበረም፣ በሌላ በኩል ኖሌዎች በስደት መጥተው በፍጥነት ሀብታም መሆናቸው፣ በሌሎች የኦሮሞ ጎሳዎች ዘንድም ተመሳሳይ የተበለጥን የቅናት ሰሜት ፈጥሯል።

ውጥረቱ በዚሁ አንዳለ፡ የሆነ ቀን ከኤርትራ ዘመቻ ወደ አካባቢው የተመለሰ አንድ የአማራ ወጣት ከብቶቹን ወሰዶ የአንዱ ኖሊ የሸንኮራ ማሳ ላይ አሰማራቸው። ባለማሳው በነገሩ ተናዶና በሰሜት ተገፋፍቶ ወጣቱ ላይ ግድያ ፈፀመ። የወጣቱ ሟች ዘመዶች በበቀል መንፈስ ተነሳሰተው የገዳዩን ብቻ ሳይሆን የኖሌ ማኅበረሰብ የሚኖርበትን ሙሉ መንደር በእሳት አጋዩ። በሰፈሩ የነበረ መስጂድም ጭምር አወደሙ። የአርሲ እና የኢቱ ሰዎች የእስልምና ሀይማኖት ተከታይ ሰለሆኑ፡ በመስጂዱ መቃጠል ተናደው ወደ ግጭቱ ተቀላቀሉ። በአፀፋው በአማራዎች መንደር ላይ በተቃጣ የበቀል እርምጃ ቤተ-ክርሰቲያን ተቃጠለ። በዚህ የተበሰጨት የክርስትና

እምነት ተከታይ የሆኑ ሰላሌዎች ከአማራው ጋር በማበር ወደ ጦርነቱ ገቡ። እስኮ ወረዳ ኢሬሳ በተባለች ትንሽዬ የገጠር መንደር በሁለት ሰዎች መካከል የተነሳው ግጭት በአጭር ጊዜ ውስጥ ሀይማኖታዊ ቅርፅ ይዞ በመስፋፋት፡ ከትንሿ መንደር አልፎ በአጎራባች ወረዳዎች የሰዎች ዕልቂት እና የሀብት ውድመትን አስከተለ።

ደርግ ከወደቀ ከወራት በኋላ፣ኦነግ ክምሥራቅ፣ ኢሕአዴግ ከሰሜን ሲመጡ፣በምዕራብ ሐረርጌ እና በአርሲ አዋሳኝ ወረዳዎች ላይ ጦርነቱ ተጋጋለ። የሽግገር መንግሥቱን ያቋቋሙት ሁለቱ አካላት ጦርነቱን ለማሰቆም መተባበር ግድ ሆነባቸው። ኢሕአዴግ ወደ ሐረርጌ ለመዝለቅ፣ ኦነግ ደጋማውን አርሲ ይዞ በዚያውም ወደ አዲሰ አበባ ለማለፍ ጦርነቱን እንደ እንቅፋት ሰላዩት፣ ሁለቱም እንዲቆም ፈለጉ።

በተጨማሪም ኦነግ የሚታገልለት ሕዝብ በሀይማኖት ድንበር ሁለት ቦታ መከፈሉ ለፖለቲካ ሥራ አላመቸውም። ከኦነግ አባላት መካከል የአካባቢው ተወላጅ ሆነው፡ ቤተሰቦቻቸው ሁለቱን እምነት የሚከተሉ እና በጦርነቱ በተቃራኒው ጎራ የተሰለፉ ብዙ ነበሩ። ኢሕአዴግ እና ኦነግ በመግባባት ከሁለቱም አካላት የተውጣጣ የሰላም እና መረጋጋት ኮሚቴ በማቋቋም ወደ ቦታው ልከው፣ ለጊዜው ግጭቱን አበረዱ። ሁለቱ ድርጅቶች በጋራ ሀገር ከማረጋጋት በተጓዳኝ የየራሳቸውን ፖለቲካ በሕዝቡ ውስጥ ለማሥረጽ ጥረት ማድረግ ጀመሩ። ኦነግ በኦሮሞዎች ላይ ሲያተኩር፣ ሕወሓት/ኢሕአዴግ በአብዛኛው አማራውን ከጎኑ ሊያሰልፍ የሚችል ፕሮፓጋንዳ ላይ አነጣጠረ።

ኦነግ ከሁለቱም ሀይማኖት የተውጣጡ የአካባቢው ተወላጅ ካድሬዎቹን በማሠማራት፡ የሀይማኖት መልክ የነበረው ክፍፍል እንዲቆምና ብሔርተኝነት እንዲፋፋም ሥራ። ሁለተኛው ዙር ጦርነት ከወራት በኋላ ሲጀመር፡ ከሀይማኖት ይልቅ የብሔር መልክ አየያዘ መጣ« ሰለሌዎች ከአርሲ፣ ከኢቱ እና ከአፍረን ቀሎ ጋር ማበር ጀመሩ። በ1983 ዓ.ም የተደረገው የመጀመሪያው ዙር የአርባጉጉ ጦርነት የሀይማኖት መልክ ሲኖረው፣ የ1984/5ቱ ብሔር ተኮር ለመሆንበቃ። ሕወሓት/ኢሕአዴ ኦነግን አሸንፎ አካባቢውን ሙሉ በሙሉከተቆጣጠረ በኋላ የአርባጉጉን ጦርነት ማሰቆም ቻለ።

በ1998 ዓ.ም ከአሜሪካ ተመልሼ ያንን ግጭት ባጠናሁበት ወቅት አካባቢው ከ15 ዓመታት በፊት ያ ሁሉ ደም መፋሰሰና ውድመት የተካሄደበት አይመስልም ነበር። ሰላም ሰፍኖ፣ ማኅበራዊ ትሰሰሮች ተጠናክረው ነው ያገኘሁት። ሕዝቡ ይገበያያል፡ በደቦ አብሮ ያርሳል። ከሁለቱም ወገን በጦርነቱ ላይ የተሳተፉ ሰዎችን አንድ ላይ አግኝቼ ሳናግራቸው ታሪኩን ያጫወቱኝ ቀለል አድርገው ነው። «ከአርባጉጉ ግጭት የምንረዳው ሕዝቦች በቅዕበት ወደ አውዳሚ ግጭት የመግባት ዝንባሌ እንዳላቸው ሁሉ፡ ሲታረቁም በፍጥነት የጦርነት ቁስላቸውን ማሻር እንደሚችሉ ነው" በማለት በጥናቴ መደምደሚያ ላይ አሰፈርኩ።

ከ2010 ዓ.ም ለውጥ ወዲሀ በተለያዩ አካባቢዎች ኦሮሞ እና አማራ መካከል ግጭት ሲከሰት የአርባጉጉን ጦርነት በተሳተፉ አካባቢዎች ላይ ግን ተመሳሳይ ግጭት አልታየም። አንድ አጎቴ እስር ቤት ሊጠይቀኝ መጥቶ ስለዚሁ ጉዳይ ስናወራ «የ1984ቱ ጦርነት አሁን አንዳንጣላ መድኃኒት ሆነልን። ጠባሳ ያለው በእሳት አይጫወትም› ያለኝ እውነት ሳይሆን አይቀርም።

## 2.5 የመጀመሪያዋ አመጽ

ኦነግ ከቻርተሩ ወጥቶ ሕወሓት/ኢሕአዴግ ሀገር ከተቆጣጠረ በኋላ፣ አካባቢያችን አለመረጋጋት ውስጥ ገብቶ ከረመ። ነገሮች መረጋጋት ሲጀምሩ፣ እኔም ወደ ዱሙጋ ተመልሼ ታላቅ እህቴ ጋር እየኖርኩ ትምህርቴን ቀጠልኩ። የገጠር ትምህርት ቤቶች በአብዛኛው ግድግዳቸው ከእንጨት ተሠርቶ በአፈር የሚመረግ ሲሆን፣ የዱሙጋው ግድግዳው ከብሎኬት፣ በሩ ከብረት፡ መሰኮቶቹ በመስታወት፣ ወለሉ ሳይቀር ከሸክላ እና ሴራሚክ የተሠራ ነበር። ይሀም የሆነው ከረጅም ዓመታት በፊት በቤልጅየሞች ስለተሠራ ነው። ወረዳችን ለመስኖ የተመቸ አምስፅት ትልልቅ ወንዞች ሰላሏት፡ ቤልጅየሞች ሰፋፊ የቡና እርሻዎችን መሥርተው ለሕዝቡም ደረጃቸው ከፍ ያሉ ት/ቤቶች እና የጤና ጣቢያዎችን ገነቡ።

ምንም እንኳን መጀመሪያ የቡና እርሻው ሲቋቋም ፈረንጆቹ መሠረተ-ልማቶችን ቢገነቡም፣ የአካባቢው ሕዝብ ከቡና ልማቱ ቀጣይነት ባለው መልኩ ተጠቃሚ ሊሆን አልቻለም። የቡና አርሻው የተመሠረተው ነባሩን ገበሬ በማፈናቀል ሰለሆነ፣ ልማቱ የሰፈሩን ነዋሪዎች ያገለለ ነበር። ሌላው ይቅርና ዘበኞች እና የጉልበት ሠራተኞችን ከሌለ አካባቢ ያሰመጣሉ እንጂ አገሬውን አይቀጥሩም። የአካባቢው ሰው ከብቱ ድንገት ጠፍቶ ቡና ውሰጥ ገብቶ ሳር ከበላ ይታሰራል፣ ወይም በገንዘብ ይቀጣል። መሠረተ-ልማትም ቢሆን መጀመሪያ ፈረንጆቹ ከሠሩት በሰተቀር ሌላ አልተጨመረም።

ሕዝቡ በተነጠቀው መሬት ላይ የለማው ቡና በየዓመቱ ተጭኖ ሲጋዝ የበይ ተመልካች ከመሆን ሌላ አማራጭ አልነበረውም። እርሻው መጀመሪያ ላይ የግል ቢሆንም ደርግ በመውረስ ሙሉ በሙሉ የመንግሥት አደረገው። ከአምሰቱ እርሻዎች ውሰጥ አንዱ በቀቅሳ ወንዝ ውስጥ የሚገኝ ሲሆን፣ ከዱሙጋ በእግር የሁለት ሰዓት ርቀት ላይ ይገኛል።

ስድሰተኛ ክፍል ስማር የእርሻ አሥተዳዳሪውን ተግባብቼ ግቢውን የማየት ዕድል አገኘሁ። በወቅቱ እርሻው ውሰጥ ተዟዙሬ ያየሁት ነገር በጣም አሳዘነኝ። አያቴ ቡና ሰለነበረው ቡና የዘወትር እንክብካቤ እንደሚጠይቅ አውቃለሁ። በዓመት በትንሹ ሁለት ጊዜ ይኮተኮታል፣ በየጊዜው ይታረማል። ለጥላ የሚሆን ዛፍ ያስፈልገዋል። ፍሬው አንደቀላ ይለቀማል እንጂ፣ ጠቁሮ ወይም ደርቆ በራሱ አሰኪወድቅ አይጠበቅም። በበሰለበት ወቅት ድንገት በንፋስ ኃይል ከወደቀ አንድ ሳይቀር ከመሬት ይለቀማል።

የመንግሥት እርሻው የተያዘበት ሁኔታ ግን ከአካባቢው ገበሬዎች ጋር ሲነጻጸር ግድየለሽነት የተሞላበት ነበር። ማሳው ከተኮተኮተ ለዓመታት ሰለቆየ አረም ወሮታል። በዓመት አንዴ አረሙ በገጀራ ይመነጠራል እንጂ፣ ገበሬዎች እንደሚያደርጉት በየጊዜው አይነቀልም። በዚህም ሰበብ አረሙ ወዲያው ያቆጠቁጣል። ቡና በመሰኖ ሲጠጣ ውኃው አፈሩን ንዶት ሥሮቹ እንዳይጋለጡ በዝግታ መሆን ሰላለበት፣ ገበሬው የውኃውን ፍሰት እና ፍጥነት በንቃት ይከታተላል። የመንግሥት እርሻው ውሰጥ ግን የመሰኖውን በይ ከፍተው ይለቁበታል። ቡናው

ሲበሰልም እንጨቱ ላይ ያለውን ብቻ ለቅመው ቀድሞ መሬረት ላይ የወደቀውን እዚያው ትተውት ይበሰብሳል፣ መልሶም አንደችግኝ በቅሉ ከአረም ጋር ይቆረጣል።

በአቅራቢያው ያሉ ገበሬዎች ከእርሻ መሬት እጥረት የተነሳ ምርታቸውን ለማብዛት ሩቡን ሔክታር ደጋግመው አየኮተኮቱና እንደ ሕፃን እየተንከባከቡ ቤተሰባቸውን እንደሚያኖሩ ስለማውቅ፣ በዚያ ማሳ የሚደረገው የምርት መባከን በጣም አናደደኝ። በአንድ ወቅት የታዘብኩትን ብክነት ለትምሀርት ቤታችን ዳይሬክተር ነገሬው፣ ከእርሻው አሥተዳደር ጋር ተወያይቶ ተማሪዎች የወደቀውን ቡና ለቅመው የሚገኘውን ምርት ለት/ቤቱ ገቢ እንዲያደርጉ ተሰማሙ። እኛም በየሰምንቱ የሁለት ሰዓት የአግር ጉዞ አያደረግን በመልቀም ጥሩ ምርት ሰብሰብን እና ሸጠን ለት/ቤቱ ገቢ በማድረግ፣ በጦርነቱ ወቅት የተጎዱ የት/ቤቱን ሕንፃዎች ለመጠገንና የትምህርት መርጃ መሣሪያዎችን ለመግዛት አዋልነው።

የዱሙጋ ት/ቤት እስከ ሰድሰተኛ ክፍል ብቻ ያሰተምር ሰለነበር፣ ሰድሰተኛን ያጠናቀቁ ተማሪዎች የቤተሰቦቻቸው አቅም ከፈቀደ ወደ መቻራ፡ ገለምሶ እና ጫንጮ በመሄድ ሰባተኛ ክፍል ይቀጥላሉ። ብዙዎቹ ተማሪዎች ቤተሰቦቻቸው አቅም ሰለሌላቸው ትምሀርታቸውን አቋርጠው ወደ ንግድ እና እርሻ ለመሠማራት ይገደዳሉ። በእኛ ጊዜ አሰተማሪዎች፣ ተማሪዎች እና ወላጆች ባደረጉት ጥረት ተጨማሪ ክፍሎች ተገንብተው፣ በሁለት ደረጃ እድገ አሰኮ ሰምንተኛ ክፍል ማሰተማር ጀመረ።

በመንግሥት የቡና እርሻ የምርት ብክነትን ተመልከቼ ጥቆማ በመሰጠት ለትምሀርት ቤታችን ጥቅም አንዲውል ያደርኩት ጥረት አስደሳች ትዝታ ትቶ ቢያልፍም፣ ያልተጠበቀ መሥዋዕትነትም አስከፍሎኛል። አንድ ቀን ቡና ለቀማ ውለን ወደቤት ስንመለስ፣ ድንገት የገጠር ወጣቶች ፈንጠር ፈንጠር ብለው ጫካ ውሰጥ ቆመው ጠበቁን። ከመካከላችን አንዲት ልጅ አሟት ደግፈናት በዝግታ አያዘገምን ሰለነበር፣ ከእኔና ከሦስት ሴቶች በሰተቀር ሁሉም ተማሪ ቀድሞን ሄዷል። የመንገዱ መታጠፊያ ጋር አንደደረሰን ከወጣቶቹ መካከል አንዱ ድንገት ሮጦ በመምጣት አንደኛዋን ልጅ ሊይዛት ሲል ደንግጣ ከጀርባይ ተጠመጠመችብኝ፤ ጠለፋ መሆኑ ገባኝ። ጉልበት ተጠቅሞ ቢጎትታትና ቢደበድባትም ከጀርባይ ማላቀቅ አቃተው።

ከፊት የቀደሙን ተማሪዎች የሴቶቹን ጩኸት ሰምተው ወደእኛ አቅጣጫ መሮጥ ጀመሩ። ለጠለፋ ከመጡ ወጣቶች አንዱ ልጅቷን እኔ የከለከልኳት ይመስል «ልቀቃት፤» ብሎ አምባረቀብኝ። ከጀርባይ የተጠመጠመችውን ልጅ ማላቀቅ ብፈልግ አንኳን ላላቅቃት የምችልበት ሁኔታ ውስጥ አልነበርኩም፣ ልጁ ግን ሊረዳኝ አልቻለም። እዚያ አካባቢ «ቡጫ» ተብሎ የሚታወቅ ጫፉ ድቡልቡልና አንደ ቡጢ ወፍራም በሆነ ዱላ ግንባሬ ላይ ነረተኝ። ወዲያው ሽልንግ (ሃምሳ ሳንቲም) የመሰሰሉ ነጫጭ ነገሮች በዓይኔ ሲዞሩ ታየኝ። ከዚያ በኋላ የሆነው ምንም ትዝ አይለኝም። ስነቃ ልጅቷን ጠልፈዋት ሄደዋል፡፡ አብረውኝ የነበሩ ተማሪዎች ጭንቅላቴን በጨርቅ አሥረው፣ አፋፍሰው ወደ መንደራችን አደረሱኝ። የዚያች ዱላ ጠባሳ አሰካሁንም ግንባሪ ላይ ትታያለች።

በቡና ለቀማው በተገኘው ሰኬት ሞራለችን ሰለተነሳሳ የትምሀርት ቤቱን ገቢ የበለጠ ለማጠናከር የሚያሰችሉ እንቅስቃሲዎችን ማከናወን ቀጠልን። አካባቢውን ኦነገ በሚያሥተዳድርበት ወቅት፡አንደ አደም ሐሩን፡ሀሉ ዳዌ እና ከድር ሠዒድ ያሉ አንጋፋ ዘፋኞች ጨፌ ጉዳ ከተባለ ባንድ ጋር ወደ አካባቢያችን መጥተው ብዙ ሕዝብ የሚታደምበት የሙዚቃ ድግስ ይካሄድ

ነበር። በዚህ ድግሰ ለድርጅቱ( ኦነግ) የገንዘብ መዋጮና የዓይነት ድጋፍ ሲደረግ ሰላየን፣ መሰል የገቢ ማሰባሰቢያ ትርዒት አዘጋጅተን ት/ቤታችንን በአቅም ማሳደግ እንደምንችል መምህራኖቻችንን አሳመንን።

ቀጥለን ከገጠር ባሰመጣነው ከበሮ ተማሪዎችን ዘፈን እና ሽጎዬ አለማምደን የመዝናኛ ዝግጅት አሰናዳን። በገጠር መንደሮች በሙሉ ቴፕ ይዘን እያዘፈንን በመዞር ማስታወቂያ ሠራን። በዝግጅቱ ቀንም ከጠበቅነው በላይ ሕዝብ ግልብጥ ብሎ በመውጣት የት/ቤቱን ሜዳ ሞላው። የኪነት ቡድናችን ያቀረባቸው ዘፈኖች ሰሜት ቀሰቃሽ በመሆናቸው ሕዝቡ ሳይሰሰት ድጋፉን ቸረን። ገሚሱ የያዘውን ገንዘብ ሲለግስ፣ ሌላው ፍየል እና ከብት ሊሰጠን በግልም በቡድንም ቃል ገብቶ ሰሙን እና ለመሰጠት የወሰነውን በጥሬ ገንዘብ እና በዓይነት አሰመዘገበ።

ከወራት በኋላ በታዳሚም በገቢም ከመጀመሪያው የላቀ ሌለ ትርዒት አዘጋጀን። ይሄ ሰኬት የኦሕዴድ ሰዎችን ቀልብ ሳበ። በወቅቱ ሕዝቡ በጣም ስለሚጠላቸው፣ በግድ ካልሆነ በሰተቀር የኦሕዴድን ዝግጅቶች አይሳተፍም። ተገዶ የሚሳተፈውም ቁጥሩ ያነሰና ሰሜቱም የቀዘቀዘ ነበር። የእኛን ከፍ ያለ ስኬት ከተመለከቱ በኋላ ለድርጅታቸው የምሥረታ በዓል ትርዒት እንድናሰናዳ አዘዙን። የድርጅታቸውን መዝሙር በጽሑፍ እና በድምፅ ቅጂ አምጥተው ተለማምደን እንድናቀርብ ነገሩን። በዝግጅቱ ቀን አርሲ እና ምዕራብ ሐረርጌ ዞኖችን የሚያዋሰኑ የሰድሰት ወረዳዎች ባለሥልጣናት ተገኙ።

የድርጅቱ ዓርማ ያረፈበትን ከወረቀት የተሠራ ኮፍያ ደፍተን፣ የባሕል ልብስ ለብሰን ዝግጅቱ ተጀመረ። የድርጅቱን መዝሙር የምንዘምርበት ጊዜ ሲደርስ የኪነት ቡድኑ መሪ ሰለነበርኩ ፊትለፊት ቆምኩ። የመድረክ መሪው «የዱሙጋ ት/ቤት ኪነት ቡድን የኦሮሞ ሕዝብ ዴሞክራሲያዊ ድርጅት መዝሙር ሊዘምር ሰለሆነ አንድ ጊዜ ተነሰታችሁ አብራችሁን አንድትዘምሩ በአክብሮት አጠይቃለሁን ብሉ ማይክራፎኑን ለእኔ አስተላለፈ። ሕዝቡ እና ባለሥለጣናቱ መነሳታቸውን ሳረጋግጥ «አንድ .... ሁለት - ሦስት - ብዬ አስጀመርኩ። ሕዝቡ ግን እኛ የተዘጋጀንበትን መዝሙር ትቶ ሌላ መዝሙር መዘመር ጀመረ። ለካ ሕዝቡ የሰማው «የኦሮሞ ሕዝብ መዝሙር» የምትለዋን ንግግር ብቻ ነበር። እኛ የተዘጋጀንበት

*የኦሕዴድ መዝሙር፡-*

*በጭቆና መጎዳታችን*
*ደከመን ሰለቸን*
*ዛሬ ለትግል ተነሳን*
*በአንድነት ታጥቀን . . እያለ ይቀጥላል።*

*ሕዝቡ ግን-*

*የኦሮሞ ባንዲራ የጨለማ ፍካት*
*ያቆምንሽ ዕለት እንወጣለን ከባርነት*
*እንቁ ልጆችሽ ካሉበት ቦታ*
*ሊያቆሙሽ ብለው ወደቁ በተርታ*
*አልፍ አእላፍ ቢሰዋ እናቆምሻለን*
*ለችግል አንሰንፍም ከፊት እንቆማለን*

*የሚለውን የኦነግ መዝሙር ነበር የዘመረው።*

የኪነት ቡድኑ አባላት የሸመደድነውን የኦሕዴድ መዝሙር የተወሰነ ሰንኝ ለመዘመር ብንሞክርም፣ የኦነግን እየዘመረ ያለው የሕዝብ ድምፅ በቀላሉ ዋጠን። እኛም ሕዝቡን ተቀላቅለን አቀለጥነው። ሕዝቡ ሰሜት ውስጥ ገብቶ ሕብረ-ዝማሬው መሬት አንቀጥቅጥ ሆነ። መዝሙሩ አንዳለቀ ዞር ብዬ ስመለከት የመንግሥት ባለሥልጣናት አንገታቸውን ደፍተዋል። ቀጥሎ የወረዳው አሥተዳዳሪና የዞን የድርጅት ኃላፊ በተረበሸ ሰሜት ንግግር ቢያደርጉም የሚሰማቸው ጆሮ ሰላልነበር ዝግጅቱን በአጭሩ ቋጭተው ተመለሱ። ዝግጅቾ የተካሄደው እሑድ ቀን ነበር፡ በነጋታው ሰኞ ፖሊስ የትርዒቱን ዋና አሰተባባሪ መምህር ወደ ጣቢያ ጠራው። ሀገር ሰለም ብሉ ሲሄድ «የኦሕዴድን ዝግጅት ወደ ኦነግ የቀየርክው አንተ ነህ› በማለት የዱላ ውርጅብኝ አውርደውበት ጭንቅላቱ አካባቢ ጉዳት አደረሱበት።

ይሀ ድርጊት ሲሰማ ከፍተኛ ቁጣ ተቀሰቀሰ። የተወሰን ተማሪዎች ተገናኝተን ምን ማድረግ እንዳለብኝ ተወያየን። በማግሥቱ ጠዋት ተማሪዎች ለባንዲራ ዝማሬ በተሰባሰቡበት እኔና የክፍል አለቆች ወጥተን አሰተማሪው ላይ ሰለደረሰው ጉዳች አብራራን። አሰተማሪው ከአሰር ተፈቶ ሕክምና አንዲያገኝ ሰልፍ መውጣት አንዳለብን ተማሪዎችን በማሳመን ከፊት ለፊት ሆነን ወደ ፖሊስ ጣቢያ ተመምን። የገበያ ዕለት ሰለነበር በሰልፍ ሰንሄድ ያየን ነዋሪ እና ከገጠር ለግብይት የመጣ ሕዝብ ከኋላ ተከተለን። ቀደም ብሎ መምሀሩ አንዲታከም የተማጸኗቸውን የአካባቢውን ሽማግሌዎች በጄ ያላሉት ፓሊሶች፣ ከተማሪዎች ጀርባ ግልብጥ ብሎ የመጣውን የሕዝብ አጀብ ሲመለከቱ ያሰሩትን መምሀር አውጥተው አሰረከቡን። እኛም በድላችን ተደሰተን ወደየቤታችን ተበተንን። ይሀ ሰልፍ በጭቆና ሥርዓት ላይ ያደራጀሁት የመጀመሪያው ተቃውሞ ነበር።

የመንግሥት አካላት በዕለቱ ለጥያቄያችን አዎንታዊ ምላሽ ቢሰጡም ቂም አዝለው፡ ነገሩ ከተረጋጋ በኋላ የበቀል እርምጃ ወሰዱ። ለክረምት ዕረፍት ትምሀርት ቤቱ ሲዘጋ የሚጠረጥሯቸውን መምሀራን ወደ ሌላ ቦታ በማዛወር፣ «የመምሀራን እጥረት አለ» በሚል ሰበብ እኔ የነበርኩበትን ሰምንተኛ ክፍል ሙሉ ለሙሉ ዘጉት። ከላይ አንደተገለጸው ት/ቤቱ ከስድሰተኛ ወደ ሰምንተኛ ክፍል ገና በማደጉ፣ ከእኛ በፊት ሰምንተኛ ክፍልን ያጠናቀቀው አንድ ባች ብቻ ነበር።

መምሀራኑን ማባረራቸው ሳይበቃቸው የመማሪያ ክፍሉን በማጠፍ በዓሉን ያበላሸባቸውን ሕዝብ ተበቀሉ። ሰምንተኛ ክፍልን መዝጋት ብቻ ሳይሆን ሌላ ቦታ ሄደን አንዳንማርም መሸኛ ከለከሉን። የተወሰኑ ተማሪዎች በምሥጢር መሸኛ አግኝተው ወደ መቻራ እና ገለምሶ በመሄድ ትምሀርታቸውን ቀጠሉ። የመንግሥት ሰዎች አሰተማሪዎቹ በምሥጢር ለተማሪዎች መሸኛ እየሰጡ እንደሆነ ሲሰሙ የትምሀርት ቤቱን ማህተም ወሰዱት። በዚሀም ምክንያት እኔን ጨምሮ መሸኛ ያላገኘን በርካታ ተማሪዎች ትምሀርታችንን የምንቀጥልበት አማራጭ አጣን።

በተለይ እኔን የመሸኛ ደብዳቤ በመከልከል ብቻ ሳያቆሙ፣ በአካባቢያችን ያሉ ስድሰቱም ወረዳዎች ሄጄ እንዳልማር «ጥቁር መዝገብ» ውስጥ አስፍረውን ደብደቤ ለሁሉም ት/ቤቶች እንደላኩ ሰማሁ። ትምሀርት የመቀጠል ተሰፋ ሰላልነበረኝ እንዲሁም ከተማ ውስጥ መቆየት አስቸጋሪ ሰለሆነ፣ ኤጀርሳ የሚባል ቦታ በመሄድ የእሀቴ ባል ያሰተከለው ወፍጮ ቤች ውስጥ መሥራት ጀመርኩ። እዚያም ከአስተማሪዎቸና ከነዋሪዎች ጋር መግባባት እንደጀመርኩ የመንግሥት ካድሬዎች ባደረጉት ጫና አካባቢውን ለቅቄ ለመሄድ ተገደድኩ።

ቀጥሉ ለገ ደርባ አንድ የአባቴ ጓደኛ ጋር ሄጄ በእርሻ ሥራ ማገዝ ጀመርኩ ይህ ሰው በደርግ

ዘመን እስከ ስድስተኛ ክፍል ተምሮ የሚረዳው ሰው ሲያጣ ወደ ግብርና የተመለሰ ነው። ለብሔራዊ ዘመቻ በግድ ወደ ኤርትራ ሊልኩት ሲሉ ወታደር መሆንና ሞት ካልቀረ ብሎ ኦነግን ተቀላቀለ። የአነግ ወታደር ሆኖ ስድሰት ዓመታት ከቆየ በኋላ፣ ደርግ ሲወድቅ ተመልሶ ሀገሩ ገባ። ኦነግ ከቻርተሩ በመውጣቱ ጦርነት እንደ አዲስ ሲቀሰቀስ ቆስሎ በመማረኩ ሁርሶ እና ሐረር እሰር ቤቶች ለዓመታት ታስሮ ሲፈታ ወደ ቀይው በመመለስ ወደ እርሻ ተሠማራ።

እኔ ባገኘሁት ወቅት ፖለቲካን እርም ብሉ ከእርሻ ባሻገር ሠንጋ በማደለብ ቤተሰቡን ያሥተዳድራል። የሄድኩት ትምሀርቴን የምቀጥልበት ዕድል አሰካገኝ እያገዝኩት ተጠግቼ ለመኖርቢሆንም፣ቶሎ ሰለተግባባን የመሰኖ መሬት አካፍሎ ሰጥቶኝለራሴእንድሠራ ያበረታታኝ ጀመር። ማሳ ውሰጥ ጎጆ ቀልሶልኝ፣ አንድ ሬዲዮም ሰጥቶኝ መኖር ስጀምር ለትምህርት ያለኝ ስሜት እየደበዘዘ፣ በአንጻሩ ገበሬ የመሆን ፍላጎት እያየለ መጣ። እንደሱ ሰፋ ባለ መሬት ላይ የቡና፣ የጫት እና የአትክልት ማሳ ኖሮኝ፡ ገመረዴማ ለብሳ፣ ወገቧን በማንቁጢ መቀነት ሸብ አርጋ፤ ምሳዬን በቀለምሺሽ አናቷ ላይ አሰቀምጣ፣ ሆጃዬን በመቀንጣ አንጠልጥላ ማሳው ድረሰ ይዛልኝ የምትመጣ ቆንጆ ሚስት አግብቼ መኖር ሕልሜ ሆነ።"? ምኞቴንም እውን ለማድረግ ጠንክሬ መሥራት ጀመርኩ። አካፍሎ በሰጠኝ መሬት ላይ የተከልኩት ሸንኮራ እና ሙዝ ቶሎ ፀደቀ። ያፈላሁት የቡና ችግኝ (በከሉ) ፍልቅቅ ብሎ ወጣ። ማሳውንም በልዩ ፍቅር መንከባከቡን ተያያዝኩት።

10 ማንቁጢ ሰዴታ በሚባል ነጭ ቀሚሰ ላይ የሚታሰር መቀነት ነው። ዋጋው ወደድ ሰለሚል ለሚያገባት ኮረዳ ማንቁጢ መገዛት የሚችለው ጥሩ ገቢ ያለው ጎበዝ ገበሬ ወይም ነጋዴ ብቻ ነው። ቀለሞሺሽ ደግሞ ሚስቶች በማሳ ውሰጥ ስራ ላይ ላሉ ባሎቻቸው ምሳ የማያወጡበት ከሀብረቀለማት ሰንደዶ የሚሰራ እቃ ነወ= መቀንጣ እንገቱ ረዘም ያለ ቅል ሲሆን፣ በወይራ ጪስ ታጥኖ ሆጃ የሚባል ወተት፣ ውሃና የቡና ቅጠል ቀላልቅሎ በማፍላት የሚዘጋጅ ለጫት ማወራረጃ የሚረዳና ሰራ ላይ ላለ ባል የሚቀርብ መጠጥ ነው: አዲስ ያገባች ሴት ወገቧን በማንቁጢ ሸብ አድርጋ፣ ቀልምሺሿን ያለ እጇ ድጋፍ በነጻ እናቷ ላይ አስቀምጣ፣ በአንድ እጇ መቀንጣዋን አንጠልጥላ ሌላኛዋን እያወርጨች ሰትሄድ የሚሰጣት ውበት ልብ ያስምጣል። ታዳጊ ወጣቶችም አንድ ቀን እንደዚያ አይነቷን ሚስት እንዲኖራችው ይመኛሉ።

# ከፍል ሦስት - የሀገር ውሰጥ ስደት

# 3.1 አሰላ

በትምሀርቴ ተሰፋ ቆርጬ ገበሬ ለመሆን በመወሰን ሸርጤን አገልድሜ ቁፋሮ ላይ ሳለሁ፣ አንድ ቀን የሆነ መንግሥታዊ ያልሆነ ድርጅት (NGO) ሠራተኞች ወደ ሐረርጌ ለማለፍ መኪናቸውን እየነዱ ለገ ደርባ ከተፍ አሉ። ተጓዦቹ እራት ሲሆኑ ሁለቱ ፈረንጆች ነበሩ። አሽከርካሪው እና አሰጎብኚው ኢትዮጵያዊያን ቢሆኑም አፋን ኦሮሞ አይችሉም። መኪናቸውን ወተት የሚሸጥበት ቦታ አቁመው ሰለ አካባቢው እና የሚሄዱበትን አቅጣጫ ሲያጠያይቁ መግባባት ተሳናቸው። ቋንቋ የሚችል ሰው ሲባል ከማሳው ተጠርቼ ሄድኩኝ። ከሁለቱ ሰዎች ጋር በአማርኛ፣ ከፈረንጆቹ ጋር ከትምሀርት ቤት በቃረምኳቸው ቁንጽል የእንግሊዝኛ ቃላት አወራን። ፈረንጆቹ የጉዚቸው ዓላማ ሀገር መጎብኘት አንደሆነና አሰጎብኒው ግን የአካባቢውን ቋንቋ ሰለማይናገር ብዙ ሊረዳቸው አንዳልቻለ ገልጸውኝ እሰከ መቻራ ከተማ መንገዱን እንድመራቸው ተማጸኑኝ። ሁለት መቶ ብር ሊሰጡን ቃል ገቡልኝ።

በሐሳባቸው ተማምቼ ጉዞ ጀመርን። በመንገዳችን ላይ አልፎ አልፎ እያቆሙ ሰለ መሬቱ አቀማመጥ፡ የሕዝቡ አፈር፣ ታሪክ እና ባሕል እንዲሁም የኢኮኖሚ እንቅሰቃሴ እየጠየቁኝ እኔም የአቅሜን እያብራራሁ፣ እነሱ ፎቶ እያነሱ ጉዟችንን ቀጠልን። መንገድ ላይ የሚያዩኝ ሰዎች “የኪነት ተማሪው” እያሉ ሞቅ ባለ ስሜት ያናግሩኛል። በዚህ ሁኔታ ከፈረንጆቹ ጋር በመንገዳችን ሕዝቡን እያናገርንና እኔም ገለጻዬን እየሰጠሁ መቻራ ሰንደርሰ መሸና ማደር ግድ ሆነ። ከተገናኘን ጀምሮ ትምህርቴን ያቋረጥኩበትን ምክንያት እየጠየቀኝና አንድመለሰበት እየገፋፋኝ ወደ እርሻ ያደላች ነፍሴን ወሰወሷት።

በማግሥቱ ከመቻራ ልመለስ ሰል ገለምሶ ካላደረሰከን ብለው ሰለወተወቱኝ እብሬያቸው ሄድኩ። የከተማውን ሕዝብና አኗኗሩን ማወቅ እና መረዳት ሰለፈለጉ ገለምሶ ውለው ለማደር ወሰኑ። ከገለምሶ ሲነሱ «እዚሀ ከደረስክ አይቀር አዳማ እና አዲስ አበባን የመሳሰሉ ትልልቅ ከተሞች አይተሀ ትመለሳለሀ፣ የትራንሰፖርት ወጪውን በእኛ ጣለውን ብለው አደፋፈሩን። የተባሉትን ከተሞች የመጎብኘት ጉጉት፣ ለረጅም ጊዜ የተለየኋት የአሰላ ነዋሪዋ አህቴ ናፍቆት ተጨምሮበት ሐሳባቸውን ተቀበልኩ። አዳማ ስንደርሰ መሸ። ያን የሚያሀል ትልቅ ከተማ፡ ብዛት ያለው መኪና እና ዓይን የሚያጠፋ መብራት አይቼ ሰለማላውቅ በጣም ተገረምኩ። ማታ ከተማ ውስጥ በመኪና ትንሽ ዞር ዞር ካልን በኋላ ሆቴል አደርን። አሰላ ቢሮ ሰላላቸው እዚያም ሊያደርሱኝ አንደሚችሉ በነገሩኝ መሠረት ጠዋት ወደዛው አመራን።

አሰላ እህቴ ጋር ሄጄ አንድ ሳምንት እንደተቀመጥኩ የደንብ ልብስ (uniform) ለብሰው የሚሄዱ ተማሪዎችን ስመለከት ቅናት አደረብኝና የመማር ፍላጎቴ አገረሸ። የእህቴን ባል ሙሐመድ ጅማን አናገርሁት። ሙሐመድ ከልጅነቱም ትምህርት ላይ ስለሚያበረታታኝ እና ስለሚደግፈን፣ እንደ አማች ሳይሆን እንደ ታላቅ ወንድም ነበር የምመለከተው። ወደ ደርባ ተመልሼ ገበሬ የመሆን ሕልሜን ትቼ፣ ትምህርት እንድጀምር ተወሰነና የሚቀበለኝ ትምህርት ቤት ወደመፈለጉ ገባን።

ነገር ግን ዞረን ያናገርናቸው የትምህርት ቤት ዳይሬክተሮች ሊቀበሉኝ ፈቃደኛ አልነበሩም። ምክንያቱም የምዝገባ ጊዜ አልፎ ሴሚስተሩ ወደ መጠናቀቁ ተቃርቧል፡ በዚያ ላይ የመሸኛ ደብዳቤም ሆነ ትራንስክሪፕት የለኝም። ይባስ ብሎ የመጣሁበትን አካባቢ ኦነግ በስፋት የሚንቀሳቀስበት እንደሆነ ሰለሚታወቅ፣ ጥርጣሬ እና ፍርሀት አደረባቸው። የአንዱ ት/ ቤት ዳይሬክተር ትውልዱ እኔ የመጣሁበት አካባቢ ስለነበረ፣ ሆዱ ይራራልናል ብለን ተሰፋ ብናደርግም ማንነቴን እና የመጣሁበትን ቦታ እንዳወቀ በፍጥነት ከቢሮው አባረረን።

በመጨረሻም ቅድስተ-ማርያም በሚባል የካቶሊክ እርዳታ ድርጅት (Mission) የሚመራ የግል ት/ቤት ሄድን። እኛ ስንገባ የትምህርት ቤቱ ርዕሰ-መምህር እና የተወሰኑ አስተማሪዎች ስብሰባ ላይ እያሉ ብንደርስም ሙሐመድን ስለሚያውቁት ተነስተው ሰላምታ አቀረቡልን። ለምን ጉዳይ አንደመጣን ሲጠይቁን መማር እንደምፈልግ ነገርኳቸው። ዳይሬክተሩ «በሴሚስተር መጨረሻ መጥቶ መዝግቡኝ የሚል ተማሪ ምን ዓይነት ነው?» ሲል በአግራሞት ተናግሮ፣ ጸሐፊዋን በመጥራት «ለጊዜው አንድ ክፍል ውሰጂውና ጉዳዩን አጣርተን እንወስናለን አላት።

እሷም ትዕዛዙን ተቀብላ፣ ስምንተኛ ክፍል አድርሳኝ፣ ለመምህሩ ከነገረችልኝ በኋላ ወደ መማሪያ ክፍሉ ገባሁ። ወንበር ፈልጌ ስቀመጥና ተማሪዎቹ ፈተና ለመፈተን ወረቀት አውጥተው ሲዘጋጁ አንድ ሆነ። ወረቀትና እስክሪብቶ ጎኔ ከተቀመጠችው ልጅ ተውሼ ፈተናውን ከሰሌዳው እያነበብኩ መልሱን መጻፍ ጀመርኩ። ልክ እዚያው ክፍል ሲማር እንደከረመ ተማሪ ፈተናውን ተፈትኜ ወደ ቤት አቀናሁ።

በማግሥቱ ደብተር እና እስክሪብቶ ገዝቼ በማለዳ ትምህርት ቤት ደረስኩ። ባለፈው የፈተነን አስተማሪ ፈተናውን አርሞ መጥቶ ስም እየጠራ ለሁሉም ተማሪዎች ሲሰጥ ቆየና፣ የእኔን ወደኃላ አስቀርቶ «ጀዋር ሲራጅ የተባለ ተማሪ አዚህ ክፍል አለ?» ሲል ጠየቀ። እኔም «አዎ አለሁ፣ እኔ ነኝ» ብዬ ተነሳሁ። እንደ አጋጣሚ ሆኖ ከክፍሉ ያንን ፈተና «የደፈንኩትን እኔ ብቻ ነበርኩ። ይህን ያስተዋለው መምህር ወደ ውጪ ይዞኝ ወጥቶ ለብቻዬ አናገረኝ፡ እኔም ያጋጠመንን የሕይወት ውጣ ውረድ ዘርዝሬ ተረኩለት።

አስተማሪውም ታሪኬን ሰምቶ ሲጨርስ፣ ችግርን ተረድቶ ወደ ርዕሰ መምሀሩ ዘንድ ይዞኝ በመሄድ የነገርኩትን አሻሽሎ ነገረው። «ከተራ ዱርዬ ጋር ናላችን ሲዞር እየዋለ፣ ለዚህ ጎበዝ ልጅማ ዕድል ልንሰጥ ይገባል› ›ብሎ ለዳይሬክተሩ አስረዳ። ዳይሬክተሩም በመንፈቅ ዓመቱ የዕረፍት ወቅት መሸኛዬን እንዳመጣ ነግሮኝ ለጊዜው ትምህርቴን እንድቀጥል ፈቀደልኝ። እኔም ከባቢውን ተላምጄ፣ ብዙም ሳይቆይ በተሰጠው የሴሚስተር ማጠቃለያ ፈተና ጥሩ ውጤት አስመዘገብኩ። በዚሁ ውጤቱም የተነሳ በትምህርት ቤቶች መካከል በሚደረግ የጥያቄ እና መልስ ውድድር ተሳታፊ ሆኜ የትምህርት ቤቴን ስም ማስጠራት "ሀ" ብዬ ጀመርኩ። የትምህርት ቤቱ መምህራን እና አመራሮች እየወደዱኝ ሰለመጡ በመንፈቅ ዓመቱ አምጣ

የተባልኩት መሸኛም ተረሳልኝ።

የስምንተኛ ክፍል ብሔራዊ ፈተና በትምህርት ቤቱ እና በዞኑ ከፍተኛውን ውጤት በማምጣት ወደ ዘጠነኛ ክፍል ተዛወርኩ። ዘጠነኛ ክፍልም እዚያው አሰላ ጭላሎ ሁለተኛ ደረጃ ት/ቤት ተመድቤ መማር ጀመርኩ። እዚህ ት/ቤት በቆየሁባቸው ጊዜያት ካሳለፍኳቸው ትዝታዎች ጥቂቱን ላካፍላችሁ።

የመጀመሪያው ትውስታዬ የዘጠነኛ ክፍል የፈተና ውጤት ሲመጣ ከክፍሌ አንደኛ፤ በአጠቃላይ ካሉት (ከአሥራ አምስት በላይ የነበሩ ይመስለኛል) ክፍሎች ሦስተኛ ከመውጣቴ ጋር ይገናኛል። ሁለተኛው ሴሚስተር እንደተጀመረ የክፍላችን ኃላፊ ሆኖ የተመደበ አንድ አስተማሪ ገና ከመግባቱ ሰሜን ተማሪዎች ፊትለፊት ጠርቶ ጉብዝናዬን በማንሳት በአማርኛ አሞጋገሰኝ። ከስሙ በመነሳት ኦሮሞ መሆኑን ስላወኩኝ፣ እኔ የመለስኩለት በአፋን ኦሮሞ ነበር። አስተማሪው በመደነቅ «ኦሮሞ ነህ?» ሲለኝ በልበ ሙሉነት «አዎ» ብለውም አላመነኝም። «አንተ ኦሮሚያ ውሰጥ ያደክ ጉራጌ ነህ እንጂ፣ በጭራሽ ኦሮሞ አይደለህም›» አለኝ። «ኦሮሞ መሆኔን ለምን ተጠራጠርከን» ስለው፡ «እዚህ ት/ቤት ያሉ የኦሮሞ ተማሪዎች የከተማ ዱርዬዎች ናቸው፡ እንደዚ ዓይነት ውጤት አያመጡም» ሲል መለሰልኝ።

ይሀ ንግግሩ እልህ ስላስያዘኝ ከሁሉም ክፍል ጥሩ ውጤት ያመጡ የኦሮሞ ተማሪዎችን አፈላልጌ በመተዋወቅ በቡድን ማጥናት ጀመርን። ያኔ የአሰላ መስጂድ አሰተማሪዎችን በመቅጠር ሙስሊም ለሆኑ ጎበዝ ተማሪዎች ቅዳሜ እና እሑድ የማጠናከሪያ ትምህርች (tutorial) ይሰጥ ነበር። እኔም ካሰባሰብኳቸው ተማሪዎች መካከል የተወሰኑት ክርሰቲያን ቢሆኑም፣ የማጠናከሪያ ትምህርቱን የሚሰጡት መምህራን ብሔርተኞች ሰለነበሩ እንዲማሩ ፈቀዱልን። ሁላችንም ትምህርታችንን በትጋት እያጠናን እና በሞራል እየተጋገዝን ጠንክረን ሠራን።

በዚሁ መሠረት የኦሮሞ ተማሪዎች በሁለተኛ ሴሚሰተር ከክፍልም ሆነ ከአጠቃላይ ት/ቤት ከፍተኛውን ደረጃ መቆጣጠር በመቻላችን አኩሪ የሆነ ታሪክ አስመዘገብን። እኔም ከአጠቃላይ ክፍሎች አንደኛ ስለወጣሁ በወላጆች ቀን ሽልማት ተሰጠኝ። በዕለቱ ስሜ ተጠርቶ ሽልማቱን ተቀብዬ ከመድረክ ስወርድ አንድ ሥርዓት አስከባሪ መምህር እጄን አፈፍ አድርጎ ያዘኝና «ሌባ፣ የሌላ ሰው ሽልማት ነው የወሰድከው አይደል?» ብሎ የተሸለምኩትን መዝገበ ቃላት እና የእጅ ሰዓት ቀማኝ። የሚያውቀኝ አስተማሪዎች እኔው መሆኔን ቢነግሩትም እሱ ግን « አይደለም፣ ይሄ በአጥር ላይ እየዘለለ ያስቸገረን ዱርዩዬ ነው!» በማለት ተከራከራቸው። ለነገሩ እሱም መምህራኑም ከእውነታው ብዙም አላፈነገጡም።

ለጥቂት ቀናት ከከተሜ ጓደኞቼ ጋር ለመዝናናት በአጥር ሾልከን ስንወጣ በአጋጣሚ ተይዤ አውቃለሁ። ለመጀመሪያ ጊዜ ፍቅረኛ የያዝኩበት ወቅት ሰለነበረ፣ በዕረፍት ሰዓት እሷ ጋር ፅድ ሥር ቁጭ ብለን ስናወራ ደውል ሳንሰማ ረፍዶብን የተያዝንበት ጊዜም አለ። ሆኖም የዱርዬነቱን ውንጀላ ሽምጥጥ አድርጌ ክጄ፣ በክፍል ውስጥ የሚያውቁን አስተማሪዎቹ እንደመሰከሩልኝ ጨዋና ጎበዝ ተማሪ መሆኔን ተከራክሬ ሽልማቴን ተቀብዬ ሄድኩ።

ሌላኛው የጭላሎ ት/ቤት ትዝታዬ ሐጂ ዋዮ የሚባሉ ሸማግሌን ይመለከታል። ሐጂ ዋዮ የአሰላ ተወላጅ ናቸው። በአንድ ዕለት ከእኛ ጋር የሚማሩት ልጆቻቸው ከሌሎች ተማሪዎች ጋር ክፉኛ ተደባድበው ጉዳያቸው ለሥነ-ሥርዓት ኮሚቴ ቀረበ።

ከተማሪ፡ ከወላጆች እና ከመምህራን ተውጣጥቶ የተዋቀረው የሥነ-ሥርዓት ኮሚቴ የልጆቹ

ጥፋት ላይ በዝርዝር ከመከረ በኋላ እንዲባረሩ ወሰነባቸው። ውሳኔው በተላለፈ ማግሥት ሐጂ ዋዮ ከዘራ ይዘው የዳይሬክተሩን የቢሮ በር በኃይል ገፍትረው ገቡና በከባድ ቁጣ ከዘራቸውን ወደ ዳይሬክተሩ እየጠቆሙ፣ «ይሄ ቦታ ስሙ ምን ይባላል »አሉት። ዳይሬክተሩ ግራ ተጋብቶ ዓይን ዓይናቸውን ተመለከተ። ሐጂ ዋዮ ደግመው የዚች ከተማ ሰም ማነው? »ብለው ጠየቁት። ዳይሬክተሩም «አሰላ ነዋ» አላቸው። «አዎ ይቺ ቦታ አሰላ ናት፤ እኔም አሰላ ነኝ፣ ልጆቹም አሰላ ናቸው፣ ይህ ቦታ ምድሩም ሰማዩም አሰላ ነው፤ አንተ ትሄድ ይሆናል እንጂ ልጆቹ የትም አይሄዱም ! »በማለት እየዛቱ ልጆቹን ለማባረር በተላለፈው ውሳኔ ላይ ቁጣቸውን ገልጸው በመጡበት ፍጥነት ወጡ።

ነገሩን እዚያው ቆሜ ያዳመጥኩ ቢሆንም ሽማግሌው ለማለት የፈለጉት ነገር በጊዜው አልገባኝም። ይህ ከመፈጠሩ በፊት አንድ የአማርኛ አስተማሪ የከተማዋ ስም የመጣው «አሰላ» (አሰላሰለ፣ አሰበ) ከሚል የአማርኛ ቃል ነው ብሎ ሲናገር ስለሰማሁ፣ እውነት መስሎኝ ነበር። ሐጂ ተቆጥተው ከወጡ በኋላ እና ዳይሬክተሩ የአካባቢው ተወላጅ የሆነ ሌላ መምህር ጠርተን ሽማግሌው ያለውን እንዲያብራራልን ጠየቅነው። እሱም «አሰላ» በአካባቢው የሚኖረው የአርሲ ኦሮሞ ንዑስ ጎሳ መጠሪያ መሆኑንና ሐጂ ዋዮም የአሰለ ጎሳ አባል መሆናቸውን ነገረን።

ይህን ሲሰማ ዳይሬክተሩ የበለጠ ደነገጠ። ኮሚቴው ለስብሰባ ተጠርቶ በልጆቹ ላይ የተላለፈው ውሳኔ እንዲሻር ሐሳብ አቀረብኩ። ስብሰባው ላይ ታድሜ «የመጀመሪያው ውሳኔ ልጆቹን ሆን ብሎ በብሔራቸው ለመጉዳት የተላለፈ እንደሆነ ተደርጎ በአካባቢው ማኅበረሰብ ሰለተወሰደ ትልቅ ቅራኔ አሰነስቷል» በማለት ነገሩን ወደ ፖለቲካ ለጥጬ አቀረብኩት። ብዙዎቹ ሐሳቤን ሲቀበሉት፣ የተቀሩት ግን ተናደዱ። የተላለፈው ውሳኔም በአብላጫ ድምፅ ተሠርዞ ልጆቹ ወደ ትምህርት ገበታቸው እንዲመለሱ ተወሰነ።

ሌላም አንድ የጮላሎ ትዝታ ልጨምር። ትምህርት የጀመርኩ ሰሞን የሒሳብ አስተማሪያችን አንድ ፎርሙላ ሰሌዳ ላይ ጻፈ። የጻፈው ፎርሙላ ስሕተት መሆኑን ተረድቼ እጄን በማውጣት «መምህር ሁለተኛው መስመር ላይ ተሳስተኻል› ብዬ ነገርኩት። መምህሩም ዙሪያ ገባውን ተመለከተና «ማንን እያናገርክ ነው?» አለኝ። «አንተን ነዋ» ብዬ መለስኩለት። ወደ ኋላው ገልመጥ ብሎ «ከእኔ ውጪ ሌላ ሰው አለ እንዴ?» ሲለኝ፣ «አይደለም መምህር ላንተው ነው እየነገርኩ ያለሁት»አልኩት። «ተነስ ደብተርህን ይዘህ ውጣ !» ብሎ ንዴት በተሞላበት ድምፅ አምባረቀብኝ። ደንግጬ እንደታዘዝኩት ተነሰቼ ከክፍል ስወጣ፣ ተከትሎኝ በመምጣት ዳይሬክተሩ ቢሮ ወስዶ በሩ ላይ ትቶኝ ወደ ውሰጥ ዘለቀ። ትንሽ ቆይቶ ሲመለሰ ዳይሬክተሩ ጠርቶ ወደ ውሰጥ አስገባኝ።

ዳይሬክተሩም «መምህሩን ለምን አናደድከው?» ሲል ጠየቀኝ።

«እረ! እኔ ምንም አላጠፋሁም። ምን አጠፋ ነው ያለሀ?» በማለት ጥያቄውን በጥያቄ መለስኩ።

«ናቀኝ ነው የሚለው» የዳይሬክተሩ መልስ ነበር።

«እረ እኔ አልናኩትም »አልኩ ራሴን በመከላከል ስሜት፡

«እስቲ ምን እንደተፈጠረ አስረዳኝ »አለኝ።

«ፎርሙላ ሲሠራ ስለተሳሳተ፣ "መምህር ተሳስተኻል" ብዬ ጠቆምኩ። ያናደደው ስሕተቱን መጠቆሜ ከሆነ ይቅርታ እጠይቀዋለሁ› በማለት አስረዳሁ። ዳይሬክተሩ ንግግሬን ሲሰማ ቆይቶ ነገሩ ስለገባው ከት ብሎ ሣቀ። «አንተ አንዴት ትልቅ ሰው ለዚያውም አስተማሪህን አንተ ብለህ እንደ ቆሎ ጓደኛህ ታናግረዋለህ?›» አለ እየቀለደ። «አርሲ እና ሌሎች ቦታዎች በዕድሜ ተለቅ ያሉ፣ መምህራን፣ የመንግሥት ባለሥልጣናት የመሳሰሉ ሰዎች በአማርኛ እርስዎ እንጂ አንተ አይባሉም። "እርሰዎ " ማለት ክብር ሲሆን፣ "'አንተ'' ማለት ግን ንቀትን ያሳያል» በማለት የተፈጠረውን ችግር አስረዳኝ። እኔ ያደኩበት አካባቢ ሽማግሌም ሆነ ወጣት፣ ታናሽም ሆነ ታለቅ ''አንተ'' ብለን እንደምንጠራ ነገርኩት። እርሱም ሐረማያ ዩኒቨርሲቲ እንደነበረና የምሥራቁን አካባቢ አነጋገር አንደሚያውቅ፣ ነገር ግን የማያውቁ ሰዎች ሊከፉ ስለሚችሉ እንድጠነቀቅ መከረኝ። የተቀየመኝን መምህር ጠርቶ የተፈጠረውን የግንዛቤ ችግር ካስረዳው በኋላ አስታርቆ ሸኘን።

ከዚያ በኋላ ሌላ ስሕተት ውስጥ ገብቼ ሰዎችን ማስቀየም እና ማዋረድ ስሳልፈለኩ «የአርሲን ሥርዓት» ቀሰ በቀስ መማር ጀመርኩ። ሆኖም ዛሬም ድረሰ አስቀድሜ ካላሰብኩበት በስተቀር አንድን ግለሰብ ሽማግሌም ሆነ ባለሥልጣን "አንቱ'' ብሎ መጥራት አይቀናኝም። ብዙ ጊዜ መጀመሪያ ላይ እርስዎ ለማለት እራሴን ባስገድድም፣ በኃላ በንግግር መሀል ድንገት እረሳና አንተ ወደማለት እመለሳለሁ።

# 3.2. የፍቅር ወላፈን

በጹመጋ ጫት መቃም የባሕሉ አባል ሲሆን አሰላ ላይ አንዳንድ አዛውንቶች ቢቅሙም ለወጣቶች ግን አንደ ከባድ ነውር ተደርጎ ይታያል። ጫላሉ ስማር ቅዳሜ እና እሑድ ከዘመዶቹ የምትተርፈውን ትንሽ ቡልቴ (ያደረ) ጫት ይዤ አጠናለሁ፤ ይህ ነገር በት/ቤቱ ተሰማና የክፍል ንደኞቹ ሊያዩኝ መጡ። አንዷት ጠባብ ሰርቪስ ክፍል ተሰጥታኝ ነበርና ግድግዳዋን በጋዜጣ፡ ወለሏን በሰሌን አሰማምሬ አጣን አጭሼባት ጠበቅኳቸው። ልጆቹም በክፍሏ ውበት እና በጨዋታዬ ድምቀት ተስበው በየሳምንቱ መመላለስ ጀመሩ። ከጫቴ አጠገብ ያለውን ለውዝ እና ስኳር መቀማመስ፣ቀጥሎም ሰኳር የዘገኑበትን የጫት ቅጠል ወደ ማኘክ ተሸጋገሩ። በሴሚስተሩ መጨረሻ ላይ ጫት ገዝተው ቀድመውኝ ቤት ደርሰው ክፍሏን አጫጭሰው ይጠብቁኛል፣ በዚህም የስኳር፣ የለውዝ እና የእጣን ወጪ ቀነሰልኝ።

አንድ ቀን ብዙ እንግዶች እሀቴ ቤት እየቃሙ እያለ፡ ምሽት ላይ ጫት አልቆባቸው እኔ እና መላኩ የሚባል ልጅ እንድንገዛ ተላክን። ጫት የሚሸጥበት አካባቢ ደርሰን ስንጠይቅ፣ ሻጩ ፈትቶ አሳየንና እንደሚሆን ተስማምተን ብር ስንከፍል፣ ጫቱን በኮባ ቅጠል ጠቅልሎ ሰጠን። አኛም ተሸክመን ቤት አድርሰን ለተሰበሰቡት ሰጥተን ፣ ዱዓ አድርገውልን ሲፈቱት አሰቀድሞ የተቃመ/ገራባ ነው። ልንሸውዳቸው ያደረግን መስሏቸው ሲጮሁብን በድንጋጤ ሮጠን ሻጩ ጋር ስንመለስ የለም። ለካ እውነተኛው ሻጭ ጨርሶ ወደቤቱ ሲገባ፣ ዱርዬዎች ቦታው ላይ ተቀምጠው ጠብቀውን ሿሿ ሰርተውን ኖሯል፤

አሰላ የነበርኩበት ወቅት የአፍላነት ዘመኔ ስለነበር አብረን ከምንማር አንዷት ልጃገረድ ጋር ለመጀመሪያ ጊዜ በፍቅር ወደኩ። በግልጽ አብሮ ማውራት እና መታየት ስለሚያሰፈራ፡ከሰፈር ርቀን በድብቅ መገናኘት ጀመርን፤ ይህ የድብቅ ፍቅር ቶይቶ ብዙ መዘዝ አመጣብኝ።

አንድ ቀን ራቅ ወዳለ ጫካ ሄደን ገና ቅጠል አንጥፈን ስንቀመጥ ጎረምሶች ከበቡን። በጥፊና በካልቾ ነብሴን እስክስት ከቀጠቀጡኝ በኋላ «ሁለተኛ እንኳን በእውንሀ፣ በሕልምህም አንዳታያት!» ብለው አስጠነቀቁኝ። እሷንም «ከዚህ መጤ ጋር እንዴት ትሄጃለሽ?› እያሉ በጥፊ አያጣደፉ ይዘዋት ሄዱ። በኋላ ስሰማ ጎረምሶቹ የከተማው ተወላጅ ዘመዶቿ ናቸው።

አንደዛም ሆኖ የዘመዶቿ ንዴት እና ዱላ የነበረንን ፍቅር ሊያደበዝዘው አልቻለም። ግንኙነታችንን የበለጠ በድብቅ ለማድረግ ሰንል ጨለማን ተገን አድርገን ለመገናኘት ተሰማማን። በወቅቱ የረመዳን ጾም ገብቶ ሰለነበር፣ ቤተሰቦቿ ለተራዊህ (የረመዷን ወር የምሽት ሰግደት) ሶላት ሲወጡ እሷ እና ታናሽ ወንድሟ ብቻ ቤት ይቀራሉ።ወንድሟ እንዳይናገር የሸንኮራ እና የከረሜላ መግዣ ሳንቲም ሰጥተነው፣ ከቤታቸው ዝቅ ብሎ ባለ ሸለቆ ቢጤ አቋራጭ የእግር መንገድ እጅ ለእጅ ተያይዘን እንሄዳለን። ይህ ዘዴ ሁለት ችግር አሰከተለ። አንደኛው፡ መጀመሪያ ስሙኒ ስንሰጠው የነበረው ታናሽ ወንድሟ ሽልንግ፣ ትንሽ ቆይቶ ደግሞ ሒሳቡን ወደ ድፍን ብር ከፍ አደረገው። ሰሙኒዋን አንኳን ቤተሰብ ለስኳር እና ለዘይት መግዣ ከሚሰጠን ቀሽበን እንጂ

ሌላ የገቢ ምንጭ ስላልነበረን ተቸገርን። አለፍ አለፍ እያልን ሳንቲም ስናገኝ መገናኘታችንን ብንቀጥልም ከልጁ የባሰ ሌላ ችግር ገጠመን።

አንድ ምሽት እንደተለመደው ደንገዝገዝ ካለው ጫካ ውስጥ ተቃቅፈን ስናቋርጥ፣ ድንገት አንድ ጅብ ከፊት ለፊታችን እየሮጠ መጥቶ በሁለታችን መሀል ሰንጥቆ አለፈ። በድንጋጤ ብትንትናችን ወጥቶ በተቃራኒ አቅጣጫ ስንሮጥ ሳንገናኝ ቤታችን ገባን። ከጅብ መሸሼ «ወንድንቴ» የከዳኝ ሰለመሰለኝ፣ ለአንድ ሳምንት ያህል ዓይኗን ማየት አፈርኩ። እንደ ድሮው ማታ መገናኘት ይቅርና፣ ትምህርት ቤት መንገድ ላይ ከተገናኘን እንኳን ፊቴን አዙሬ እሸሻት ጀመር። አንድ ቀን ከኋላ ተደብቃ ይዛኝ ነገሩን ቀለል አደረገችውና ግንኙነታችንን ቀጠልን።

ረመዷን ከተጠናቀቀ በኋላም በሌላ ዘዴ ጨለማን ተገን አድርገን መገናኘቱን ገፋንበት። ማታ ማታ በሳምንት ሦስቴ ከቤታቸው ወደ አምስት መቶ ሜትር ርቀት ላይ ከሚገኝ ሱቅ ለቤተሰብ ወተት ታመጣ ስለነበር፣ ሁለት ሰዓት ሲሆን ከቤት እንድትወጣ ተነጋገርን። ቀድሜ ወጥቼ መንገድ ዳር ጨለማ ውስጥ ተሸሽጌ አጠብቃታለሁ።

በሩን ከፍታ ስትወጣ ስለሚታየኝ፡ከጨለማው ወጥቼ እየተሳሳምን እሰከ ሱቁ ድረስ እንሄዳለን። ባለሱቆቹ እንዳያዩን ወደ ኋላ ቀርቼ ወተቱን ይዛ ስትመለስ ቤታቸው ድረስ አሸኛታለሁ። በዚህ ሁኔታ የልጅነት ፍቅራችንን ስናጣጥም ቆይተን በአንድ የተረገመ ቀን ውርደት ተከናነብኩኝ።

ሁሌ እሷን በማገኛት ምሽት እንደማደርገው ጨለማ ውስጥ ቆሜ በራቸው ላይ ዓይኔን ተክዬ በመጠባበቅ ላይ አያለሁ፣ በሩ ተከፍቶ ወደእኔ ሰትመጣ እንደሁል ጊዜው አቅፌ ልሰማት ወደ መንገዱ ወጥቼ ሰጠመጠምባት ጨኸትዋን ለቀቀችውና ገፍትራ ሳማ ውሰጥ ጣለችኝ። አየጠበኳት የነበረችው ልጅ አንዳልሆነች ስረዳ፣ ያንን ትንሽ ሲጠጉት ቀዳ የሚለበልበውን የአሰላ ሳማ አያቋረጥኩ ወደ ቤት ሸመጠጥኩ። ቤት ገብቼ ሲጠይቁን «ዱርዬዎች ገንዘብ ያለኝ መስሏቸው ሊወጉኝ ሲሉ በሳማ ውስጥ አቋርጬ አመለጥኳቸው» ብዬ ዋሽሁ።

እህቴም አፈር እና የተለያየ መድኃኒት በመቀባት በሳማ ተለብልቦ ያበጠውን ሰውነቴን ልታክምልኝ ሞከረች። ለካ እኔ ለመሳም የተጠመጠምኩባት ፍቅረኛዬ ሳትሆን እናቷ ነበረች። እናትየው የዛን ዕለት ከሰፈር ሌላ እቃ ለማንሳት ሰለፈለገች እግረ መንገዷን ወተቱን ለማምጣት ልጅቷን አሰቀረቻት። እንደዛሬው ሞባይል ስልክ ስላልነበረ ልጅቷ ድንገት የተከሰተውን የእቅድ ለውጥ ልታሳውቀኝ የምትችልበት መንገድ አልነበራትም። ደግነቱ እናቷ ዱርዬ የተተናኮላት እንጂ፣ የልጇ ፍቅረኛ መሆኑን አልገመተችም። እኛም ጉዳዩን ለማንም ስላልተናገርን በዛው ተዳፍኖ ቀረ።

# 3.3. የመጀመሪያው እስር

አሰላ እንደገባሁ ጁሙጋ ላይ ትምህርቴን እንዳቋርጥ ያደረገኝ ጣጣ እንዳይከተለኝ በተቻለኝ መጠን ከፖለቲካ ርቄ ቆየሁ። የጭላሎ ት/ቤት ተማሪዎች አብዛኞቹ ከተሜ ሰለሆኑ፣ የፖለቲካ ንቃታቸውም ሆነ ፍላጎታቸው ያን ያህል ጠንካራ ስላይደለ ወደ ፖለቲካ እንቅሰቃሴ የመሳብ ዕድል አልነበረኝም። በተማሪዎች እና በአስተማሪዎች የፓለቲካ ንቃት የሚታወቀው ጭላሎ ሳይሆን አዳማ መውጫ ላይ የሚገኘው አሰላ አጠቃላይ ት/ቤት (Assella Comprehensive) ነበር። ነገር ግን የባሌ ደን ሲቃጠል የዩኒቨርሲቲ ተማሪዎች የጀመሩት ተቃውሞ ተስፋፍቶ እኛ ጋር በመድረሱ ምክንያት ራሴን ከፖለቲካ በማራቅ ትምህርቴ ላይ የማተኮሩ ትልሜ ሊቀጥል አልቻለም።

የዩኒቨርሲቲ ተማሪዎች በመምህራኖች በኩል እያገኙን ለተቃውሞ ይቀሰቅሱን ጀመር። በዚህ ሰበብ የተወሰንን ተማሪዎች ወደ አዲስ አበባ በመሄድ ምኒሊክ ት/ቤት በተደረገው የሚጫና ቱለማ ድርጅት ስብሰባ ላይ ተሳትፈን በባሌ ደን ጉዳይ ገለፃ ተደረገልን። ከአዲስ አበባ ወደ አሰላ እንደተመለስንም የጭላሉ እና የአሰላ አጠቃላይ ተማሪዎች ጋር ተመካክረን በጋራ ሰላማዊ ሰልፍ ለመውጣት ወሰንን። የትዕይንተ ሕዝብ እቅዳችን የአሰላ አጠቃላይ ተማሪዎች በታች በኩል፣ ጭላሎዎች ደግሞ በላይ በኩል ዋናውን መንገድ ይዘን መሀል ከተማ ላይ ተገናኝተን ወደ ዞን አሥተዳደር ቢሮ መሄድ ነበር። በዕለቱ ግን ፓሊሶች በብዛት ተሰማርተው ሰለነበር፣ በእቅዱ መሠረት መሀከል ላይ ከመገናኘታችን በፊት በተኑን። አብዛኛዎቹ ተማሪዎች የጥይት ድምፅ ሰምተው ስለማያውቁ ፖሊሶቹ ገና ወደ ሰማይ መተኮስ ሲጀምሩ በድንጋጤ ሸሽተው በደቂቃዎች ውስጥ ተበተኑ። ለብቻችን የቀረነውን ጥቂት ልጆች ፓሊስ ለቃቅሞ ወሰደን።

ሌሎቹን ተማሪዎች ወደ ፓሊሰ ጣቢያ ሲወሰዷቸው እኔን ለብቻ ነጥለው የእህል መጋዘን ውስጥ አሠሩኝ። መጋዘኑ በጣም ሰፊና ምንም ብርሃን የሌለው ጨለማ ስለነበር ከልክ በላይ ያስዕፈራል። ትንሽ ስንቀሳቀሰ የሚፈጠረው ኮሽታ እንደ ገደል ማሚቶ መልሶ ያስተጋባል። በራሴው እንቅስቃሴ መልሼ ራሴን ከምረብሽ በማለት ጸጥ ብዬ ቁጭ አልኩ። ብዙም ሳይቆይ ቁጭ ባልኩበት እንቅልፍ ጣለኝ፡ ከእንቅልፌ ሥነቃ ርሀብ አንገበገበኝ። ምግብ ሊያመጡልኝ ይችላሉ ብዬ «ጥበቃ ... ጥበቃ .. ጥበቃ» እያልኩ ብጣራም መልስ አጣሁ። በኋላ ተሰፋ በመቁረጥ በእጄ መሬቱን ስነካ፣ የፈሰሰ እህል አገኘሁና ዘግኜ እየቆረጠምኩ ርሀቤን አስታገስኩ። ይህች እስር በፖለቲካ ተሳትፎዬ ውስጥ የመጀመሪያዋ ሆና ተመዘገበችልኝ።

የያዙኝ ሰዎች ባደረጉት ምርመራ በፓለቲካ ሰበብ በፊት ከነበርኩበት ት/ቤት መባረሬን ደረሱበት። በአጋጣሚ ጉዳዩን የያዘው መርማሪ ሩህሩህ ስለነበር ነገሩን ራሱ ጋር በማስቀረት «ለአሁኑ ማንም አላወቀህም። ውሎ አድሮ ግን መሰማቱ ስለማይቀር የምትችል ከሆነ አሰላን ለቀህ ብትሄድ ይመረጣል» በማለት ጠርቶ መከረኝ። ያኔ የዞኑ አቃቤ ሕግ ከነበረውና የሙሐመድ ጅማ ወንድም ከሆነው ሐሰን ጅማ ቤት ተቀምጬ እማር ነበር። እንደ አጋጣሚ ሆኖ በዛው ሰሞን ሐሰን ጅማ ወደ ምዕራብ ሐረርጌ ጭሮ ሲቀየር፡ ቤተሰቦቹ እንዲቀርቡት አዳማ ሊያዛውራቸው ወሰነ። እኔም እየመጣብኝ ካለው ችግር ማምለጫ ስላገኘሁ ቤተሰቡን ተከትዬ ወደ ሰምጥ ሸለቆዋ መናገሻ አዳማ ሰተት ብዬ ገባሁ።

# 3.4. አዳማ፤ የከተማ አክቲቪስት

አዳማ ከገባን በኋላ ት/ቤት እስኪከፈት ድረሰ የሐሰን ጅማን አዲሰ ቤት ማሰገንባት ላይ አተኮርኩ። ቤቱ የሚሠራበት ቦታ አሁን ቦሌ ተብሎ የሚጠራው ሰፈር ነው። በወቅቱ ቦሌ የእርሻ መሬት በመሆኑ፣ ለቤት መሥሪያነት ገና መከፋፈሉ ነበር። እኛም አዲስ በታጨደ የጤፍ ማሳ ላይ ቤት መሥራት ጀመርን። ቦሌ የሚለውን ስም መሰየም በራሱ ከባድ ትግል ነበር። መሬቱ ለቤት ግንባታ እንደተከፋፈለ በሌላ ስም መጥራት ተጀመረ። እኛ ግን የኦሮሞ ስም ልንሰይምለት ፈለግን። መሆን ባለበት ስም ላይ ስንወያይ ቤት እንዲሰሩ መሬት የተሰጣቸው አብዛኞቹ የመንግሥት ባለሥልጣናት እና በሀብት ሻል ያሉ ነጋዴዎች እንደሆኑ ተረዳን። የሚሰየመው ስም እንዲጸና ከተፈለገ ማራኪ እና ደስ እያለቸው የሚጠሩበት መሆን እንዳለበት ተግባባን።

ፊንፊኔ (አዲስ አበባ) ውሰጥ ሀብታሞች የሚኖሩበት ሰፈር ቦሌ ስለሆነ ለአዳማውም ተመሳሳይ ስም መስጠት ቤት ከሚሠሩ ሰዎች ድጋፍ ያስገኛል በሚል ተመረጠ። ስሙ እንዲጸና ጋሪ ነጂዎችን ማሳመን ጀመርን። በወቅቱ ወደሰፈሩ የሚወሰድ መንገድ አልነበረም። ድንጋይና ሲሚንቶ ከሚያቀርቡ የጭነት መኪኖች በስተቀር የትራንስፖርት አገልግሎት የሚሰጠው በፈረስ ጋሪ ብቻ ነበር። ስለዚህ ቤት መሥራት የጀመሩ ጥቂት ሰዎች ለጋሪ ነጂዎች ጉርሻ (tip) በመስጠት አካባቢውን «ቦሌ›› ብለው እንዲጠሩ አሳመኗቸው። ባለጋሪዎቹ «ቦሌ»ን በማላመድ «ቦሊ..ቦሌ›› እያሉ ተሳፋሪዎችን መጥራት የሰርክ ሥራቸው ሆነ። መንገዱ ተሠርቶ ታክሲ መሄድ ሲጀምር «ቦሌ›› የሚለው ስያሜ በዛው ጸና።

ከዚህ ተሞክሮ በመነሳት አዳማ በቆየሁባቸው ሁለት ዓመታት የከተማዋን ሰፈሮች ወደ ቀድሞ የአፋን ኦሮሞ ስሞች ለመቀየር ሰፊ ዘመቻ አደረግን። ነገር ግን የኦሐዴድ የዞንና የከተማ አመራሮች «ከጠባብነት የመነጨ እሳቤ›› እያሉ በማስፈራራት አጣጣሉብን። ይህን ሐሳብ ይሄ የዞን የድርጅት ጽ/ቤት ስሄድ፣ አንዱ ባለሥልጣን በጥፊ ብሎ አባረረኝ። ከዓመታት በኋላ ከአሜሪካ ስመለስ ሌላ የከተማዋ ባለሥልጣን ወደ አፋን ኦሮሞ የተቀየሩትን ስሞች አዟዙሮ አስጎበኘኝ። እግረ መንገዱን የኦሕዴድ ብሔርተኝነት ውጤት እንደሆነ ሊያሳምነኝ ሞከረ። እኔም በሆዴ «አይ ጊዜ» ብዬ አለፍኩት።

መስከረም ሲጠባ ጎሮ ሁለተኛ ደረጃ ት/ቤት አሥረኛ ክፍል ተመዘገብኩ።ትምህርት ቤቱ ከተማ ዳር እንደመሆኑ፣ አብዛኞቹ ተማሪዎች የገጠር ልጆች ነበሩ። የት/ቤቱ ክፍሎች ከመጥበባቸው የተነሳ ያሠሩት ባለሥልጣናት «ገንዘቡን ኪሳቸው ከተው ግድግዳውን አቀጨጩት›› እየተባሉ በመምህራን እና በተማሪዎች ዘንድ ይታማሉ። ትምህርት እንደተጀመረ ከመምህራንና ተማሪዎች ጋር ለመግባባት ጊዜ አልወሰደብኝም። አስተማሪዎቹ አሰላ ያመጣሁትን ከፍተኛ ውጤት ሲመለከቱ በጥሩ ሰሜት ተቀበሉኝ። የተማሪዎችን ቅሪታም ሆነ የሥነ-ምግባር ግድፈት በማስተካከል ረገድ በሐሳብ እየተረዳዳን ቀጠልን። ሁኔታው ዳይሬክተሩን ጨምሮ ከመምህራን ጋር በአጭር ጊዜ እንድቀራረብ ዕድል ፈጠረልኝ።

ጎሮ ት/ቤት የተማሪዎች ፖለቲካዊ እንቅሰቃሴ ብዙም አልነበረም። እኔም በአብዛኛው

ትምህርት ላይ አተኩሬ ፖለቲካን ከትምህርት ቤት ውጪ ማራመድ መረጥኩ። የነበረው ብቸኛ ውዝግብ በቋንቋ ትምህርት ላይ ነበር። በአፋን ኦሮሞ ክፍለ ጊዜ ኦሮሞ ያልሆኑ ተማሪዎች አስተማሪው ሳይገባ ክፍሉን ለቀው ይወጣሉ። በተመሳሳይ ሁኔታ በአማርኛ ክፍለ ጊዜ ኦሮሞ ተማሪዎች አድማ ያደርጋሉ። አስተማሪዎች የተማሪዎቹን ድርጊት በዛቻ እና ቅጣት ማሰቆም ስላልቻሉ ለመተው ተገደዱ። በሁለቱም ቋንቋዎች ክፍለ ጊዜ ተቀምጠን የምንማረው እኔና ጥቂት ልጆች ብቻ ነበርን። ከልጅነቴ ጀምሬ ቋንቋና ሒሳብ በጣም እወዳለሁ። ስለሆነም የአፋን ኦሮሞ፣ የእንግሊዝኛ እና የአማርኛ ክኅሎቴን ለማሳደግ ከፍተኛ ፍላጎት ነበረኝ። በተጨማሪም ቄስ ትምሀርት ቤት ስገባ የአማርኛ ፊደል ስለተማርኩ ገና በማለዳው ብዙ መጽሐፍት ለማንበብ ታድያለሁ። በአማርኛ ትምህርት ጎበዝ የምባል ተማሪም ነበርኩ።

አብዛኞቹ ተማሪዎች ከክፍል ለቀው ሲወጡ የነበሩት በብሔር ፉክክር ብቻ አልነበረም። የቋንቋ ችሎታቸው ደካማ በመሆኑም ጭምር እንጂ። ብዙ ተማሪዎች ከታች ጀምሮ አሥረኛ ክፍል እስኪደርሱ ድረሰ ከሁለቱ ቋንቋዎች አንዱን ብቻ እየተናገሩ ወይም እየተማሩ ነው የመጡት። ጎሮ ት/ቤት የሚማሩ የኦሮሞ ልጆች በአብዛኛው ከገጠር ስለመጡ፡ አማርኛ እያወሩ አላደጉም። ከታችኛው ክፍል ጀምሮ የተማሩት በአፋን ኦሮሞ ነው። አማርኛ ከአምስተኛ ክፍል ጀምሮ ሲሰጥ ቢቆይም፣፡ የነበረው የመማር ማስተማር ሁኔታ የልጆቹን ችሎታ የሚያጠናክር አልነበረም።

አፋን ኦሮሞ ላይ አድማ በሚያደርጉ ተማሪዎችም ተመሳሳይ ችግር ነበረባቸው። አሥረኛ ክፍል እስኪደርሱ ድረስ በአስተዳደግም ሆነ በትምህርት ቤት የአፋን ኦሮሞ ክኅሎታቸውን ማሳድግ የሚያስችል ሁኔታ አልነበረም። ኦሮሚያ ውስጥ ትምሀርት በአፋን ኦሮሞ መስጠት ሲጀመር፣ የአማራ ብሔር ተማሪዎች እና ቤተሰቦቻቸው ተቃውሞ ስላሰሙ በቋንቋቸው እንዲማሩ ተፈቀደላቸው። «ከአ፣ ባ፣ ጫ፣ ዳ፣11 ይሻለል ጤፍ አጨዳ›› በሚል መፈክር በተካሄደ ተቃውሞ፣ መንግሥት የአማራ ማኅበረሰብ በሚበዛባቸው ት/ቤቶች ተማሪዎች በአማርኛ እንዲማሩ ፈቀደ። ከተሞች አካባቢ አብዛኞቹ የመንግሥት እና የግል ት/ቤቶች ሙሉ በሙሉ ሊባል በሚቻል ደረጃ በአማርኛ ማስተማሩን መረጡ።

በዚህ የተነሳ የአማራ ብሔር ተወላጅ ተማሪዎች ብቻ ሳይሆኑ፣ ኦሮሞዎችን ጨምሮ ብዙ የከተማ ልጆች ከታች ጀምሮ ሲማሩ ያደጉት በአማርኛ ብቻ ነው። እንዲህ ባለ ሁኔታ በቋንቋ ተለያይተው የተማሩ ልጆች ናቸው እንግዲሀ አንደኛ ደረጃን አጠናቀው ዘጠነኛ ክፍል ላይ እንዲቀላቀሉ የተደረጉት። ከቋንቋ ትምህርት በሰተቀር ሁሉም ትምህርት የሚሰጠው በእንግሊዝኛ ነበር። አፋን ኦሮሞ እና አማርኛ እንደ አንድ ትምህርት እንዲወሰዱ ሲወሰን በችሎታ ማነስና በፉክክር ስሜት 'መፎረፍ' ፋሽን ሆነ። ሁለቱም ቡድኖች ተቃራኒ ቋንቋ ላይ አድማ እያደረጉ ቆይተው የአሥረኛ ክፍል ብሔራዊ ፈተና ውጤት ሲመጣ አብዛኞቹ ተማሪዎች ኤፍ (F) ቢያመጡም ቅር ያለው ሰው ግን አላየሁም። እኔ ሁለቱንም ቋንቋ A አመጣሁ።

በሌላ በኩል የአሥረኛ ክፍል ብሔራዊ ፈተና አብረን ካጠናናቸው ተማሪዎች ውስጥ አንድ ልጅ ብቻ ሲወድቅ፣ የተቀረነው ሁላችንም አለፍን። በልጁ መውደቅ እያዘንን ሳለ፡ አንድ ቀልደኛ ልጅ «እከሌ ለምን እንደወደቀ ገብቷችኋል?›› ብሎ ጠየቀን። እኛም ግራ ገብቶን ምን ምሥጢር ሊያወጣ እንደሆነ እያሰብን በጉጉት ማዳመጥ ጀመርን። ልጁም «ያኔ ፈተና ልንጀምር ስንል

11 የቁቤ አልፋቤት

ስንጸልይ ትዝ ይላችኋል? ሁላችንም ሁለት አጃችንን ወደላይ ዘርግተን አሜን ስንል እሱ ግን አንድ እጁን ብቻ ነበር የዘረጋው። ረጅም ስለሆነ አንድ አጇ ይበቃል ብሎ እሰቦ ነው። በጸሎት ጊዜ ሁለት እጅ የሚዘረጋው ፈጣሪ ችሎታውን በእያንዳንዱ እጅ ላይ ግማሽ ግማሽ ስለሚያስቀምጥ ነው።

እናም ልጁ አንድ እጅ ብቻ ስለዘረጋ፣ አንዱን ግማሽ ብቻ አግኝቶ ሌላው ግማሽ መሬት ላይ ወደቀበት።

እኛ ያለፍነው በሁለት እጃችን ያገኘነው ተደምሮ ነው። እሱ ግን በአንድ እጁ ያገኘው ከ50% በታች ስለሆነ ወደቀ›› ብሎ ሀዘናችንን በሣቅ ቀየረው።

አዳማ መግባቴ ትምሀርቴን አጥብቄ ከመያዝ ባሻገር ፖለቲካውም ላይ በተነቃቃ ስሜት መሳተፍ እንድጀምር አስቻለኝ። አዳማ ከአሰላ በተሻለ ብዙ ኦሮሞዎች ከተለያየ ዞን መጥተው የሚኖሩባት ከተማ ናት። በትምህርትም ሆነ በማኅበራዊ ሕይወት ከአዳዲስ ሰዎች ጋር ለመተዋውቅና በኦሮሞ ጉዳይ ላይ ለማውራት ዕድል አገኘሁ። ከእኛ ጋር የሚማሩ ብዙ ተማሪዎች፣ ከተለያዩ ዞኖች መጥተው የመንግሥት ሠራተኛ ከሆኑ ዘመዶቻቸው ዘንድ በመጠጋት ይማሩ ነበር። ዘመዶቻቸውም የተማሩ እና ብሔርተኛ ስለነበሩ ተማሪዎቹም ጥሩ ንቃት ነበራቸው። በህሀ የተነሳ ፖለቲካዊ ጉዳዮችን ለማውራት ያመቻል።

በተጨማሪም የአካባቢዬ ተወላጅ የሆኑ የኦነግ ወታደሮች ለረጅም ዓመታት በአሰላ፣ በባቱ እና በፊንፊኔ ታስረው ሲፈቱ ወደ ቀዬኣቸው መመለስ ስለማይችሉ አዳማ ይማሩ ነበር። ዕድሜያቸው ቢገፋም ሰባተኛ፣ ስምንተኛ እና ዘጠነኛ ክፍል ገብተው መማር ጀመሩ። የኦሮሞን ታሪክ፡የትግል ዓለማ እና ግብ በየፈርጁ ያፅተማሩኝ እነሱ ናቸው። ከእነሱ አንዱ ዱጎምሳ ዋጂ ይባለል፡ ውልደቱ ጎሎልቻ ሲሆን፣ አዳማ ሳንገናኝ በፊት አውቀዋለሁ።

ስድሰተኛ ክፍል በምማርበት ጊዜ ለተማሪዎች ጥያቄ እና መልስ ውድድር የወረዳችን ዋና ከተማ ወደሆነችው ጫንጮ ሄድን። በወቅቱ ዱጎምሳ ከሌሎቻችን በዕድሜ ብዙ የሚበልጠን ሲሆን የመጣውም ሌላ ት/ቤት ወክሎ ነው። የውድድሩ አሸናፊም ሆነ። ከውድድሩ በኋላ ስንሰማ ዱጎምሳ ጎልማሳ ሆኖ ከእኛ እኩል ስድስተኛ ክፍል ለመማር የተገደደው፣ በልጅነቱ ትምህርቱን አቋርጦ የኦሮሞ ነጻነት ሠራዊትን ተቀላቅሎ በመታሰሩና ሲፈታ ካቆመበት በመቀጠሉ እንደሆነ አንድ አስተማሪ አስረዳን። እስር እና ጦርነት ውሰጥ ባይቆይ ኖሮ የዛኔ ዩኒቨርሲቲ ሊገባ ይችል እንደነበረ ጨምሮ ነገረን።

ውድድሩ አልቆ ስንለያይ ዱጎምሳ መታሰሩን ሰማን። የእሰሩ መነሻ በቃለ-ምልልሱ ባሳየው ችሎታ ከተማሪዎች እና ከሕዝቡ አድናቆትን ሰላገኘ አሁንም ሕዝቡን ያነሳሳብናል በሚል ጥርጣሬ ነበር። ከሦስት ዓመት በኋላ በመታሰሩ ምክንያት ወዳቋረጠው ስድሰተኛ ክፍል ተመልሶ ሲማር ዕጣ ፈንታ አዳማ ላይ አገናኘችን። እንደ ዱጎመሳ ሁሉ ጎሎልቻ የተወለደውና የኦነግ ወታደር የሆነው ፊጣ ባይሳ (የትውልድ ስሙ ናሲር አብይ) ከእሰር ተፈቶ ቆየኝ። ሁለቱ ኦብሴ እና ፈይሳ ከሚባሉ ሌሎች የኦነግ አባላት ጋር በኅቡዕ አደራጁን። የኦነግን ድርጅታዊ ዓለማ እና ግብ ካሰተማሩን በኋላ፣ አዳማን ጨምሮ አጎራባች በሆኑ የምሥራቅ ሸዋ፣ የአርሲ እና የምዕራብ ሐረርጌ ወረዳዎች ተማሪዎችን በድብቅ እንድናደራጅ ተልዕኮ ሰጡን።

አዳማ ከምሠራቸው የትግል ሥራዎች እንዱ፡ ሕዝቡ በኢሬቻ በዓል ላይ እንዲታደም

ማነሳሳት ነበር። አሰላ ዘጠነኛ ክፍል ስማር ኢሬቻ ሄጄ ስለነበር፣ አዳማ ሰገባ ከመሰተፍ ወደ ማስተባበር ተሸጋገርኩ። ለበዓሉ አንድ ወር ሲቀረው ከሌሎች ተማሪዎች ጋር ተመዳድበን፡ ሕዝቡ ከአዳማና አጎራባች ወረዳዎች ወደ ኢሬቻ እንዲሄድ ወደ መቀስቀሱ አንሰማራለን። ከነጋዴዎችና ከመንግሥት ሠራተኞች ገንዘብ በማሰባሰብ የጋራ ትራንስፓርት እንከራያለን። በአዳማ አንደ ድንቁ ደያሰ ያሉ ሀብታሞች በግልጽ ይረዱናል። ሌሎቹ ደግሞ በድብቅ ልገሳ በማድረግ ሰዎች በገንዘብ እጦት ከኢሬቻ እንዳይቀሩ ያደርጋሉ።

በተገኘው አጋጣሚ ኢሬቻ ላይ የሚሳተፈውን ሕዝብ ቁጥር ለማብዛት እንዘጋጃለን። በተቃራኒው የመንግሥት ሰዎች አቅዳችንን አክሽፈው የተሳታፊውን ቁጥር ለማሳነስ ይሠራሉ። የመንግሥት ሰዎች ለበዓሉ አንድ ሳምንት ሲቀረው ጠንካራ አስተባባሪዎች ብለው የሚጠረጥሯቸውን በማሰር ይጀመራሉ። ይህን ሰለምናውቅ አስተባባሪዎች ከእይታ በመሰወር ጥንቃቄ እናደርጋለን። ቀጥሉ በየዞኖቹ የሚገኙ የመጓጓዣ አገልግሎቶች የኢሬቻ ተጓዦችን እንዳይጭኑ ጫና ያደርጋሉ። በማሰከተል «ኢሬቻ መሄድ የሚችሉት በባሕል እና ቱሪዝም ቢሮ የተመዘገቡ ሰዎች ብቻ ናቸው› የሚል ሰልት አመጡ።

የመንግሥትን ሰልት ለማክሸፍ ሰዎች እገዳው ሳይጀመር በፊት ከየዞኖቹ በመምጣት ፊንፊኔ እና አዳማ ቆይተው፡ ለዋዜማው ቢሾፍቱ ይሄናሉ፡ መንግሥትም ይህን በመረዳት ፍተሻ በሚል ሰበብ ከዋዜማው ጀምሮ ወደቢሾፍቱበሚያሰገቡ ዋናመንገዶች ላይ ፖሊስ በማሰማራት ሕዝቡን ያንገላታል። የሚፈትሹት ታዳሚው ላይ ጉዳት የሚያደርሰ የጦር መሣሪያ አልነበረም። ከዚያ ይልቅ የኦነግ ባንዲራ፣ የጥለቱ ቀለም ወደ ባንዲራው የሚጠጋ ነጠላ፣ ጋቢ እና ቀሚስ የለበሱ ሰዎችን ነበር ዒላማ የሚያደርጉት። ድንገት ቀይ እና አረንጓዴ ቀለም ያለው ልብስ የለበሰ ሰው ካዩ ይደበድባሉ፡ ሴቶችን ሙሉ ልብሳቸውን በማስወለቅ ጭምር ያዋርዳሉ።

በአንድ የኢሬቻ ክብረ በዓል ወቅት ከአዳማ ወጥተን ሞጆ እንኳን ሳንደርሰ፣ ፖሊስ መንገዱን በመዝጋት ከሃምሳ በላይ የትራንሰፖርት መኪኖችን በማስቆም ማለፍ ክልክል እንደሆነ አሳወቀ። ይህንን ያደረጉት ሰዉ ተሰፋ ቆርጦ ወደኋላ ይመለሳለል በሚል ነበር። ሕዝቡ ግን ከመኪናው ወርዶ በእግሩ ጉዞውን ቀጠለ። መንገድ መዝጋት ሳይበቃቸው የእግር ጉዞውንም ከለከሉ። ሕዝቡ ግን እጅ አልሰጠም፣ በአካባቢው ተወላጆች እየተመራ የመኪና መንገዱን ትቶ በገበሬ ማሳ ውስጥ በማቋረጥ ጉዞውን ገፋበት።

ብዙ ቦታ የመንደር ሚሊሻዎች ለመከልከል ቢሞክሩም፣ ሕዝቡ በቁጥር በልጦ በመገኘቱ ቢሾፍቱ ገባን። ቢሾፍቱ ሐይቁ ላይ የኢሬቻ ሥርዓት ከተፈጸመ በኋላ ወጣቱ በመፈክር እና በጭፈራ የወያኔን ሥርዓት ሲቃወም ዋለ። የሕዝቡን ብዛት ተገን በማድረግ፣ የትግለ ሕዋሶች በድብቅ በመገናኘት መከሩ። በኢሬቻ ላይ የሚታየው ባሕላዊ አለባበሰ፡ ዘፈን፣ ግጥም፣ የሕዝቡ አንድነትና ፍቅር አንዳች የጋለ የትግል ሰሜት ውስጥ የመክተት ኃይል ነበረው።

## 3.5.ከአባዱላ ጋር በአንድ አዳራሽ

ከኢሬቻ መልስ ትምሀርት ቤት እና ውጪ ላይ ተማሪዎችን በተለያየ መንገድ ማንቀሳቀስ እና ማደራጀቱን ቀጠልንበት። በፊንፊኔ ዳግማዊ ምኒሊክ ት/ቤት በሚደረገው የሜጫ አና ቱለማ ማኅበር ዝግጅት ላይ በየጊዜው እስተፍ ነበር። በገዳ ሥርዓት እና በኦሮሞ ማንነት ዙሪያ ዶ/ር ገመቹ መገርሳ የሚሰጠው ትምህርት የነበረኝን ግንዛቤ በእጅጉ አሰፋልኝ። በመድረኩ ላይ ኡሰማዮ ሙሳ፣ ሱቴ ባሬንቶ፣ ዘሪሁን ወዳጆ፣ ጀዌ ቦራ እና አድናን ሙሐመድ የሚያቀነቅኗቸው የትግል ዜማዎች የተማሪዎቹ ንቃት ከፍ እንዲል ትልቅ ሚና ተጫውተዋል።

ከሜጫ አና ቱለማ ዝግጅቶች ባፈራነው እውቀት እና ድፍረት ተማሪዎችን የበለጠ ማደራደት ቀጠልን። የተማሪዎቹ እንቅስቃሴ ሲበረታ ኦሕዴድ አንድ ሰብሰባ አዘጋጀ። በመላው ምሥራቅ ሸዋ ዞን የሚገኙ የሁለተኛ ደረጃ ት/ቤት ተማሪዎች ሊሰበሰቡ መሆኑ ተሰማ። እኛም አጋጣሚውን ወደ ተቃውሞ ለመቀየር ወስነን፤ የሥራ ድርሻ ተከፋፈልን። ገሚሱ ከተለያዩ ት/ቤቶች ከመጡ ተማሪዎች ውሰጥ ንቁ የሆኑትን በመቅረብ ላሰብነው ተቃውሞ ሚና እንዲኖራቸው ለማሳመን ተላከ። ከፊሉ ደግሞ በስብሰባው ላይ ተቃውሞ እንዲያሰማ እና ጥያቄዎችን እንዲያቀርብ ተመደበ። እኔ ሁለተኛው ምድብ ውሰጥ ተካተትኩ።

ስብሰባው ገና ከመጀመሩ ጮክ ብዬ «አካሄድ!» አልኩ። ይህን ያደረኩት በኦሕዴድ ሰብሰባ ላይ አንድ የስብሰባው ተካፋይ «አካሄድ!» ካለ ያ ሰው ሐሳቡን እሰኪያሰማ ድረሰ መድረኩ በአጀንዳው መቀጠል አይችልም ሲባል ስለሰማሁ ነው። «ጥያቄ!» ብዬ እጅ ባወጣ ኖሮ «የጥያቄ ሰዓት በኋላ ሰለሚሰጥ ታገስ» ልባል እችል ነበር። እናም «አካሄድ« በማለቴ የመድረክ መሪው ንግግሩን አቁሞ ዕድል ሰጠኝ።

«ይሀ ሰብሰባ በመላው ሀገሪቱ እየተካሄደ ነው፤ የሌላ ክልል ተማሪዎች አበል ይከፈላቸዋል። ለእኛ ግን ምሳ እንኳን አልተዘጋጀም። ይህ ኦሮሞ/ኦሮሚያ ላይ ከሚደረግ መድሎ አንዱ ማሳያ ነው» በማለት ተናገርኩ። ቀጥተኛ የፖለቲካ ጥያቄ ትቼ ሰለ አበል ያነሳሁት አብዛኞቹ ተሰብሳቢዎች ከተለያየ ብሔረሰብ የተውጣጡ የከተማ ልጆች ሰለሆኑ፡ ከፖለቲካ ይልቅ በብር ጉዳይ ማነሳሳት ይቻላል ብዬ ሰላሰብኩ ነበር። አንደገመትኩትም ባነሳሁት ሐሳብ አዳራሹ በጭብጨባ ተናጋ። መድረኩን የያዙት ባለሥልጣናት ትንሽ ተማክረው «የአበሉን ጉዳይ የበላይ አካል ጠይቀን እንመለሳለን፣ አሁን ስብሰባውን እንቀጥል» አሉ። እኛ ግን «የአበል ጉዳይ ካልተፈታ በተዓምር ሰብሰባውን አንቀጥልም» አልን።

ከረጅም ውዝግብ በኋላ ምሳ አንደሚያዘጋጁና አበልም መጨረሻ ላይ አንደሚከፍሉ ነገሩን። እውነተኛ ዓላማችን ምሳ እና አበል ሰላልነበረ «አሁኑኑ ይከፈለን!» በማለት ሰበብ ፈጥረን መረበሹን ቀጠለንበት። ሰዎቹ አበል እንከፍላለን ያሉት ውሸታቸውን ሰለነበረ በተጨባጭ እርምጃ ተማሪዎቹን ማሳመን አልቻሉም። የመጀመሪያው ቀን እንዲሁ በውዝግብ ባከነ። በሁለተኛው ቀን ኦሕዴድዎች ከወቅቱ ከፍተኛ ባለሥልጣናት መካከል አባዱላ ገመዳን አመጡት። አባዱላ መከላከያን ለቆ ወደ ኦሕዴድ አመራርነት ገና መምጣቱ ነበር።

አባዱላ ሲመጣ ፖሊሶች አዳራሹን ሞልተው በተማሪዎች መካከለ ቆሙ። የመጀመሪያ ቀን መድረክ መሪው ጥያቂያችንን ትቶ ለማለፍ ሲሞከር በመንጫጫት እናስቆመዋለን። በቀጣዩ ቀን ፖሊስ መሀከላችን ቆሞ ድምፅ የሚያሰማ ሰው ማስወጣት ጀመረ። ከፖሊሰ ውጪ ሲቪል የለበሱ ሰዎችን ተማሪ አስመስለው በአዳራሹ ውስጥ ሰገሰጉ። እኛ እጅ ስናወጣ ተንጠራርተው ለእነሱ ሲሰጡና እነሱም መንግሥትን የሚደግፍ ሐሳብ ሲያቀርቡ ነበር ማንነታቸው የተገለጠልን። ይህ ሁኔታ እንደትላንትናው በጥያቄም ሆነ በመጮኽ ተቃውሞውን ማስቀጠል እንደማንችል ሰላሰገነዘበን፣ ዕረፍት ላይ ተወያይተን በሌላ ሰልት ተመለስን።

ይኸውም እነርሱ ከመድረክ ማውራት ሲጀምሩ፣ እጅ ማውጣት እና ድምፅ ማሰማቱን ትተን እግራችንን ከወንበሩ ሥር መሬት ላይ በማሸት አዋኪ ድምፅ መፍጠር ነበር። አዳራሹ ሰፊና ጣሪያውም ቆርቆሮ ሰለነበረ ድምጹ ያስተጋባል። በሺህ የሚቆጠሩ ተማሪዎች በአንድ ላይ እግራቸውን ከመሬት ጋር እያሻሹ ኮሽታ ሲፈጥሩ፣ ከመድረኩ የሚባለውን መሰማት ቀርቶ በትዕግሥት መቀመጥ በራሱ ይከብዳል። ሁሉም ተማሪ ከወንበሩ ሥር ማንኮሻኮሹን ስለገፋበት ፖሊሶች ለይተው ከአዳራሽ ማሰወጣት አልቻሉም። በዚህም ሰብሰባው ቆሞ ምን እንደምንፈልግ ስንጠየቅ «ጥያቄ የመጠየቅ እና ሐሳብ የመሰጠት ዕድል እናንተ ላሰገባችኋቸው ብቻ ሳይሆን፣ ለሁሉም ተማሪ ያለ አድሎ በነጻነት ይሰጥ!›› አልን።

ጥቂት ተመካክረው «አደገኛ›› (Hard Core) ተብለው የተለዩ ተማሪዎችን ከልክለው ለሌሎች ተማሪዎች ዕድል መሰጠትን እንደ ስልት ተጠቀሙ። ይህን ስንረዳ አሁንም ሌላ ስልት ቀየስን። ሁሉም ተማሪ እጅ ያወጣል፡ ዕድሉ የተሰጠው ተማሪ የሰዎችን ስም ጠርቶ «እከሌ እንዲጠይቅልኝ ዕድሌን አሳልፌለታለሁ›› ብሎ ማይክራፎኑን ያሳልፋል። መድረኩን የሚመራው ባለሥልጣን አሻፈረኝ ቢልም አባዱላ ግን ፈቀደልን። በዚህ መንገድ ዕድሉ ለእኔ እና ጥያቄ እንድንጠይቅ ለተመደብን ልጆች መድረሰ ቻለ።

ኦሕዴድን እንደ ድርጅት፣ አባዱላን እንደግለሰብ የሚወቅሱ ጥያቄዎችን አወረድንባቸው። ሊያስቆሙን ሲሞክሩ በጩኸት እናበእግራችን በመረበሽ ሰብሳቢዎቹን ትዕግሥት አሳጣናቸው። በዚህ መሀል አባዱላ «አሰተዋይ እና ጭንቅላት ያላችሁ የነገ ሀገር ተረካቢ ተማሪዎች እንጂ እንደዚ ዓይነት ዱርዬ አልመሰላችሁንም፤ ሥርዓት ያለው ውይይት እምቢ ካላችሁ ተውት!» በማለት ከመድረክ ወርዶ ሄደ። ምሳ ሰዓት ላይ እኔና የተወሰኑትን 'Hard Core' አባዱላ ዘንድ አቀረቡን። በወቅቱ አባዱላ ብሔሩ ኦሮሞ ሳይሆን የትግራይ ተወላጅ፣ ሰሙም ምናሴ ወ/ጊዮርጊዕ እንደሆነ በስፋት ይወራ ነበር። እኛም ጉዳዩን ስብሰባ ላይ አሉታዊ በሆነ መልኩ አንሰተናል። በምሳ ሰዓት አሰጠርቶን ስንወያይ ስለ ውልደቱ እና አስተዳደጉ አጫወተን።

ከማንነቱ ጋር አያይዘን ያነሳነው ጥያቄ አንዲሁም በሕዝቡ ውስጥ የሚናፈሰው ሀሜት ስሜቱን እንደነካው ተረዳሁ። ሰለራሱ የነገረን ታሪክ እውነት ስለመሆኑ በራሳችን ጥናት እረጋግጥን በግልጽ ለተማሪዎች እንደምናሳውቅ ቃል ገባንለት። በዚሁ መሠረት ስብሰባው እንዳለቀ ሦሰት ሰዎች ወደ ትውልድ ቀዬው ሄደን ቤተሰቡን እና ዘመዶቹን አግኝተን ኦሮሞ መሆኑን አረጋገጥን። ያገኘነውን መረጃ ለኦሮሞ ነጻነት ድምፅ ሬዲዮ እና ለተለያዩ አደረጃጆቶች አሰተላለፍን። ከዚህ ጊዜ በኋላ አባዱላን በትግሬነት መጠርጠሩ እየቀነሰ መጣ። ከእኔ ጋር የዚያን ቀን የጀመረው ትውውቅም እያደገ ሄደ። ምንም እንኳን የተለያየ የፖለቲካ አመለካከት ቢኖረንም መነጋገር ለሁለታችንም ቀለለን። አባዱላ ከፖለቲካ ውጪ ባሉ ማኅበራዊ ጉዳዮች ሲናገር

አሰደማሚ ነው። ኦሮሚያን ከጫፍ እስከ ጫፍ ሰለሚያውቃት ሰለመጣችሁበት ወረዳ ጉዳይ ቦታዎችን እና ሰዎችን በስም እየጠራ ያዋራችኋል። ይህ ሁኔታው ለሰውዬው ፖለቲካ ያላችሁን ጥላቻ ለጊዜውም ቢሆን ረስታችሁ እንድታዳምጡት ይጋብዛል። አሜሪካ ሳለሁ የሰላማዊ ትግል ስልቶችን ለመቀየሰ የአገዛዙን የውሰጥ አሠራር እና አመለካከት ለመረዳት ከፍተኛ ጉጉት ስለነበረኝ ከአባዱላ እና ከሌሎች ባለሥልጣናት ጋር ያዳበርኩት ግንኙነት ጠቅሞኛል።

## 3.6. «የኦነግ አባል እንድትሆኑ ተወስኗል!»

በአዳማው የተማሪዎች ሰብሰባ ላይ ባንሰኳቸው ጥያቄዎች በተማሪዎች እና በባለሥልጣናት ዘንድ ዝናን አተረፍኩ። ከዚህ በኋላ ትኩረቱ በረታብኝ። በመንግሥት በኩል እኔን ወደራሳቸው ለመሰብ አንዱ ሲያሰፈራራኝ፣ ሌላው ደግሞ ሊያባብለኝ ቢሞክርም በአምቢታዬ ጸናሁ። ጫናው በመንግሥት በኩል ብቻ አልነበረም። ስብሰባው ከተደርገ ከጥቂት ጊዜያት በኋላ ኦነግን እንወክላለን ያሉ ሰዎች ወደ ሀያ የምንደርሰ ተማሪዎችን ሰብስበው «አሁን ብሰለታችሁ ሰለጨመረና ተሳትፏችሁም እየጠነከረ ሰለመጣ፣ ቃለ-መሐላ ፈጽማችሁ ከደጋፊነት ወደ አባልነት መሸጋገር አለባችሁን አሉን። አባልነቱን ባልጠላም ግልጽ ያልሆነልን ነገር ስለነበር «አባል ስንሆን አሁን እየሠራን ካለው የበለጠ ሌላ የሚሰጠን ግዳጅ አለ? ለምሳሌ ጦር ግንባር እንሄዳለን?» በማለት ጥያቄ አቀረብኩ።

እነርሱም «አይደለም አሁን የተሰማራችሁበትን ሥራ ትቀጥላላችሁ» ብለው መለሱ። «የአሁኑን ሥራ (ተማሪዎችን ማደራጀት) ለመቀጠል ከደጋፊነት ወደ አባልነት ማደግ ለምን አስፈለገ?» ብዬ በጥያቄ ሳፋጥጣቸው «ድርጅቱ ወስኗል! ቃለ-መሐላ ፈጽማችሁ አባል መሆን አለባችሁ» አሉን።

እኔ ግን «ያቀረባችሁት ገለፃ እና ምክንያት ስላላሳመነኝ አሁን አባል ለመሆን ዝግጁ አይደለሁም» ብዬ ትቻቸው ወጣሁ። ከሁለት ሰው ውጪ ሌሎች ተማሪዎችም አብረውኝ ወጡ። ከአንድ ሳምንት በኋላ፣ አባል ለመሆን ፈቃደኛ ያልሆንነውን «በወያኔ መንግሥት የሚፈለጉ የኦነግ አባላት» ተብለን ስማችን በሚዲያ ላይ ተነበበ። በዚህ ድርጊት እጅግ አዝነን ቅሬታችንን ለምናውቃቸው የድርጅት አባላት አቀረብን።

በዚህ ሁኔታ የፖለቲካ ተሳትፎዬ እያደገ ሰለሄደ፤ በኑሮዬ ላይ ከባድ ተጽዕኖ አሳድሮ የአሥረኛ ክፍልን ፈተና በአስቸጋሪ ሁኔታ ውስጥ ለመውሰድ ተገደድኩ። በፊት ከምኖርበት ቤት ወጥቼ አንድ አስተማሪዬ አነሰተኛ ቤት ተከራየልኝ። ትንሽ እንደሰነበትኩ ያከራየችኝ ባልቴት ጋር መጥተው «ኦነግ ነው!» ሲሏት ወዲያውኑ አባረረችኝ። ከዚያም የሆኑ ኦሮሞዎች ጋር ቤት አግኝቼ ተከራየሁ። እነዚህኞቹ ደግሞ ከሁለት ሰዓት በኋላ መብራት ያጠፋሉ። በመንገድ ዳር መብራት እያጠናሁ ለአሥረኛ ክፍል ፈተና ተሰናዳሁ። የመንገድ መብራት ሥር ስቀመጥ አንዳንዴ የሚያውቁኝ ሰዎች በአጠገቤ ሲያልፉ፣ ለምን ውጪ እንደተቀመጥኩ ይጠይቁኛል። ችክክለኛውን ምክንያት ትቼ «ቤት ውሰጥ ስለሞቀኝ አየር ለማግኘት ነው» እያልኩ አመልሰላቸው ነበር።

በዚሀ መልኩ የአሥረኛ ክፍል ብሔራዊ ፈተና ወሰጄ ከፍተኛ ውጤት በማምጣት እዚያው አዳማ ውሰጥ ሐዋስ፣ በቀድሞ ስሙ ገላውዲዎስ ት/ቤት 11ኛ ክፍል ገባሁ። በሐዋስ ት/ቤት የፖለቲካ እንቅስቃሴዬን አጥብቄ ገፋሁበት። በሚኒ-ሚዲያ ዝግጅቶች፣ በአፋን ኦሮሞ ክበብ እንዲሁም የተማሪዎች አሥተዳደር ውሰጥ ንቁ ተሳትፎ ነበረኝ። በተጨማሪም ወደ አጎራባች ወረዳዎች በመሄድ ገበሬዎች እና ጎልማሶችን ትምህርት በማስተማር እሳተፍ ነበር።

የኦነግ አባል ለመሆን ፈቃደኛ ባልሆንም ከድርጅቱ የሚመጡትን ግዴታዎች መቀበሌን ግን አላቆምኩም። አንዴ ከድርጅቱ የተሰጠኝ ግደታ ለከፍተኛ አደጋ አጋልጦኝ ያውቃል። የሆነ ቀን ከት/ቤት ስመለስ አንድ ሰው መንገድ ላይ ጠብቆኝ የድርጅት ግዴታ እንዳለ ነገረኝ። «መንገዱን የምታውቀው አንተ ስለሆንክ የሆነ ሰው ወደ ሐረርጌ አሳልፍ» አለኝ። ያ ሰው ፎቶው ብዙ ቦታ ተበትኖ እየተፈለገ ስለሆነ በዋናው መንገድ ወደ ሐረርጌ መሄድ እንደማይችልና በአርሲ በኩል እንዲያልፍ መወሰኑን ሲነገረኝ ሳለመነታ እሺ አልኩት። አመሻስሽ ላይ አንዲት ሴት እና ወንድ ይዞ መጣ። በታለቅ ፍርሀት ውሰጥ እንደሚገኙ ሰሜታቸው ይናገራል። የጉዞ እቅዱን ሳወጣ ወደ ፍተሻ ጣቢያ የሚያደርሰንን ማንኛውንም አጋጣሚ በሚያስወገድ መልኩ አዘጋጀሁ። በአውራ ጎዳና ላይ ለረጅም ጊዜ መጓዝ ተጋላጭነትን ሊጨምር እንደሚችልና በትንንሾ ከተሞች በየመሀሉ መኪና እየቀያየሩ መሄድ እንደሚሻል አሳቅውቄያቸው በእቅዱ እንደተግባባን ያመጣቸው ሰውዬ ጥሎን ሄደ።

እንዳቀድነውም ጠዋት ከአዳማ በሚኒባስ ተሳፍረን ከሰደሬ ዝቅ ብላ አዋሽ ወንዝ ዳርቻ ወደምትገኝ ዶኒ የተባለች ትንሽዬ ከተማ ደርስን። በሸንኩርት ምርቷ በምትታወቀው በሌ ከተማ ወርደን መኪና በመቀየር ድሮ የአርባጉጉ አውራጃ ዋና ከተማ ወደነበረችው አቦምሳ ደረስን። ከአቦምሳ ተነስተን በልጅነቴ ወደማውቃት አባጀማ የተባለች ከተማ ስንደርሰ ቢመሽም ፖሊስ የሚበዛባት የወረዳ ከተማ ስለሆነች ማደር አልፈለግንም። ከዚያ በኋላ መኪና ስለማይሄድ በእግራችን ጨለማውን ሰንጥቀን ስንጓዝ ጉና የሚባል ስፍራ ደርሰን አንድ የማውቀው መምሀር ዘንድ ጎራ አልን። መምህሩ ድንገት ስላየን ደነገጠ። ከቤቱ ፊትለፊት ፖሊሰ ጣቢያ መኖሩ ተጋለጭ ቢያደርገንም፣ እኛን ከማሳደር አላገደውም። ድምጻችንን አጥፍተን አድረን በጠዋት ወደ ዲማ (የእናቴ ቤተሰቦች አካባቢ) ገሰገስን።

ጠዋት ስንወጣ ያደረ ቂጣ ተከፍለን ስለበላን፣ መንገድ ላይ ርሀብ ሆዳችንን ያጨኸው ጀመር። ምግብ እንዳንገዛ በመንገዳችን ላይ ከተማ የለም፤ የሰው ቤት ጎራ ብለን እንዳንጠይቅ ራሳችንን ማጋለጥ ሆነብን። ወቅቱ በጋ ቢሆንም ሌላ ጊዜ መንገዱን የሚሞላው የባቄላ እና የአተር እሸት አልነበረም። ሆዳችንን አስረን ጉዟችንን ቀጠልን። ከአክስቴ (የእናቴ እህት) ሰፈር ስንደርስ ርሀቡ ስለጠናብን ጎራ ለማለት ተገደድን። ቤቷ ደርሰን «ቤቶች!» ስንል መልስ የለም። ሰዎቹን አጥር ሥር አስቀምጬ ቀስ ብዬ ወደ በሩ በመጠጋት አጮልቄ ስመለከት ማንም የለም። ደግነቱ የገጠር ቤት ቁልፍ ስለሌለው መዝጊያውን ከፍቼ ገባሁ፣ እነሱንም ጠራኋቸው። ያገኘነውን የጎመን ወጥ፣ የቀዘቀዘ ሽሮ እና እንጀራ እየተሻማን በላን። ነብሳችን መለስ ሰትል ጓዳ ውስጥ ስዟዟር እንሥራ ውስጥ እየረጋ ያለ ወተት አግኝቼ እሱንም አንሰተን ጠጣን። ወጥ ስለጨረስን የተረፈውን እንጀራ በበርበሬ ጠቅልለን ይዘን ሹልክ ብለን ወጣን።

በምግብ የበረታ ሰውነታችንን በፍጥነት አንቀሳቅሰን። ሜዳውን ጨርሰን ወደ ጎሎልቻ ተራራ ጫፍ ስንደርስ የኦነግ አባል የሆነ አንድ ዘመዴ ጋር ጎራ አልን። ሁሉንም ነገር ከገለጽንለት በኋለ እሱ መቻራ እንደሚያደርሳቸውና እኔ ወደ አዳማ መመለስ እንዳለብኝ አሳመነኝ።

ሰዎቹም በሐሳቡ ተስማምተው እዚያው አድረን በማለዳው ይዟቸው በሪቡ በኩል ወደ መቻራ ሄዱ። ለእኔ ፈረስ ጭኖልኝ ከአንድ ታናሽ ወንድሙ ጋር ሸኘኝ። ልጁ አባ ጀማ አድርሶ መኪና አሳፍሮኝ ተመለሰ።

ለለፉት ሁለት ቀናት ከአሁን አሁን ተያዝን ብዬ ስጨነቅ ነበር። ከአባ ጀማ ወደ አቦምሳ በመኪና

መጓዝ ስጀምር ነፍሴ መለስ ስትል ተሰማኝ። አቦምሳ ላይ ምሳ ከበላሁ በኋላ ከቢሮ የሚባል ቀይ ጫት ገዝቼ አሥር ሰዓት ገደማ ወደ አዳማ አውቶቡስ ተሳፈርኩ። መኪናው ውስጥ ከጎኔ ለተቀመጡ ሰዎች ጫቴን አከፋፍዬ ሞቅ ያለ ወሬ ይዘን እየተጓዝን ቦሌ ከተማ ለመድረስ ትንሽ ሲቀረን አንድ ፒካፕ መኪና በፍጥነት አውቶቡሱን ከፊት አቋርጦ አስቆመው።

ረዳቱ ወርዶ ካናገራቸው በኋላ ሁለት ሰዎች ተከታትለው ገቡ። አንዱ ክላሹን ዝቅ አድርጎ በሩ ላይ ሲቆም፣ ሁለተኛው ከፊት ወንበር ጀምሮ ተሳፋሪዎችን አንድ በአንድ እየገረመመ መጥቶ እኔ ያለሁብት ወንበር ጋር ሲደርስ ዓይን ለዓይን ተጋጨን። «ይኸው!» ከማለቱ ሁሉም ዞር ብለው አዩኝ። «ጀዋር ሠዒድ» አለኝ። አቤት ለማለት ትንሽ ሲቀረኝ የጠራው የአባት ስም የኔ እንዳልሆነ ተረድቼ በሆዴ «ፈጣሪ አወጣኝ!» ብዬ ዐይን ዐይኑን ማየት ቀጠልኩ። በአማርኛ «አንተ ጀዋር ሠዒድ አይደለህም?» ሲለኝ «አይደለሁም» አልኩት። መታወቂያ ሲጠይቀኝ አውጥቼ ሰጠሁት። የያዝኩት የቀበሌ መታወቂያ ፎቶዬ ቢኖርበትም ስሙ ግን ሌላ ነበር። በሩ ጋር ወደ ቆመው ይዞት ሄዶ፣ አንዴ እኔን አንዴ ወረቀቱን እያዩ ሲያወሩ ከቆዩ በኋላ ተመልሶ መጥቶ «ተነስ፣ የምትፈለገው አንተ ነህ!» አለኝ።

ከተሳፋሪዎቹ መካከል ሽማግሌዎች «ምን አጠፋ? ወዴት ነው የምትወስዱትን» እያሉ መነሳት ሲጀምሩ አንደኛው ሰውዬ «አሸባሪ ነው!» ብሎ መለሰላቸው። ሽማግሌዎቹም «አይ ተሳስታችሁ ይሆናል እንጂ ይህ ሕፃን ልጅ እንዴት አሸባሪ ይሆናል?» አሏቸው። ሌሎች ተሳፋሪዎችም በመነሳት ሊያስነሳኝ የሚሞክረውን ሰውዬ ከኋላ መንገድ ሲዘጉበት በሩ ላይ የነበረው መሣሪያውን አቀባብሎ መንገድ እንዲከፍቱ አሰጠነቀቃቸው።

ሹፌራቸውም መሣሪያ ይዞ መጥቶ ወደ አውቶቡሱ ገባ። በዚህ ጊዜ በእኔ ሰበብ ሕዝቡን ሊጎዱ እንደሆነ ስለተረዳሁ ቆም እንዳልኩ «‹ተዉ! ምንም አልሆንምን» በማለት ተሳፋሪዎቹን አረጋግቼ ተነስቼ ወጣሁ። ሲወሰዱኝ ከሹፌሩ ጋር ሦስት ነበሩ።

ትንሽ እንደተጓዝን ወደ አዳማ የሚወሰደውን ዋና መንገድ ትተው በሐዋስ የአትክልት እና ፍራፍሬ እርሻ ወደ ውስጥ ገቡ። ከመንገዱ ዘወር ብለው ወደ ማሳው እንደዘለቁ መኪናውን አቆሙና «ይዘኸቸው የሄድካቸውን ሰዎች የት እንዳደረስክ ተናገር!» አሉኝ። «እኔ ማንንም ይዤ አልሄድኩም፣ ቤተሰቦቼን ጠይቄ ነው የምመለሰው» ብዬ ዋሸሁ። ከግራና ከቀኝ በጥፊ እያላጉኝ፣ አንዱ ጆሮዬን እየጠመዘዘኝ፣ አጠገቤ የተቀመጠው ደግሞ አራቱን የእጅ ጣቶቼን ወደኋላ በመግፋት ቢያስጨኸኝም መካዴን ቀጠልኩ።ጋቢና የተቀመጠው ወጣብሎ ወታደራዊ ሬዲዮ በሚመስል ነገር ተነጋግሮ ሲመለስ ድብደባውን አቁመው ጉዞ ጀመርን። ቆይተው ትራስ ጨርቅ የሚመስል ነገር ጭንቅላቴ ላይ አልብሰውኝ ዓይኔን ሸፈኑት። በጣም ፈራሁ፣ ሊገድሉኝ ነው ብዬ ስለጠረጠርኩ «ሽንቴ መጥቷል» አልኳቸው።

አንደኛው «ራስህ ላይ ሽናው!» አለኝ። ስማጸናቸው ተከራክረው አቆሙልኝ። ወደ ብርትኳን ማሳ ልገባ ስል «እዚሁ ቆመህ ሽናው!» አለኝ። መልሼ «አይ የውኃ ሽንት አይደለም» አልኩት። «እሺ እዚያ እንጨት ሥር ተፀዳዳ» ብሎ ተከትሎኝ መጣ። ሐሳቤ በብርትኳን ዛፎች ተከልይ ሮጬ ለማምለጥ ነበር። ሰውዬው አምሰት ሜትር እንኳን በማይሞላ ርቀት ላይ መሣሪያውን ደግኖ ቆመ። የማምለጥ ዕድል እንደሌለኝ አውቄ የተፀዳዳሁ መስዬ ወደ መኪናው ተመለስኩ። የቅድሙን ጨርቅ ጭንትላቴ ላይ መልሰው ዓይኔን ሸፈኑና መሄድ ቀጠልን።

በግምት አንድ ሰዓት ያክል እንደተጓዝን «የእርሻ ምርቶች ፍተሻ ኬላ ነው፡ ፍጥነትህን

ቀንሰህ አቁምለት›» ብሎ አንዱ ለሾፌሩ ነገረው። የሰዎች የእግር ኮቴ ሲቃረብ እሰማለሁ። እኛ ጋር ሲደርሱ «ከየት ነው የመጣችሁት? ወዴት ነው የምትሄዱት? የጫናችሁትስ ምንድነው?» ብለው አከታትለው ጠየቋቸው። «ከቦሌ መጥተን ወደ አዳማ እየሄድን ነው» ብለው መለሱላቸው። «የኋላውን በር ክፈቱ» ሲሏቸው፣ «እኛ ግዳጅ ላይ ያለን ፖሊሶች ነን አንከፍትም፣ ነገር አትፈልጉን መንገዱን ክፈቱልን» አሏቸው። «ፖሊስ ከሆናችሁ የደንብ ልብሳችሁ የታለ? መታወቂያችሁን አውጡ» አሏቸው። «እናንተ የእርሻው አቃ እንዳይጠፋ ከመጠበቅ ውጪ ምን አገባችሁ» በማለት አንዱ በንቀት ተናገራቸው።

እንዲሁ ሲከራከሩ ያስቆሙን ሰዎች አማርኛን የሚናገሩበት ዘዬ ኦሮሞ እንደሆኑ ስለጠቆመኝ ድንገት ካዘኑልኝ ብዬ «ኡኡኡ...ኡኡ!» ድረሱልኝ ከአባቴ ነጥለው እየወሰዱኝ ነው» ብዬ ጮኽኩ። በዚህ ጊዜ ጋቢና የነበረው ሰውዬ «አፉን አፍነው!» አለው።

ከጎኔ የተቀመጠው ሊያፍነኝ ሲሞክር እንዳጋጣሚ አንድ ጣቱን እግኝቼ ነከስኩት። በቡጢ አፌን ነርቶ መልሰ አፈነኝ። በዚህ መሀል የእርሻው ጠባቂዎች መሣሪያቸውን በማቀባበል አንዳይንቀሳቀሱና አንድ በአንድ አጃቸውን ከፍ አድርገው ከመኪናው እንዲወርዱ አዘዟቸው። አፍኖኝ የነበረው «መተናቸው እንለፍ!» አለ። ፊትለፊት የተቀመጠው «አንችልም! እነሱ አራት ናቸው። ሲቪሎችም ወደዚህ እየሮጡ ነው። ወርደን እናሳምናቸዋለን ወይም ሌላ ዘዴ እንፈልጋለን» አለው። በዚሁ ተስማምተው ወረዱ።

አጠገቤ የተቀመጠው እጁን እንዳነሳልኝ መማጸኔን ቀጠልኩ። የታጠቁት ይዘውኝ የመጡትን ሲያነጋግሩ፤ ሲቪሎቹ እኔን መጠየቅ ጀመሩ። አፍነው አየወሰዱኝ እንደሆነና ገድለው አዋሽ ወንዝ ውስጥ ሊጥሉኝ እንዳቀዱ ሲያወሩ አንደሰማሁ (ዋሸቼ) እንባዬን እያዘራሁ ነገርኳቸው። እየተንሰቀሰኩ ነፍሴን አንዲታደጓት ለመንኳቸው። ከአጭር አሰጣ ገባ በኋላ እዚያው ጥበቃዎቹ ጋር እንድቆይና የወረዳውን ፖሊስ አሳውቀው በሕጋዊ መንገድ ይዘውኝ ለመሄድ ተሰማምተው ትተውኝ ጉዟቸውን ቀጠሉ። እኔም ጠባቂዎቹ ጋር ቀረሁ።

ሲያናግሩኝ ከነበሩ ሲቪሎች ውሰጥ አንዱ ወደ ጎን ወስዶ «እውነቱን ንገረኝ፣ ያንተ ጉዳይ ከፖለቲካ ጋር ይያያዘል?» አለኝ። «አዎ» ሰለው፣ «እነዚህ ሰዎች ፖሊሰ ይዘው ከመጡ ይወሰዱኸል። ሰለዚሀ አሁኑኑ መላ እንፈልጋለን፣ መጥፋት አለብሀ» አለኝ። ወዲያው ሁለት ጎረምሶችን መድቦልኝ «የተሰበረ እጁን እንሸለት» ብሎ ወደ አንድ ጎጆ ገባን። እዚያም በጀርባ ሾልከን ወጥተን የአዋሽን ወንዝ በእግራቸው አሻግረውኝ፣ በቦሰት ተራራ ጀርባ አቋርጬ አዳማ ገባሁ። በእነዚያ ጠባቂዎች ሰበብ ፈጣሪ ከረጅም እሰር ወይም ሞት አተረፈኝ።

አዳማ እንደደረሰኩ ትንሽ ተደብቄ በዝምታ ብጠባበቅም ማንም ሊፈልገኝ አልመጣም። በኋላ አንድ የፖሊስ አዛዥ «የፌደራል ደኅንነት ሰዎች አንተን ፍለጋ መጥተው ሲጠይቁን አላየንም ስንላቸው ሄዱ» አለኝ። ከዛሬ ነገ መጥተው ይወሰዱኛል እያልኩ ብሠጋም በዚያው ቀሩ። ከጥቂት ጊዜ በኋላ ሁለቱን ሰዎች መንገድ እንድመራቸው ያመጣቸው ልጅ ወደ አዲሰ አበባ ሲመለስ ተይዞ ምሥጢሩን እንዳወጣ ሰማሁ።

በአዳማ ከተማ አሥራ አንደኛ ክፍል ስማር ለፖለቲካ ያለኝ ፍላጎት እንዲሁም ተሳትፎዬ ጨመረ፤ የሚደረግብኝ ትኩረትም በዚያው ልክ ከፍ አለ። ቀልቤም ከትምህርት ይልቅ ወደ ፖለቲካው እየተሳበች መጣች። ጓደኞቼ «ከዛሬ ነገ ይታሰራል ወይም ወደ ጫካ ይሸፍታል» ብለው ቀን ሲቆጥሩ በሕልሜም ሆነ በእውኔ ያለሰብኩት ሁኔታ ተከሰተና ከሀገር ወጣሁ።

# ትውስታ በምስል #1



የአባቴን National ቴፕ ሪኮርደር ይዤ። ምናልባትም መጀመሪያ የተነሳሁት ፎቶ ሳይሆን አይቀርም።



ከአባቴ ጋር።



ከአባቴ፣ አጎቶቼ ጠሃ እና መሀመድ አሚን እንዲሁም ከእህቶቼ ጋር።



አያቴ ማሞ ቱፋ ከልጅ ልጅ ልጆቹ (Great Grandchildren) ጋር 2008



አያቴ ሙሉ በዳኔ ከእናቴ ሸምሲ ቶላ ጋር 2019 (እ.አ.አ)።



የዱሙጋ ት/ቤት የኪነት ቡድን ትዕይንት በማሳየት ላይ።








ከዱሙጋ ትምህርት ቤት ጓደኞቼ ጋር።



አዳማ ስማር የኦሮሞ ባህልን ማስተዋወቅ እንዱ ሥራችን ነበር
ፎቶው ላይ በባህል ልብስ ባሸበረቁ የክፍል ጓደኞቼ ጋር ለኢሬቻ ስንዘጋጅ።



ለስኮላርሺፕ ከተመረጥነው ተማሪዎች ጋር ጎንደር ፋሲለደስ።



አሰላ ጭላሎ ትምህርት ቤት
ከክፍል ጓደኞቼ ጋር 1992




ወደ ሲንጋፖር ለመጓዝ
የተጠቀምኩበት ፓስፖርት።





ስኮላርሺፕ አግኝቼ ወደ ሲንጋፖር ለመሄድ ስዘጋጅ ቤተሰብ ለመሰናበት ዱሙጋ በሄድኩበት ወቅት፣ አብሯደጎቼ እስከ ወንዙ ድረስ ተከትለውኝ "ከዱሙጋ ኤርፖርት" የተደረገልኝ ሽኝት። ከዱሙጋ እስከ መቻራ በበቅሎ ሄጄ ከዚያ በአውቶቢስ ተጓዝኩ።

# ክፍል አራት - ውጭ ሀገር

### 4.1 ሲንጋፖርን ፍለጋ

አንድ ቀን አሥረኛ ክፍል የተማርኩበት የጎሮ ትምህርት ቤትዳይሬረክተር አበራ ደሳለኝ ጠርቶኝ «ለአንድ የውጪ የትምህርት ዕድል ባለፈው ዓመት ሀገር አቀፍ ፈተና ከወሰዱ ተማሪዎች መካከል የጎበዝ ተማሪዎችን ሰም ላኩ ሲባል ያንተን ሰም ሞልቼ ልኬያለሁ› አለኝ። «እኔ አዚሁ መኖር እናመታገል አንጂ፣ ወደ ውጪ የመሄድ ፍላጎት የለኝምን አልኩት። መምህር አበራ በጣም የሚያሰብልኝ እናየሚረዳኝ ሰው ነበር፤ በትምህርቴ ከማበረታታት አልፎ ከዘመድ ቤት ወጥቼ ሰቸገር የቤት ኪራይ የከፈለልኝ አሱ ነዉ። ቀልቤ በትግል እንደተማረከ ጠንቅቆ ሰለሚያውወቅ፡ ወደ ውጪ አልሄድም የሚለው ተቃውሞዬቆ ብዙም ሳያሰገርመው፡ «ለማንኛውም የመጣው ቅጽ ላይ ሰምህን ሰለሞላሁት፣ መልሳቸውን አይተን አንወስናለን› አለኝ። ከሁለት ወር በኋላ «ማጣሪያውን ስሰላለፍክ ለቃለ-መጠይቅ አዲስ አበባ እንድትመጣ የሚል ደብዳቤ ሲላክ በመምህር አበራ ውትወታ እና ወጪ ወደ ፊንፊኔ ሄድኩ።

ውድድሩ የሚካሄደው ዩናይትድ ዎርልድ ኮሌጅ (United World College) የሚባል ት/ ቤት ለመሄድ ሲሆን፡ ተወዳዳሪዎችን አወዳድሮ የሚመርጠው የውጪ ምሁራን፡ዲፕሎማቶች አና ኢትዮጵያውያን ዜጎችን ያካተተ ብሔራዊ ኮሚቴ ነበር። የዚያን ቀን ከፈተኑን ፈረንጆች መካከል ታዋቂው የታሪክ ምሁር ሪቻርድ ፓንክረስት እናባለቤታቸው ሪታ ፓንክረሰት ይገኙበታል። በመላው ሀገሪቱ ካሉ ሁለተኛ ደረጃ ት/ቤቶች ከአያዳንዳቸው አንዳንድ ጎበዝ ተማሪዎችን ተቀብለው በመመዘን ሀያ አምስት ተማሪዎች በአካል ቀርበው አንዲወዳደሩ ጋበዙ። ውድድሩ የተካሄደው ሳንፎርድ (Sanford English School) ት/ቤት ሲሆን፣ ሙሉ ቀን የፈጀው ፈተና ጽሑፍ፣ ቃለ -መጠይቅ፣ ጠቅላላ አውቀት እናማኅበራዊ ግንኙነትን ያካተተ ነበር። ለውድድሩ የቀረቡት አብዛኞቹ ተማሪዎች አንግሊዝኛን አቀላጥፈው ይናገራሉ፤ በሰዋሰው (grammar) የተሻልኩ ብሆንም፣ በንግግር ግን ከአነሱ ጋር አልመጣጠንም። ከጽሑፍ ፈተና ውጪ ቃለ-መጠይቁም ሆነ የማኅበራዊ ግንኙነት መመዘኛው በአንግሊዝኛ ስለነበር፡ ኣንግሊዝኛን አቀለጥፈው የሚናገሩ ተማሪዎች ባሉበት የማሸነፍ ዕድል አለኝ ብዬ አላሰብኩም።

ወድድሩን ሰንጨርሰ፣ «ከመሄዳችሁ በፊት ካሸነፋችሁ ወደ የትኛው ሀገር መሄድ እንደምትፈልጉ ከተሰጡት አማራጮች ውስጥ (ከአሥር ሀገራት መካከል) አምሰት በመምረጥ እንደፍላጎታችሁ በደረጃ ከአንድ እስከ አምሰት አዚሀ ቅጽ ላይ ፃፉ» በማለት ቅጹን

ሰጡን። ከአሥሩ ሀገራት መከካል  እንደ አሜሪካ፣ እንግሊዝ፣ ኖርዋዊይ እናጣሊያን የመሰሰሉ ቢኖሩም፡ እኔግን ሲንጋፖርንብቻ ሞልቼ ቅጹን መለሰኩ። ለዚሀም ሁለት ምክንያቶች ነበሩን። የመጀመሪያው ምክንያቴ ውድድሩን አሸንፋለሁ ብዩ ሰላለሰብኩ ከተዘረዘሩት ሀገራት መካከል ለመምረጥ አልተጨነኩም። ሁለተኛው ደግሞ ሲንጋፖር የሚለውን ሰም በልጅነቴ አይቼ ተማርኬበት ስለነበር ነው።

አናቴ አጣን አንድገዛ ሰትልከኝ መጠቅለያውን ጋዜጣ ተቀብዩ በማንበብ የአንግሊዝኛ ችሉታዩን ለማሻሻል አሞክር ነበር። በወቅቱ አጣን ለመጠቅለል ከሚውሉ ጋዜጦች መካከል የእንግሊዝኛው "Strait Times" አንዱ ሲሆን፣ የሚታተምበት ሀገር ሲንጋፖር  እንደሆነ ይጻፍበታል። ጋዜጣው ላይ የሚወጣው የከተማዋ ምሰል እጅግ ማራኪ ከመሆኑ የተነሳ እንድ ቀን በሄድኩ አያልኩ እመኝ ነበር። ሀገራቱን ምረጡ ተብለን ቅጽ ሲሰጠን የአሥሩን ሀገራትት/ቤቶች መረጃ የያዘ ወረቀች (brochure) አብረው ሰጡን። እንደ አጋጣሚ ከላይ የነበረው የሲንጋፖር ስለነበር በዚያው ቅፅበት ከ Strait Times ጋር ያለኝ የልጅነት ትዝታ ስለተቀሰቀሰ ሲንጋፖርን ብቻ ሞልቼ መለሰኩ።

ውድድሩ ሲጠናቀቅ መሸቶ ስለነበር ወደ አዳማ ለመመለስ ባለመቻሌ ዘመድ ቤት ለማደር ወሰንኩ። ፈታኝ ኮሚቴው «ድንገት የምንፈልጋችሁ ከሆነ ልናገኛችሁ የምንችልበትን ሰልክ ቁጥር ሰጡን›» ብሉ በጠየቀን ጊዜም የዚሁ የማርፍበትን ዘመድ ቤት ሰልክ ቁጥር ሰጠሁ።የትራንስፖርት እናሌሎች ወጪዎችን አስልተው ሁለት መቶ ሥላሳ አምሰት (235) ብር ሰጡን። ቤት እንደገባሁ ያገኘሁትን ገንዘብ እንዴት እንደምጠቀም ማሰላሰል ጀመርኩ። መምህር አበራ ለትራንስፖርት ወጪ የሰጠኝን መልሼ፡ ያረጀ ፍራሼን ቀይሬ፡ በተረፈው ጓደኞቼን አጋብዛለሁ አያልኩ ሰደምር እና ሰቀንሰ ቆየሁ።

በወቅቱ ዘወትር ቅዳሜ ዕለት ሻይ ቤት አየሄድን ደንጋ (Dhangaa) የተሰኘውን ተወዳጅ የኦሮምኛ መዝናኛ ፕሮግራም በኢትዮጵያ ቴሌቪሽን እንከታተል ነበር። ፕርግራሙ ሳያልቅ ያዘዝነውን ሻይ ከጨረሰን የካፌውን ወንበር ለቅቀን አንድንወጣ እንገደዳለን። በዚህ ምክንያት አንድ ሻይ አዘን አንዳታልቅብን ትንሽ ጎንጨት እያደረግን የአንድ ሰዓቱ የደንጋ ፕሮግራም አሰኪያልቅ ድረስ እንቆጥባታለን። አስተናጋጇ መጥታ «መቀመጫውን ለሌላ ተሰተናጋጅ ልቀቁ› ስትለን «ሻያችንን አልጨረሰንም› ብለን አንከራክራለን።

በዚህ መሀል ሻዩ  ይቀዘቅዛል ወይም ዝንብ ይገባበታል። ሰለዚሀ ባገኘሁት ገንዘብ አራሴን እናጓደኞቼን እጃችን ለይ ከሚቀዘቅዝ ሻይ ነጻ  እንደማወጣ አያሰብኩ ደሰ አለኝ። በዚህ መሀል ያረፍኩበት ቤት ሰልክ ተደውሎ ተጠራሁ። የደወለልኝ ሰው ቀን ሲፈትኑን ከዋሉት የኮሚቴ አባላት ውስጥ አንዱ ነበር። ማሸነፌን ነግሮኝ «አንኳን ደስ አለሀ› አለኝ። ድምጹ ከአንድ ጓደኛዬ ጋር ሰለተመሳሰለብኝ የሚቀልድ መስሉኝ «አቦ ቀልዱን ተው፤ አሪፍ ገንዘብ ስለሰጡኝ ነገ ፈታ አንላለን ጠብቀኝ› አልኩት። ሰውዬው ግን የኮሚቴው አባል መሆኑን ቀን ያወራነውን ነገር በማሰታወስ በድጋሚ አረጋገጠልኝ። በመቀጠል ወደ ሲንጋፖር  እንደምሄድ፤ በአንድ ሳምንት ውስጥ ማብራሪያ ለማግኘት አንድመለስ ነግሮኝ ማንኛውም ዓይነት ጥያቄ ካለኝ ኮሚቴውንም ሆነ አሱን ማግኘት  እንደምችል ገልፆ ቁጥሩን ሰጥቶኝ ሰልኩን ዘጋው።

አሁን የማሸነፌ ዜና አውነት መሆኑ ሲረጋገጥ «ትሄዳለሀ» የተባልኩባትን ሲንጋፖር ካርታ ለይ መፈለግ ጀመርኩ። ከሲንጋፖር ጋር ያሰተዋወቀኝ Strait Times ጋዜጣ በአንግሊዝኛ

ቋንቋ ይታተም ስለነበር፣ ሲንጋፖር ከአውሮፓ ከተሞች አንዷ እንጂ በፍጹም እስያ ውስጥ ትሆናለች ብዬ ሰላላሰብኩ አውሮፓ አህጉር ውስጥ ሰፈልግ ቆየሁ። ፈልጌ ማግኘት ሰላለቻልኩ ለቅድሙ ሰውዬ ደወልኩለትና «እኔ የምሄድባት ሲንጋፖር የትኛው አህጉር ነው የምትገኘው?» ብይ ጠየኩት። እሱም ሣቅ እንደማለት ብሉ «አምስት ዕድል እያለህ ሲንጋፖርን ብቻ ጽፈህ አሁን የት ነው ብለህ ትጠይቀኛለህ? እኛ እኮ ሲንጋፖርን ብቻ ሰትመርጥ ሄደህ አይተኻት ብዙ ነገሯን የወደድክ ወይም ዘመድ ኖሮህ በሰጡህ መረጃ የተማረክ መሰሎን ነበር። አሁን እንደመረጥካት መልሰህ ካርታ ላይ ፈልጋት» ብሉ አፌዘብኝ። በራሴ ሰላፈርኩ ከዚህ በላይ መጠየቅ አላሰፈለገኝም።

በማግሰቱ ጠዋት አዳማ እንደደረስኩ ለመምህር አበራ ደውዬ ደሰታዬን ካካፈልኩ በኋላ፣ ሲንጋፖር የት እንደምትገኝ ፈራ ተባ እያልኩ ሰጠይቀው፡ እስያ ውስጥ እንደሆነች ነገረኝ። የእስያን ካርታ ከፍቼ ሲንጋፖርን ቶሉ ማግኘት ቀላል አልሆነም። ከብዙ ፍለጋ በኋላ በታይላንድ እና ማሌዥያ አቅራቢያ የምትገኝ ትንሽዬ ነጥብ ሆና አገኘኋት። የአውሮፓ ከተማ መስላኝ የመረጥኳት ሲንጋፖር እስያ ውስጥ መገኘቷ ብዙም አላስደሰተኝም። ይባሰ ብሎ በዚያው ሰሞን የSARS ቫይረሰ ወረርሽኝ በሲንጋፖር ውስጥ እየተሰፋፋ መሆኑ በሬዲዮ መወራት ጀመረ።

ይህ ዜና ቤተሰቦቼን እናጓደኞቼን ቢያሰፈራቸውም በመምህሬ ግፊት እናምክር ለመሄድ ወሰኜ ወደ አዲሰ አበባ ተመልሼ ከኮሚቴው ለጉዞው አሰፈላጊ ሰለሆኑ ነገሮች መመሪያ ተቀበልኩ። ፓሰፖርት አንዳወጣና ሰመለሰ ቪዛ እንደሚያሰጡኝ ነገሩኝ። ፓሰፓርት ለማውጣት ሰሄድ «ዕድሜህ 18 ሰላልሞላ እናትህን ወይም አባትህን ማምጣት አለብህ» ብለው መለሱኝ። አባቴ በሕይወት የለም፤ እናቴን ከጹሙጋ ለማምጣት ጊዜ አልነበረም። በአንድ ሳምንት ውስጥ ፓስፖርቱ ለቪዛ ኤምባሲ መግባት ሰላለበት በአሰቸኳይ አንዲሰጠኝ የድጋፍ ደብዳቤ ተጽፎልኛል።

በወቅቱ ጹሙጋ ሰልክ ስላልነበረ እናቴን በአካል ሂጄ ነግሪያት ማምጣት ነበረብኝ። ከአዲሰ አበባ ጹሙጋ ለመሄድ ብቻ ፈጠነ ከተባለ ሦስት ቀን ይፈጃል። ያውም በሁሉም ከተሞች በማለዳ ወጪ አውቶቡሰ መያዝ ከተቻለ። ጹመጋ የሚኪድበት ብቸኛ መንገድ በምዕራብ ሐረርጌ በኩል ነበር። ከአዲሰ አበባ ማልጄ ከተነሳሁ ጭሮ አድሬ፣ ከጭሮ ተነሰቼ በድጋሜ መቻራ አዳር ይሆንና በማግሰቱ በአግር ጉዞ ጹሙጋ ይደረሰል። እናቴን ከዚያ ድረሰ ለማምጣት በትንሹ ደርሶ መልሰ ሰድሰት ቀን ሰለሚፈጅ ፓስፖርት አውጥቼ ለኤምባሲ ለመሰጠት ያለኝ ሳምንት አለቀ ማለት ነው።

ያጋጠመኝን ችግር ኮሚቴው ኢሚግሪሽሽን አንዲያደርሰኝ ለመደበልኝ ሾፌር ሳወያየው «አሰቲ ቆይ መላ አንፈልጋለን› ብሎ ከመኪና ወረደና በአካባቢው ጉዳይ የሚያሰጨርሱ ወጣቶችን አነጋግሮ እንደተመለሰ ፊቱ በደሰታ በርቶ «መፍትሔ ተገኝቷል» አለኝ። በጉጉት «ምን ዓይነት መፍትሔ?» ሰለው «እናት አንከራይልኸለን› ብሉ መለሰልኝ። የሚያወራው ነገር ስላልገባኝ አንዲያሰረዳኝ ሰጠይቀው ደላሉቹ አንዲት አሮጊት በብር አግኝተው፣፡ መታወቂያ በእናቴ (ሾምሲ ቶላ) ሰም አውጥተው ምን ማለት አንዳለብን ሁለታችንንም አሰጠንተው እንደሚያዘጋጁን ነገረኝ። በዚሁ መሠረት ለአሮ፲ጊቷ መታወቂያ አውጥተውላት በሦሰተኛው ቀን ይዣት ኢሚግሪሽን ገባሁ።

ተራዬ ደርሶ ወደ አንድ መሰኮት በመሄድ የማመልከቻውን ቅጽ ፎቶግራፍ እናደረሰኝ ሰጠሁ።

ከመሰኮቱ ጀርባ ያለው ሰው አሮጊቷን እናአኔን ጥቂት ጥያቄዎች ጠየቀን። መጀመሪያ በአማርኛ ሲያናግረን ቆይቶ በመሀል «ዕድሜሽ ስንት ነው?» ብሎ አሮጊቷን በአፋን ኦሮሞ ሲጠይቃት «ሰልሳ› ብይመለሰኩለት። «የጠየኩት እናትህን ነው» ሲለኝ ሁታለታችንም ደነገጥን። ቀልጠፍ ብዬ «አይ አሷ አፋን ኦሮሞ አትችልም» አልኩት። «ለምን? ኦሮሞ አይደለችም?» ብሎ በጥያቄ ሲያጣድፈኝ «የተወለደችው አዲስ አበባ ነው» ብዬ መለሰኩለት። «አዲስ አበባ ብትወለድስ፣ አርሲ ኖራ አንዴት ቋንቋ መልመድ አቃታት?» ብሎ አፈጠጠብኝ። ማመልከቻዬ ላይ የትውልድ ቦታዬ አርሲ ተብሎ መጻፉን በማሰተዋሉ ነበር  እንደዛ ያለው። በቃ ተያዝኩኝ ብዬ እግሮቼ ሲንቀጠቀጡና ላብ በጀርባዬ ሲንቆረቆር ይሰማኛል። «አስመሰለሀ ልብህ ውልቅ ብሏል፡ አንኳንም አኔ ላይ ጣለሀ!» ብሎ ፓስፖርቴን ከሁለት ቀን በኋላ ተመልሼ አንድወሰድ በፈገግታ ታጅቦ አበሰረኝ፣ ድንጋጤዬ በደስታ ተተክቶ አመሰግኜ ወጣሁኝ።

## 4.2 ሰሜኑን ብቻ ያየንበት የሀገርህን አወቅ ጉዞ

ፓስፖርቴን ወስጄ ቪዛ እንዲመታበት ሰጥቼ ቤተሰቤን ለመሰናበት ወደ ጆሙጋ አመራሁ። በትምህርት ምክንያት የተለዩኝ የልጅነት ጓደኞቼ ውጪ እንደምሄድ ሲሰሙ ከመቻራ፣ ከገለምሶ እና ከድሬዳዋ መጥተው ተገናኘን። ወጣቶች ጨፍረው፣ የሀገር ሽማግሌዎች መርቀው ሸኙኝ። ወደ አዲስ አበባ ሰመለሰ የኮሚቴው ሰዎች «በምትሄዱበት ሀገር ኢትዮጵያን በአምባሳደርነት ማሰተዋወቅ ሰላለባችሁ፣ ከመሄዳናችሁ በፊት ሀገራችሁን ማወቅ ይኖርባችኋል› በማለት የኢትዮጵያ ቱሪዝም ድርጅት ሰኮላርሺፕ ለደረሰን አምስት ተማሪዎች ወደ ባሕርዳር፣ ጎንደር እና ላሊበላ ከተሞች በመውሰድ አስጎበኙን። ይህ ጉዞ ለመጀመሪያ ጊዜ ክኦሮሚያ የወጣሁበት አጋጣሚ ነበር።

የአማራ ክልል ሕዝብ ካሰብኩት በላይ አስከፊ ድህነት ውስጥ እንደሚገኝ የዓባይን ወንዝ እንደተሻገርኩ መንገድ ላይ ማሰተዋል ጀመርኩ። ከመንገዱ ግራና ቀኝ የምናያቸው ገበሬዎች የተጎሳቆለ ሰውነታቸውን በተቀዳደደ ልብስ ሸፍነው ይታያሉ። በተለይ ሴቶቹ አጅግ ከመክሳታቸውም በላይ ከባድ ሸክም ተሸክመው ባዶ አግራቸውን ይሄዳሉ። ከባሕርዳር ወደ ጢሰ ዓባይ ፏፏቴ ስንሄድ፣ አንዲት አሮጊት ድፍርስ ውኃ ከጉድጓድ ውስጥ ሲቀዱ አየሁ። የዓባይ ወንዝ አሳቸው ከሚቀዱበት ከሦስት መቶ ሜትር በላይ የሚርቅ አይመሰለኝም። ጠጋ ብዬ ወንዙ አዚህ አያለ ለምን ድፍርስ ውኃ ይቀዳሉ?» ሰላቸው በሚያሳዝን ድምፅ «ልጄ አውነት ነው ዓባይ ሞልቶ በእኛው ደጅ እየፈሰሰ ያልፋል። ግን ማን ከሸለቆው ውስጥ ያውጣልን?» አሉን። ባደኩበት አካባቢ በበጋማነት እናበበረሃማነት የተነሳ ወንዞች ስለሚደርቁ፣ አሮጊቷ የሚቀዱትን ዓይነት ውኃ ለመጠጣት ይገደዳሉ። በአነሰተኛ የውኃ ሞተር ከሸለቆ ውስጥ የሚሰብላቸው አካል ባለመኖሩ፡ አሮጊቷ ዓባይን በዓይናቸው አያዩ የደፈረሰ ውኃ ለመቅዳት ተገደዱ። ያየሁት ነገር በአማርኛ ክፍለ ጊዜ «የዓባይን ልጅ ውኃ ጠማው!» ብለን የተማርነውን ብሂል በገሃድ አሳየኝ።

ጎንደርን ጎብኝተን እዚያው ካደርን በኋላ በደሴ ዞረን ወደ አዲስ አበባ አየሄድን አያለ መኪናችን ተበላሽቶ ለመጠገን ገጠር ውስጥ ሰንቆም፣ መንገድ ዳር ካለ ጎጆ ቤት ልጆች አየሮጡ ወደ እኛ መጡ። እኛን በአማርኛ አያናገሩ አርሰ በራሳቸው ግን በአፋን ኦሮሞ ያወራሉ። በአፋን ኦሮሞ ሳናግራቸው በደሰታ ተውጠው ከበቡኝ። የአነጋገር ዘዬአቸው ካደኩበት አካባቢ ጋር ተመሳሰለብኝ፤ በዴሳ እናገለምሶ አካባቢ ያለሁ ያህል ተሰማኝ። ሰሜን፣ የመጣሁበትን እና ወዴት እንደምሄድ አየተቀባበሉ ጠየቁኝ። ጎልማሳ ሰው በቀዬው ያለ እንደሆነ ጠይቄ ስላረጋገጡልን ለማናገር ወደዚያው አመራሁ በቤቱ አጠገብ ካለ ማሳ ውስጥ በአንድ ትልቅ ዛፍ ሥር አራት ሽማግሌዎች ተቀምጠው አየሁ። ከሎይታ (የሙስሊም ወንዶች ቆብ) ሰላደርጉ «አሰ-ሰላሙ አለይኩም» አልኳቸው። «ወአለይኩም አስ-ሰለም› ብለው ከተቀመጡበት አየተነሱ መለሱልኝ። እንደኛቸው አጃቸውን ቀድመው ዘረጉልኝ። ለምላሹ አጄን ሰዘረጋ አጄን ከፍ አድርጎ አይበሉባዬን ስለሳመው አኔም አፀፋውን መለስኩ፡ አራቱም በዚህ መልኩ ሰላም አሉኝ። ይሀን ዓይነት ሰላምታ አሰጣጥ ከጆሙጋ ከወጣሁ በኋላ አይቼ ሰለማላውቅ ያደኩበት

አካባቢ ሽማግሌዎችን ያገኘሁ መሰለኝ። ሽማግሌዎቹ ማንነቴን፣ ከየት እንደመጣሁ እና የት እንደምሄድ ጠየቁኝ። እኔም ሰለ አካባቢው ሕዝብ ብዙ ነገር ጠይቄ ማወቅ ቻልኩ።

ከአነሱጋር አያደረኩ የነበረው ጭውውት ሰሜቴን ተቆጣጥሮት ጉዞ ላይ መሆኔን ሰላሰረሳኝ፡ምን ያሀል  እንደቆያሁ ሳለውቅ አሰጎብኚያችን ሊጠራኝ መጣ። ከአዲስ አበባ ተነሰተን፣ ባሕርዳር፣ ጎንደር እናደሴ እስክንደርሰ ለአምሰት ቀናት አብረን የነበርን እና ብዙ ነገር ሰንጨዋወት አንድም የአፋን ኦሮሞ ቃል ሳይወጣው ቆይቶ «nagaa ooltanii? (ደህና ዋላችሁ?)» ብሎ ጨዋታችንን አቋረጠ። ሽማግሌዎቹን ሰላም ብሎ በጠራ የአፋን ኦሮሞ አነጋገር ሰለ ሀገሩ፣ ስለ ጤናቸው፣ ሰለ ምርቱ ጠየቃቸው፡ እኔ ተገርሜ አየዋለሁ። «ቆይተን አያወራን ብናድር ምኞቴ ነበር። አዲሰ አበባ መግባት ሰለሚኖርብን መሄድ አለብን መርቁን» ብሉ የተወሰነ ገንዘብ አውጥቶ ሰጣቸው። ሽማግሌዎቹም «በሰላም ግቡ,» ብለው እስከ መንገድ ዳር ሸኙን። ወደ መኪና ስንሄድ «አጅሬው! አንተ ብቻ ቋንቋ የምትችል መሰሎሀ ነበር አይደል?» አለና ሣቅ አለ። መኪና ውስጥ ከገባን በኋለ በአፋን ኦሮሞ ሳናግረው ሊመልሰልኝ አልፈቀደም ፤ ነገሩ ገባኝና ተውኩት።

ከመሄዳችሁ በፊት ሀገራችሁን ዞራችሁ ማየት አለባችሁ ሰለተባለ፣ ከሰሜኑ ጉዞ በኋላ ወደ ደቡብና ምሥራቃዊ የሀገራችን ክፍሎች የምንሄድ መሰሎኝ ነበር። አዲሰ አበባ ልንገባ ሰንል «ቀጣይ ጉዟችን መቼ ነው?» ብዬ በየዋህነት ጠየኩ። አስጎብኚያችን «ለሌላ ጉዞ የለም፤ ይኸው ነው። ከዚሀ በኋለ ወደተመደባችሀበት ሀገር ትሄዳላችሁ» አለን። ፊንፊኔ  እንደደረሰን ከመኪናው ወርደን ልንለያይ ስንል «አውቃችሁ ለዓለም የምታሰተዋውቋት ኢትዮጵያ ሰሜን አንጂ ደቡብ የለችም» ብሉ ፈገግ አለ። ለዚህ ጉዞ ያየኸውን ብቻ ሳይሆን፣ ካላየኸውም የሆነ ነገር  እንደተገነዘብክ ተሰፋ አደርጋለሁ፡ በትምህርትህ በርታ። በሄድክበት ሁሉ ራስህን እና ሕዝብህን አትርሳ» ብሉኝ ጥቂት ገንዘብ ኪሴ ውስጥ ሻጥ አደረገልኝ።

አዳማ ተመልሼ ዘመድ እናጓደኞቼን ከተሰናበትኩ በኋላ ለጉዞ መሰናዳት ጀመርኩ። በሰንብቱመሀል አንድ አሥቂኝ ነገር ሰማሁ። በወቅቱ የነበረችኝ ፍቅረኛ ዘመድ በጣም ይጠላኝ ስለነበር ልጅቷን ከአኔ ለመነጠል በሰንት ምክርና ተግሳጽ አቅቶት ተወ። ወደ ውጪ ልሄድ መሆኑን ሲነግሩት «የት ሀገር ነው የሚሄደውን» ብሎ ጠየቀ። ሲንጋፖር መሆኑን ነገሩት። አሱም ሲንጋፖር መሄድ ትልቅ ነገር ሆኖ ነው የምታዳንቁት? ሲንጋፖር ማለት ቻይና ነው። ቻይና መሄድ ውጪ ሀገር መሄድ አይደለም» በማለት አጣጣለባቸው አሉ። ወሬውን የሰማሁ ዕለት ሥቄ ዝም አልኩ።

ሲንጋፖር ከሄደኩ በኋለ  እንደ አሁኑ በኢንተርኔት እናበሰልክ መገናኘት ሰለማይቻል በውድ ገንዘብ ካርድ ገዝተን ወደ ሀገራችን  እንደውላለን። በወቅቱ የእጅ ሰልክ ሰላልነበረ ቤት በመደወል የምንፈልገውን ሰው ማስጠራት ግዴታ ነበር። እናም ሲንጋፖር ደርሼ ከሳምንት በኋላ ፍቅረኛዬን ለማናገር ቤታቸው ስደውል ሰልኩን ያነሳውን ወንድ «እከሊት አለች?» ብዬ የልጅቷን ስም ጠርቼ ሰጠይቀው ንዴት በተቀለቀለበት ድምፅ «የለችም!» አለኝ። «የት ሄደች›» ብዬ ከመጠየቄ «ሞታለችን» ብሎ ጆሮዬ ላይ ጠረቀመብኝ። በደንጋጤ አብሮን ይማር ወደነበረ ጓደኛዬ ስደውል ደሀና መሆኗን እናየዚያኑ ቀን ት/ቤት አንዳያት ነገሮኝ በማግሰቱ ቤቱ ጠርቷት በሰልክ  እንደሚያገናኘን ቀጠሮ ያዘልኝ። በቀጠሮው ሰዓት ደውዩ ሳናግራት ሰልኩን አንሰቶ «ሞታለች›»በማለት ያሰደነገጠኝ ያ ዘመዷ እንደሆነ ነገረችኝ።

## 4.3. ሕልም እናእንግሊዝኛ

በ1995ዓ.ም. ነሐሴ ወር አጋማሽ ኢትዮጵያን ለቅቄ ወደ ሲንጋፖር በረርኩ። አውሮፕላን ስሳፈር የመጀመሪያዬ ነበር። አውሮፕላኑ ገና ሲነሳ ሆዴ ቢላወስም፣ በኋላ ተረጋግቼ መጽሐፍ ማንበብ ጀመርኩ። በኢትዮጵያ አየር መንገድ በረራ ወደ ታይላንድ ባንኮክ ከደረሰን በኋላ፣ አውሮፕላን ቀይረን ወደ ሲንጋፖር አቀናሁ። ሲንጋፖር እንደደረሰኩ ወዲያውኑ አዳዲስ ገጠመኞችን ማሰተናገድ ጀመርኩ። የትምህርት ቤቱ ዶርም (dormitory) አስተባባሪ ከአውሮፕላን ማረፊያ ተቀብላኝ መኪና ውስጥ እንደገባን ከአሽከርካሪው ጋር አስተዋወቀችኝ። «Jawar, meet my partner Steve» እለችኝ። መኪና ውስጥ ስንገባ ስለሳመችው ባለቤቴ ነው እንዳለችኝ ቆጠርኩት። ቤት ሰንደርሰ አንድ ሌላ ወንድ መጥቶ በርሳዬን ተቀብሎ ወደ እንግዳ መቀበያ(Reception) ሰንደርሰ፣ «Jawar, meet Max, he is my partner. He is responsible for male dormitory and will show you your room›› አለችኝ። አሁን ደነገጥኩ።

ሁለተኛውን ሰውዬ እንደ በፊቱ «partner» ብላ ሰለገለጸች ሁለት ባል ይኖራት ይሆን? ብዩ አሰብኩ። ከአዲስ አበባ ሳንነሳ በፊት በሀገራችን እና በውጪው ዓለም መካከል ሰላለው የባሕል ልዩነት የግንዛቤ ማሰጨበጫ (cultural orientation) ተሰጥቶን ነበር። የተመሳሳይ ፆታ ግንኙነት (Homosexuality) ጨምሮ ሀገራችን ውስጥ የማይታወቁ ብዙ ነገሮች ሊያጋጥሙን እንደሚችሉ እና የሀገሬውን ባሕል አክብረን በትዕግሥት ትምህርታችንን አንድንማር አበክረው ነግረውናል። ምናልባት በሀገሩ ባሕል ሴት ሁለት ባል ሊኖራት ይችል ይሆናል ብይ ዝም አልኩ።

ከጥቂት ቀናት በኋላ ማክሰ (የዶርማችን አስተዳዳሪ) መኖሪያ ቤቱ ጋበዞ ከሚሰቱ እናከልጆቹ ጋር ሲያሰተዋውቀኝ ነገር ዓለሙ ድብልቅልቅ አለብኝ። መጀመሪያ አንድ ሴት ሁለት ባል የምታገባ መሰለኝ። አሁን ደግሞ ሌላ ሴት ሲጨመር የባሰውን ተምታታብኝ። እንደው አራቱም ተጋብተው ይሆን ብዬ ልጠይቅ አሰብኩና ፈርቼ ተውኩት። ከአንድ ሳምንት በኋላ ከሰዋዚላንድ ከመጣ ልጅ ጋር ሰለተቀራረብን ደፈር ብዬ ሰጠየቀው «partner» የሚለው ቃል ሁለት ትርጉም ሊኖረው እንደሚችል ነገረኝ። እንደኛው በሕግ ሳይጋቡ እንደ ባል እናሚሰት አብረው የሚኖሩ ሴት እናወንድን ግንኙነት የሚገልጽ ነው። አንድን ሥራ በጋራ የሚሰሩ ሁለት ሰዎችም «partner» ተብለው እንደሚጠሩ ገለጸልኝ። ሰለዚህ አውሮፕላን ጣቢያ ያሰተዋወቀችኝ ሰው ባሏ ሲሆን፣ ት/ቤት ከደረሰን በኋላ ያሰተዋወቀችኝ የዶርም አስተዳዳሪ ደግሞ የሥራ ባልደረባ (colleague) እንደሆነ አሰረዳኝ። በዓመቱ መገባደጃ ለክረምት ዕረፍት የሽኝት ፐሮግራም ሲደረግ አራቱ ሰዎች በተገኙበት ያን የመጀመሪያ ሳምንት ገጠመኝ ነግሯያቸው ተማሪዎቹን እናአስተማሪዎቹን አሳቃቸው።

ሲንጋፖር በዚህ መልኩ ገና ከመሄዱ በማይረሳ ገጠመኝ ተቀበለችኝ። ሄጄ በሦስተኛው ቀን ሌላ ጨመረችልን። ለአዲስ ገቢ ተማሪዎች አቀባበል የእራት ድግስ በአንድ ታዋቂ ምግብ

ቤት ተዘጋጀ። የባሕር ምግቦች (sea food) በመሥራት የሚታወቅ ሬሰቶራንት ነበር። እንደተቀመጥን የምግብ ዝርዝር (menu) አመጡልን። የማውቀው የምግብ ሰም ሰላልነበረ አላውቅም ብዬ መጠየቁ አሰፈርቶኝ ከተዘረዘሩት ውስጥ አንዱን በጣቴ ጠቁሜ አዘዝኩ። ከዚያም ካዘዝኩት ምግብ ጋር አንድ በውኃ የተሞላ ትራንስፓረንት (transparent) የሆነ ጠርሙስ አንበጣ የሚመስል ነገር ውሰጡ አየተርመሰመሰ አምጥተው አሰቀመጡት። «ይሄ ምንድነው?» ብዬ ሰጠይቅ ያዘዝከው ምግብ ሳይጠበስስ በፊት እንዲህ ነበር፣ ሰሙም Shrimp ይባላል አሉኝ፣ ምግቡ ትኩሰ (fresh) መሆኑንና ወዲያው ከውኃ ውስጥ ተይዞ መጥቶ ባዘዝኩበት ቅፅበት መጠበሱን ለማረጋገጥ አንዳመጡት ነገሩኝ። አስተናጋጁ እና አጠገቤ የነበረ አስተማሪ እንደጥሩ ነገር አየተቀባበሉ ሲያወሩ አኔግን አቅለሸልሾኝ የቀረበውን አራት መብላት አይደለም ቀን የበለሁትም ሊያሰመልሰኝ ወደ መፀዳጃ ቤት ሮጥኩ። ሰመለስሰ የቀረበውን ምግብ አንዲያነሱት ስነግራቸው፡ ደንግጠው አነሱትና «ሌላ ነገር አንዘዝልሀ? » አሉኝ። በጊዜውበጠርሙሱ ውስጥ ያየሁትን ምሰል ከአእምሮዬ ለማጥፋት አየሞከርኩ ስለነበር ምግብ መብላት አላሰኘኝም። ከምግብ ቤቱ ለመውጣት ብቸኩልም፣ የአራት ፐሮግራሙ አሰኪያልቅ እንደምንም ብዬ መጠበቅ ነበረብኝ ።

ከዚያን ቀን በኋላ የሀገሪቱ ምግብ ሰላሰጠላኝ ከሁለት ወር በላይ ዳቦ በቅቤ እናማር ቀብቼ አየበላሁ ሕይወትን ገፋኋት። በሂደት ሩዝ እናየዶሮ ሥጋ መሆኑን በዓይነ አረጋግጬ መመገብ ጀመርኩ። የባሕር ምግብ የዚያኔ አርም ያልኩ አሰካሁንም አልበላም። ብዙ ሰዎች እሰያ መኖሬን ሲሰሙ የ55 ደ664 ምግብ ቤት ለጋብዙን ይፈልጋሉ፡ እንደማልወድ ሰነግራቸው በጣም ይገረማሉ። ከላይ የገለጽኩትን ታሪክ ነግሩ በማሳመን ሌላ ቦታ አንሄዳለን።

ሲንጋፖር በ2ር፡545 ፓቷ ጋዜጣ ካየኋትም በላይ ቆንጆ እና ያደገች ሆና አግኝቻታለሁ። ከመሄዴ በፊት ሲንጋፖር ዋና ከተማ ሆና ሌሎች ትንንሽ ከተሞች እናገጠሮች ያሏት ይመሰለኝ ነበር። አንድ ቀን በመኪና ለጉብኝት ወጥተን ከተማዋን ከጥግ እስከ ጥግ ዞረን ለማየት ከሁለት አስከ ሦስት ሰዓት ብቻ ወሰደብን። በሁሉም አቅጣጫ መጨረሻ ላይ ያየነው ባሕር ስለነበር «ቀጣዮቹ ከተሞች በየት በኩል ነው የሚገኙት? › ብዬ ሰጠይቃቸው ሌላ ከተማም ሆነ ገጠር እንደሌለና ከተማዋም ሀገሪቷም የጎበኘናት ብቻ እንደሆነች ነገሩኝ።

## 4.4. እውቀት እና ብልሀት ያበለፀጋት ሚጢጢ ሀገር

ሲንጋፖር እንደደረሰን የሀገሪቷን ባሕል እናሕግ በተመለከተ የግንዛቤ ማሰጨበጫ ለሁለት ሳምንት ሲሰጠን፣ ሀገሪቱ ሲበዛ ሕግ አጥባቂ በመሆኗ ጥንቃቄ እንድናደርግ ደጋግመው አሳሰቡን። በተለይ ንጽሕና እናሥነ-ምግባር ላይ ጠንካራ አቋም እንዳላት አስረዱን። አደንዛዥ ዕፅ በሀገሪቷ ይቅርና ሌላ ሀገር ተጠቅሞ መጥቶ ሲንጋፖር ሲመለስ ደሙ ውስጥ የተገኘ ሰው በረጅም አሰር እንደሚቀጣ ነገሩን። እንደኛ ተማሪ ከሆነ ደግሞ ቅጣቱ ከሀገር መባረር ይሆናል፡ ያውም ዕድለኛ ከሆነ። በንጽሕና በኩል እንደ ወረቀት ያለ ቆሻሻ መጣል ያስቀጣል። ማስቲካ ማኘክም ሆነ ከሀገራችን ሰንመለስ ይዞ መምጣት በእሰር የሚያሰቀጣ ወንጀል እንደሆነ አሰጠነቀቁን። ምክንያቱም ማሰቲካ ከተማ ሰለሚያቆሽሽ ነው ተባለ።

በወሬ እንደሰማነው ከሆነ አንድ ቀን የሀገሪቷ የመጀመሪያ መሪ ሊ ኩዋን ይው ሲንጋፖር ከቅኝ ግዛት ነጻ እንደወጣች ገና ሥራ የጀመረ ባቡር ለማየት ሄዶ በሩ አልዘጋ ሲል አየ አሉ። ጠጋ ብሎ ሲመለከት በሩ አንዳይዘጋ የከለከለው ታኝኮ የተጣለ ማስቲካ ሆኖ ተገኘ። ከዚያን ዕለት አንሰቶ ማሰቲካ መብላትም ሆነ ወደ ሀገር ውስጥ ማሰገባት ከለከለ።

ስለ ሊኩዋንይው የምሰማቸውታሪኮች ሰላስደነቁኝ ስለሱ የበለጠ ለማወቅ መጻሕፍት ማንበብ ጀመርኩ። የእንግሊዝ ቅኝ ግዛት የነበረችን ደሀ ደሴት በሠላሳ ዓመት ውስጥ በተዓምር ቀይሮ ካደጉት ሀገራት ተርታ እንዳሰለፋት ተረዳሁ። አኔ ሲንጋፖር ሰደርስ ሥልጣኑን ለቆ ስለነበር በቴሌቭዥን የሚተለለፍ ንግግሩን፣ በትምህርት ተቋማት እናየሕዝብ መሰብሰቢያ አዳራሽ የሚሰጠውን ትምህርት (lecture) በመካፈል ብዙ ነገር ተማርኩ። «ሲንጋፖር ሊ ኩዋን ይው የሠራት ተዓምር ናት› ቢባል ከእውነት የራቀ አይሆንም።

ሀገሪቷ ትንሽዬ ደሴት ብትሆንም በምጣኔ ሀብት ዕድገት ግን በመጀመሪያው ደረጃ ላይ ከሚገኙ የዓለም ሀገሮች ተርታ ትመደባለች። ይህንን ፈጣን ዕድገት ከማሰመዝገቧ በፊት ግን ብዙ ውጣ ውረድ ውስጥ አልፋለች። በድሮ ዘመን የማላይ ሕዝቦች ዓሣ የሚያጠምዱባትደሴት፡ አቀማመጧ ለውኃ ላይ ንግድ አመቺ ስለሆነ የአንግሊዝ ቅኝ ገዢዎች እ.አ.አ በ1819 ተቆጣጥረዋት ትልቅ የጦር እናየንግድ ወደብ ጣቢያ አደረጓት። ወደቡ ላይ የሚያገለግሉ ሠራተኞችን ደግሞ ከቻይና ያመጡ ነበር። አቀማመጧ ለአጎራባች ሀገሮች አምብርት ስለሆነች የወደብ አገልግሎቱ ተሰፋፍቶ የቀጠናው ዋና የንግድ ማዕከል ሆነች።

በሁለተኛው የዓለም ጦርነት ወቅት ጃፓን ለአጭር ጊዜ ተቆጣጥራ ካሰተዳደረቻት በኋላ እንግሊዝ ተመልሳ በመቆጣጠር የፓሲፊክ የጦር ወደብ አድርጋ ቀጠለችበት። በሂደት የሲንጋፖር ነዋሪዎች አብዛኞቹ የቻይና ዝርያ ቢሆኑም አንግሊዝ የታላቋ ማሌዥያ ቅኝ ግዛት አካል አድርጋ ሰታሥተዳድራት ቆይታለች። እ.አ.አ በ1939 ማሌዥያ ነጻነቷን ሰትጎናጸፍ ችግሮች ተፈጠሩ። ነጻይቷ ማሌዥያ በሀገሬው የማላይ ብሔር እና ከቻይና መጥተው በሰፈሩት መካከል በተፈጠረ ውጥረት ትታመስ ጀመር። በትልቋ ማሌዥያ (mainland) የቻይና

ዝርያ ያላቸው በቁጥር ብዙ ሰለሆኑ በሲንጋፖር ያሉት ከተጨመሩ ከሀገሬው (Native Malay) ጋር በቁጥር ሊመጣጠኑ ሆነ። የሲንጋፖር ቻይኖች መሪ ሊ ኩዋን ይው በሁለቱ ጎራ ያሉ ቻይኖችን በማሰተባበር ያሳየው ችሎታ ሲጨመርበት በማላይ ብሔርተኞች ለተቋቋመው የማሌዥያ መንግሥት አስፈሪ ሆነበት። አንዲሁም የማሌዥያ እናየሲንጋፖር ቻይኖች አንድ ለይ ከተጣመሩ፣ የማላይ ብሔርን አብላጫ (majority) ኃይል ያሳንሳል። ይሀ ደግሞ በታሪክ፣ በባሕል እናበፖለቲካ ለተገፋው የማላይ ሕዝብ የሀገር ባለቤትነት ዓላማውን ለማሳካት አንቅፋት እንደሚሆን ተገነዘቡ።

የቻይኖቹን ቁጥር ለመቀነስ በማሰብ ሲንጋፖርን ከዋናዋ ማሌዥያ አንድትgነጠል ገፏት። ሲንጋፖር ኦገስት 9 ቀን 1965 በዓለም ላይ ያለፍቃዷ ነጻነትን የተጎናጸፈች ሀገር ሆነች። የፖለቲካ ነጻነት የተጎናጸፈችዋን ሲንጋፖር በኢኮኖሚ እራሷን ማስቻል ከባድ ፈተና ደቀነ። ደሴቷ በባሕር በመከበቧ ለወደብ አገልግሎት አመቺ ቢያደርጋትም ከዚያ ያለፈ የተፈጥሮ ሀብት አልነበራትም። ለአርሻ የተመቸ መሬትም ሆነ ማዕድን ሰላልነበራት፣ አብዛኛው ሕዝብ የሚኖረው ከአንግሊዝ የጦር ሰፈሮች አገልግሎት በሚያገኘው ገቢ ነው።

ሲንጋፖር ነጻነቷን እንደተቀዳጀች አንግሊዝ የጦር ካምፓን ለቃ ለመውጣት ወሰነች። ይህ የሕዝቡን ዋና የገቢ ምንጭ በማድረቅ ከፍተኛ አደጋ ጋረጠ። ፈጣሪ ሲረዳቸው ሊ ኩዋን ይው የተባለ ጠንካራ መሪ ሰጣቸውና ከተጋረጠባቸው የኢኮኖሚ ውድቀት መትረፍ ብቻ ሳይሆን በፍጥነት አንዲመነደጉም ረዳቸው። ሊ ኩዋን ይው እንግሊዝ በሚገኘው ታዋቂው የካምብሪጅ ዩኒቨርሲቲ የተማረ የሕግ ባለሙያ ሲሆን፣ ማሌዥያ ከቅን ግዛት ወጥታ ሲንጋፖር ነጻ ሀገር እንድትሆን ሲወሰን ጠቅላይ ሚኒስትር በመሆን ተመረጠ። ገና ሥልጣን እንደያዘ የሲንጋፖርን መፃዒ ዕድል ሊቀይሩ የሚችሉ ወሳኝ ሐሳቦችን በማፍለቅ በፍጥነት ተገበረ።

ሲንጋፖር ብዙ የተፈጥሮ ሀብት የሌላት እናየገቢ ምንጯም በሀገሪቱ በሰፈረው የአንግሊዝ ጦር ለይ ጥገኛ ስለነበረ፣ ይህ ጦር ሲለቅ ሊያጋጥማት የሚችለውን የኢኮኖሚ እናየደኅንነት አደጋ ቀልብሶ ለማደግ የምትችለው በሁለት መሠረታዊ ነገሮች ነው ብሎ አሰበ። የመጀመሪያው የሀገሪቷን ሰለም በማረጋገጥ የአካባቢው የኢንቨስትመንት ማዕከል ማድረግ ሲሆን፤ ሁለተኛው ደግሞ እንደሌሎች ሀገራት ኢንቨሰትመንት ለመሳብ የሚሰያችል የተፈጥሮ ሀብት ስለሌላት ያላት አማራጭ ጠንካራ ሙያ እናሥነ-ምግባር ያለው የሠራተኛ ኃይል መፍጠር ነበር። አሳቤው በጠንካራ ሥነ-ምግባር የታነጸ እናብቃት ያለው ሠራተኛ ካለ በአቅራቢያው ከሉ ሀገራት የበለጠ ኢንቨሰትመንት መሳብ ይቻላል የሚል ነው። በተጨማሪም ሕጎች እናአሠራሮችን የኢንቨስትመንት ሥራን ሊያቀላጥፉ በሚችሉ መልኩ በመቅረጽ የሀገሪቷን ተወዳዳሪነት የበለጠ ማጠናከር ይቻላል በማለት አቅድ ነድፎ ወደ ሥራ ገባ።

በወቅቱ በሀገሪቷ ሰላም ላይ ሁለት ነገሮች አደጋ ይጋርጣሉ ተብሎ ይታሰብ ነበር። የመጀመሪያው ኮሚኒዝም ሲሆን፣ ሁለተኛው የብሔሮች ብዝኀነትና ግጭት ነው። ዘመኑ ኮሚኒዝም በአካባቢው ሀገራት ብሎም በዓለም ላይ እንደ ሰደድ እሳት የተሰፋፋበት ስለነበር፣ አብዛኞቹ የሲንጋፖር ዜጎች ቻይናውያን ከመሆናቸው ጋር፣ ቻይና ለምትተዳደርበት የኮሚኒዝም ሥርዓት ሊጋለጡ ይችላሉ የሚል ሥጋት ነበር። እንደተፈራውም የኮሚኒሰት ፓርቲ ሲንጋፖር ውስጥ ተቋቁሞ ከፍተኛ ድጋፍ አያገኘ መጣ። ሊ ኩዋን በኮሚኒሰት ኃይሎች የተጋረጠውን አደጋ ጎረቤቷ ኢንዶኔዥያ አንዳረገችው በኃይል ለማጥፋት መሞከር አደጋ እንዳለው ሰለገመተ፣ የተሻለውአማራጭ ሕዝቡ በኮሚኒዝም ፖለቲካ የሚሳብበትን ምክንያት መቅረፍ ላይ ሆነ። ለዚሀም ሥራ አጥነት እናየመደብ ልዩነት (በሀብታም እናበደሀ መካከል ያለውን የኑሮ መበላለጥ)

ችግርን ለመግታት ቅድሚያ እንዲሰጠው በየነ። ኢንቨስትመንትን በስፋት በመሳብ ሥራ አጥነት እንዲቀንስ እንዲሁም ሠራተኞች የተሻለ ክፍያ አግኝተው ሙያዊ ብቃታቸውን ከጊዜወደጊዜ በሥልጠና እንዲያሳድጉ ወሰነ።

ካፒታሊዝምን የኢኮኖሚ ፖሊሲ አድርጎ ቢጠቀምም የገቢ ልዩነት (income disparity) እንዳይሰፋ መንግሥት ኢኮኖሚውን ለመቆጣጠር ያለው ድርሻ ጠንካራ እንዲሆን አደረገ። ለፖለቲካ ሥልጣንም ሆነ ለልማት ድርጅት አመራርነት ችሎታ (meritocracy) በብቸኛ ሰፈርትነት ተወሰደ። መስፈርቱን ራሱ በሚሾማቸው ሚኒስትሮች ላይ በመተግበር ምሳሌ ሆነ። የመደብ ልዩነት ሳይሰፋ እና ሥራ አጥነትን በመቀነስ የሠራተኛውን ገቢ የሚጨምር ፈጣን የኢኮኖሚ ዕድገት ማስመገብ ከተቻለ ለኮሚኒዝም በር የሚከፍት የሠራተኛው እና የደሀው ሰሞታ እና በደል አይኖርም በሚል እሳቤ ተንቀሳቀሰ።

ሁለተኛው የሰላም አጦት ምንጭ በብሔሮች መካከል ያለ ግኙኝነት ሊሆን  እንደሚችል ሊኩዋን ይው ገና በጠዋቱ አስተዋለ። ይህን አደጋ ለመቀልበስ የብሔሮች የቅሬታ እናየኩርፊያ ምክንያት ሊሆኑ የሚችሉትን ጉዳዮች ከመጀመሪያው መፍትሔ አበጀለቸው። በወቅቱ በሀገሪቱ የነበሩት ሦስት ብሔሮች ቻይና፣ ማላይ እናሕንዶች ናቸው። ሦሰቱ ብሔሮች የሚናገሩት ቋንቋዎች፣ ማለትም ማላይ፣ ቻይና እናታሚል (አዚያ ያሉ ሕንዶች የሚናገሩት) አኩል ኦፊሴላዊ እንዲሆኑ ወሰነ። በቅኝ ግዛት ምክንያት ሁሉም ብሔሮች እንግሊዝኛን ስለሚናገሩ፡ የጋራ ቋንቋ እንዲኖራቸው እና የሀገሪቷ ዜጎች በዓለም ገበያ ውስጥ ተወዳዳሪ እንዲሆኑ ታሰቦ እንግሊዝኛ ሁለገብ የሥራ እና የትምህርት ቋንቋ ተደረገ። ቤተሰብ ከራሱ ቋንቋ በተጨማሪ ልጆቹን እንግሊዝኛ እና ሌላ የመረጠውን ቋንቋ የማስተማር መብት ተሰጠው።

ለነባሮቹ ሕዝቦች (native) እውቅና ለመስጠት ማላይ የሀገሪቷ ብሔራዊ ቋንቋ እንዲሆን በሕገ-መንግሥት ተደነገገ። የሊ ኩዋን ይው ወገኖች (ቻይኖች) ከሀገሪቷ ሕዝብ 75% ሆነው እያሉ፡ 14% ብቻ የሆኑትን የማላዮችን ቋንቋ ብሔራዊ ቋንቋ እንዲሆን መወሰኑ ብስለት እና አርቆ አሳቢነቱን ያሳያል። ይህ ውሳኔ ትልቋ ማሌዥያ የማላይ ብሔርተኝነትን በመቆስቆስ በሲንጋፖር የውስጥ ጉዳይ አጇን እንዳታስገባ ለማስቆም እናቀዳዳ ለመድፈን ታስቦ ነው።

በሀገሪቷ ውስጥ ችግር ሊፈጥሩ የሚችሉ ቁልፍ ጥያቄዎች ከላይ በተጠቀሰው መልኩ ከመፈንዳታቸው በፊት መልስ በመስጠት፣ የመደብ እናየብሔር ቅሬታ እንዳይፈጠር በማድረግ የብጥብጥን ምንጭ አሰቀድሞ ማድረቅ ተቻለ። ሲንጋፖር ከአካባቢው ሁሉ ሰላሟ የተረጋገጠ መሆኗ የአሜሪካ፣ የአውሮፓ እናየጃፓን ትልልቅ ኢንቨሰትመንቶችን በአጭር ጊዜ ውስጥ እንድትስብ ረዳት።

ሊ ኩዋን ይው ሲንጋፖር እ.አ.አ በ1959 ራሰ-ገዝ ሰትሆን ሥልጣን ይዞ፣ ከ30 አመታት በኋላ በ1990 ለቀቀ። በራሱ ብቃት እናአሱ መልምሎ ባሰማራቸው መሪዎች ጠንካራ አመራር ለቀን ጉርሷ እንኳን በእንግሊዝ የጦር ወደብ ላይ ጥገኛ የነበረች፣ ማሌዥያ አልፈልግሽም ብላ ያባረረቻትን ትንሽዬ ደሴት፣ በሠላሳ ዓመታት ውስጥ ከበለጸጉ ሀገራት ምድብ አሰለፋት።

ሲንጋፖር በኖርኩበት ጊዜ የሥራ ሥነ-ምግባራቸው፣ የሀብት አጠቃቀማቸው እናቁጠባቸው በጣም ያስሰገርመኝ ነበር። ለምሳሌ ጡረታ የወጡ ሰዎች  እንደሌላው ሀገር አያርፉም፡ የተገኘውን ሥራ በሙሉ ይሠራሉ። የትልቅ ኩባንያ ሥራ አስኪያጅ (CEO) የነበረ ወይምያጦር ኃይል የመራ ኮሎኔል ጡረታቸው ሲደርሰ ከማረፍ ይልቅ ታክሲ ሲነዱ ማየት የተለመደ ነው።

ያቺን ሀገር እንዳደንቃት ያደረገኝ ሌላው ነገር የውኃ አጠቃቀማቸው ነው። ሲንጋፖር ትንሽ ደሴት ስለሆነች ለመጠጥ የሚሆን ወንዝ ሰለሌላት የመጠጥ ውኃ የምታስገባው ከጎረቤት ሀገር ነው። ይሀንን ጥገኝነት ለመቀነስ ዝናብ ሲዘንብ ከየቦታው በቱቦ በአንድ ማዕከል ተጠራቅሞ ከተጣራ በኋለ ለመጠጥ እናምግብ ለማብሰል ጥቅም ላይ ይውላል። በየቤቱ ለፅዳት የሚውልውኃ እንደሌላው ሀገር አይወገድም፤ ከተጠራቀመ በኃላ በዘመናዊ ቴክኖሎጂ ተጣርቶ ለመጠጥ እና ሌሎች አገልግሎቶች ይውለል። ደረቅ ቆሻሻም አይጣልም፤ ተሰብሰቦ ተቃጥሎ ለኤሌክትሪክ ኃይል ምንጭነት፣ የሚቀረው አመድም የተለያየ አገልግሎት ይሰጣል።

በነበረኝ ቆይታ አንድም ቀን ትራፊክ ፖሊስ መንገድ ላይ ቆሞ አላየሁም። ሕግ የተላለፈ ተሽከርካሪ ካለ ካሜራው መዝግቦ የቅጣት ደረሰኝ ቤቱ ድረሰ ይላክለታል። ፖሊሰ የለም ብሎ ሕግ የሚተለለፍ ሰው የለም። ለምሳሌ ከእኛ ጋር የሚማሩ ሴቶች ማታ ጠጥተው ሰክረው ወደ ዶርም ሲመለሱ ያመጣቸው የታክሲ ሹፌር ግቢ አድርሷቸው ት/ቤቱን ያስከፍላል እንጂ በርሳቸውን አይከፍትም። ሲንጋፖር ከነጻነት በኋላ ያሳየችው ማኅበራዊ እናኢኮኖሚያዊ ለውጦች፣ እውቀት፣ ቁርጠኝነትና የሀገር ፍቅርን አመዛዝኖ የያዘ የፖለቲካ አመራር ማግኘት ምን ያሀል ወሳኝ እንደሆነ እንድገነዘብ አድርጎኛል።

# 4.5.የየናዩይትድ ዎርልድ ኮሌጅ ተማሪ

ሲንጋፖር በሰኮላርሺፕ ሰሄድ ሰዎች ለጉብኝት እና ለሥራ የሚጎርፉበት ሀብታም ሀገር ነበረች። እኔን ጨምሮ ከመቶ በላይ ሀገራት ከተመረጡ መቶ ሠላሳ (130) ተማሪዎች ጋር ትምህርት ጀመርን።ትምህርት ቤቱ ዩናይትድ ዎርልድ ኮሌጅ ኦፍ ሳውዝኢሰት ኤዥያ (United World College of Southeast Asia) ይባላል። በወቅቱ በተለያዩ ሀገራት የሁለተኛ ደረጃ ት/ ቤት የነበረው ዩናይትድ ዎርልድ ኮሌጅ ድርጅት ቅርንጫፍ ነው። ዩናይትድ ዎርልድ ኮሌጅ አ.አ.አ በ1962 ከርት ሀን (Kurt Hahn) በተባለ የትምህርት ምሁር ተቋቋመ። ሰውዬው ትምህርት ለዓለም ብሔሮች እና ሀገራት የአንድነት እናየሰላም ምንጭ መሆን አለበት ከሚል ሐሳብ በመነሳት እንቅስቃሴውን ጀመረ። ከርት ሀን የአይሁድ ዝርያ ያለው ጀርመናዊ ሲሆን፣ ሁለተኛው የዓለም ጦርነት ካሰከተለው ጥፋት ቀጥተኛ ልምድ ነበረው። ሀገራት እናብሔሮች መካከል የሚነሳ ውዝግብ እናጥላቻን ለማሰቀረት እንዲሁም ሌላ የዓለም ጦርነት እንዳይፈነዳ ለማድረግ ትምህርት ላይ ማተኮር እንደሚገባ አመነ። ትምህርት የጋራ መግባባት፣ የመከባበር እና የመቻቻል ምንጭ እንዲሆን ከተለያየ ባሕል እናሀገራት የተውጣጡ ወጣቶችን አንድ ላይ ማሰተማር አሰፈላጊ ነው ብሎም ወሰነ።

ከ16-19 ያለው ዕድሜ የወጣቶች ፀባይ እናባሕርይ የሚቀረጽበት (formative age) ስለሆነ ከተለያየ ባሕል፣ አምነት እናሀገራት ሰብስቦ አንድ ላይ ማገናኘት ከሁሉም ጎራ መግባባትን ለመፍጠር ይጠቅማል በሚል ከሁለተኛ ደረጃ የመጨረሻ ክፍሎች ማስተማርን መረጠ። በዚሁ አቅድ መሠረት የመጀመሪያውን ት/ቤት በዌልስ፤ እንግሊዝ ውስጥ ዩ.ደብሊው.ሲ አድሪያቲክ (UWC Adriatic) የሚባል ትምህርት ቤት ከፈተ። የት/ቤቱውጤታማነት በፍጥነት ሰለታየ በለጋሾች እናበመንግሥት ባለሥልጣናት ድጋፍ ከአውሮፓ ውጪ በመስፋፋት እኔ የሄድኩበት ኮሌጅ እ.አ.አ በ1971 ሥራ ጀመረ።

በሄድኩበት ወቅት ዓለም ላይ ታዋቂ ከሆኑ የሁለተኛ ደረጃ ት/ቤቶች መካከል በመጀመሪያው ረድፍ ላይ ይገኛል። ሲንጋፖር በነበርኩበት ጊዜ አሥር የUWC ት/ቤቶች በተለያዩ ሀገራት ተከፍተው የመማር ማሰተማር አገልግሎት ይሰጡ ነበር። ይህ መጽሐፍ አሰኪጻፍ ድረስ የት/ ቤቶቹ ብዛት አሥራ ሰምንት ደርሷል። በዚሀ የሰኮላርሺፕ ዕድል ከኢትዮጵያ የሄዱ ተማሪዎች በመቶዎች ይቆጠራሉ። በእኛ ባች 5 ተማሪዎች ተመርጠን ወደተለያዩ ሀገራት ተላለክን።

ትምህርት እንደጀመርኩ በጣም ከበደኝ። ሀገር ቤት እስከ አሥራ እንደኛ ክፍል ስማር በፈተና ጥሩ ውጤት የማመጣ ጎበዝ ተማሪ ብሆንም የሄድኩበት ትምህርት ቤት ለሚከተለው የማሰተማር ደረጃ ዝግጁ አልነበርኩም። የሀገራችን የቋንቋ ትምህርት ሰዋሰው ላይ ሰለሚያተኩር የማንበብ እና የመጻፍ ችሎታን ለማዳበር አይረዳም። ለእንግሊዝኛ ብቻ ሳይሆን ለአፋን ኦሮሞ እና ለአማርኛ የጽሑፍ ችሎታም ተገቢው ትኩረት አይሰጥም። የሚሰጠን የቤት ሥራም ሆነ ፈተና እውነት/ሐሰት፣ ምርጫ፣ እና ባዶ ቦታ መሙላት እንጂ አንድ ገጽ እንኳንአንድንጽፍ የተጠየቅንበትን ፈተና አላሰታውሰም።

ሲንጋፖር ሰሄድ ሰድስት የትምህርት ዓይነቶችን እየተማርኩ፡ በሳምንት ለአያንዳንዱ ጽሑፍ ከሁለት እስከ አራት ምዕራፍ ማንበብ እናከሁለት እስከ ሦስት ገጽ አርትዖት በእንግሊዝኛ ለመጻፍ ተገድድኩ። ኢትዮጵያ እያለሁ አውነት/ሐሰት፣ ምርጫ እና ባዶ ቦታ ሙላ ለሚለው ፈተና ብዙም ሳለጠና እናሳልጨነቅ ከፍተኛ ነጥብ አመጣ ነበር። አሁን ግን ሀገር ቤት አያለሁ ሴሚስተሩን ሙሉ አንብቤ የማላውቀውን ጽሑፍ በሳምንት መጨረሰ ግዴታ ሆነብኝ። በፊት አንድ ገጽ አንኳን ለመጻፍ ያልተገደድኩት ሰው ለአያንዳንዱ የትምህርት ዓይነት በሳምንት ከ2-3 ገጽ ጽሑፍ ማዘጋጀት መደበኛ የቤት ሥራዩ ሆነ።

ከሌለ ሀገር የመጡ አብዛኛቹ ተማሪዎች አሁን እንደተናኘንበት ት/ቤት ማንበብ እና መጻፍ ከታችኛው የክፍል ደረጃ ጀምሮ የሥርዓተ-ትምህርታቸው አካል ስለሆነ፡ የአሁኑ ክሰተት አዲስ ስላልሆነባቸው አልከበዳቸውም። ራሴን ከአነሱ ጋር ሳነጻጽር የበታችነት ተሰማኝ፣ ፍርሀት ወረሰኝ። ያለኝ አማራጭ ወድቄ ሴሚሰተሩ መጨረሻ ላይ መባረር ወይም ጥርሴን ነክሼ ማለፍ ነበር። አህያ ከፍርሀቷ የተነሳ ጅብን ነክሳ እንደማትለቀው ሁሉ፡ አኔም አማላዩን የወጣትነት ማኅበራዊ ሕይወት እናየመዝናናት አምሮት ባላየ ባልሰማ ትቼ ጥናቴን የሙጥኝ አልኩ።

ሕይወቴ ቤተ-መጻሕፍት፣ ክፍል እናመኝታ ቤት ሆነ። ከአስተማሪዎች ጋር ቶሎ በመቀራረብ፣ የገጠመኝን ችግር በግልጽ አሰረድቼቹ ከትምህርት ሰዓት ውጪ አንዲያግዙኝ ተማጸንኳቸው። በዚህ ሁኔታ የመጀመሪያው ሴሚስተር ሲጠናቀቅ፣ የዚያን ሴሚሰተር ብቻ ሳይሆን የቀጣዩንም አንብቤ አዳረስኩ። ፈተናም ቀድሞ እንደፈራሁት ሳይሆን በጥሩ ውጤት ሰላለፍኩ፡ የራስ መተማመኔ ጨመረና ከጓደኛቼ ጋር ወጥቼ መዝናናት ጀመርኩ።

በ እንደኛው ሴሚሰተር በፍርሀት የተነሳ ጠንክሬ ተምሬ ጥሩ ውጤት ሰሳሰመዘገብኩ፣ በሁለተኛው ሴሚስተር በተለያዩ የት/ቤቱ እንቅስቃሴዎች ለመሳተፍ በራሰ መተማመንነአዳበርኩ። ከነዚሀም አንዱ ለተማሪዎች ፕሬዝዳንትነት በአጨነት መወዳደር ነበር። ይሀ ውድድር እንደ ፖለቲካ ምርጫ ሁሉ ሰፊ የምረጡኝ ቅሰቀሳ ይፈልጋል። ማኒፌሰቶ እና የትግበራ ስልት ማዘጋጀት እናማሳተም፣ ተማሪዎች በተሰበሰቡበት ማስተዋወቅ፣ አንዲሁም ከሌሎች አጨዎች ጋር መከራከር (debate) ይጠይቃል። እኔም የምርጫ ዘመቻ ኮሚቴ አዋቅሬ ገባሁበት። በመጨረሻ ከብዙ ተፎካካሪዎች መካከል ሁለቱ ቀረን። ከሁለት ሳምንታት ዘመቻ በኋለ ተማሪዎች አጠቃላይ ድምፅ ሰጡ። ውጤቱ ሲገለጽ መሸነፌን አወኩ። ቅሰሜ ተሰበረ። በዕለቱ በአካል አንጂ ሐሳቤ ክፍል ውስጥ አልነበረም። በዘመቻው እናበክርክሩ ወቅት የሰራኋቸውን ሰሕተቶች አሰታውሼ ተፀፀትኩ። ምናልባት የቋንቋ ችሎታዬ ጎድቶኝ ይሆን ብዬ ለራሴ ምክንያት ለመሰጠት ሞከርኩ። በማግስቱ ተኝቼ ሰነቃ ለቀቀኝ። በሠራኋቸው ሰሕተቶች ተፅፀዕቼ እናለሸንፈቴ አስተዋጽዖ ያደረጉ ምክንያቶችን ዘርዝሬ፡ ከእኔ ጋር በተወዳደረው ልጅ ተበልጬ መሸነፌን አመንኩ። የእንኳን ደሰ አለህ ደብዳቤም ጻፍኩለት። ክሰተቱ ለመጀመሪያ ጊዜ የተሸነፍኩበት ውድድር ስለነበር፣ መጀመሪያ ላይ ሞራሌ ቢነካም፣ ሽንፈትን አንዴት መቋቋም እንደምችል (coping with defeat) ለመማር ዕድል ሰጠኝ።

እንደ UWC ካሪኩለም ከምንማረው ውስጥ አንዱ ሥነ-ጽሑፍ (literature) ነበር። አንግሊዝኛ የአፍ መፍቻቸው የሆነ ወይም ችሎታቸው ከፍተኛ ደረጃ ላይ የሚገኝ ተማሪዎች ሥነ-ጽሑፍን በእንግሊዝኛ ይማራሉ። የተቀረነው ደግሞ በአፍ መፍቻ ቋንቋችን መማር አንችላለን። ሥነ-ጽሑፍን በአፍ መፍቻ ቋንቋ የመማር ዕድል አንዳለ አውቄ በደሰታ አፋን ኦሮሞ ለመመዝገብ ሰሄድ «አውቅና ያለው አማርኛ ብቻ ነው› አሉኝ። የእፍ መፍቻ ቋንቋ

አስተባባሪ ጋር ሄጄ ሳነጋግረው «ከሀገርህ የአፍ መፍቻ ቋንቋህ አማርኛ ተብሎ ሰለተላከልን የተዘጋጀነው ለአማርኛ ነው። አማርኛ በደንብ እንደምትችል እና የፈተና ውጤትህም A እንደሆነ ይዘህ ከመጣኸው የትምህርት ማስረጃ አይቻለሁ። ለምን አሱኑ አትማርም?'» አለኝ።

አማርኛ ብችልም የአፍ መፍቻዬ አፋን ኦሮሞ እንደሆነ፣ ቋንቋው ለረጅም ዓመታት ተጨቁኖ ከትምህርትና ከሥራ መታገዱን በመግለጽ፣ በቋንቋዬ መማር ለአውቀት ብቻ ሳይሆን ያሳደገኝ ሕዝብ ትግል አካል መሆኑን ነገርኩት። አሱም «ከትምህርት ቤቱ አሥተዳደር ጋር ተወያይቼ መልሰ አሰጥኸለሁ» አለኝ። በማግሰቱ አሰጠርቶኝ «አስካሁን በምናሰተምረው የትምህርት ሥርዓት ውስጥ አፋን ኦሮሞ አልገባም። ከሀገርሀ የመጡ ተማሪዎች የሚማሩት አማርኛ ቢሆንም አዲሰ ቋንቋ መጨመር የሚከለክል ሕግ ግን የለም። ሰለዚሀ መጻሕፍት በፍጥነት ማግኘት የምትችል ከሆነ አቅድ አውጥተን መማር ትችላለሀ» አለኝ።

የሚያስፈልጉትን መጻሕፍት ይዘት ካሰረዳኝ በኋላ በአሰቸኳይ በምን መልኩ ማግኘት እንደሚቻል ተወያየን። አፋን ኦሮሞ የሚያሰተምሩ ዩኒቨርሲቲዎች ሰለመኖራቸው ሲጠይቀኝ ጅማ፣ ሐረማያ እናአዲሰ አበባ እንደሚያስተምሩ ስነግረው ት/ቤቱ ደብዳቤ አዘጋጅቶ ለዩኒቨርሲቲዎቹ እና ለኦሮሚያ ትምህርት ቢሮ ጻፈ። የተጻፈለቸው አካላት ግን ምላሽ አልሰጡም። ለአዲስ አበባ ዩኒቨርሲቲ የቋንቋዎች ዲፓርትመንት በቀጥታ ተደውሎ ሲጠየቁ ያገኙት ሰው አፋን ኦሮሞ የ«ጎሳ» ቋንቋ (tribal language) እንደሆነ እናበሥነ- ጽሑፍ ደረጃ እንደሌለ ነገራቸው።

ከዚሀ በኋላ መጻሕፍቱን ከቻልኩ በግሌ አንድፈልግ ተነግሮኝ ሀገር ቤት ባሉ አስተማሪዎቼ እና ንደኞቼ በኩል አፈላልጌ ተሰካልኝ። በወቅቱ ገበያ ላይ የነበሩ የአፋን ኦሮሞ መጻሕፍት ጥቂት ከመሆናቸውም ባሻገር፤ ት/ቤቱ ያሰቀመጠውን መስፈርት የሚያሟሉት በጣት የሚቆጠሩ ናቸው። በዚሁ መሠረት ከደረሱኝ መካከል ዳባ ወቆሳ፣ አሰፋ ዲባባ፣ ጋዲሳ ብሩ በመሳሰሉ ደራሲያን የተጻፉትን የአፋን ኦሮሞ ሥነ-ጽሑፍ መማር ጀመርኩ። ሰንማርበት የነበረበት ሁኔታ «self-taught» (ራሰን በራሰ ማሰተማር) የሚባል እናከማውቀው የቋንቋ ትምህርት የተለየ ነው። በተለያዩ የአፍ መፍቻ ቋንቋዎች ሥነ-ጽሑፍ ለመማር የተመዘገቡ ብዙ ተማሪዎች በአንድ ክፍል ይማራሉ፤ መምህራኑ በአንግሊዘኛ ሰለ ሥነ-ጽሑፍ ያስተምሩናል።

ዓለም ላይ ታዋቂ ከሆኑ የሥነ-ጽሑፍ መጻሕፍት መካከል እንደ Things Fall Apart (Chinua Achebe) እናMetamorphosis (Franz Kafka) ላይ በመመሥረት ያሰተምሩናል። በተማርነው ላይ ተመርኩዘን በራሳችን ቋንቋ የተጻፉትን አየተነተንን እንመዝናለን። የትንታኔ እናየምዘናው ጽሑፍ (analysis and review) አንድ ላይ ተሰብሰቦ የማናውቃቸው ፈታኞች (anonymous examiners) ጋር ተልኮ ተገምግሞ፣ ኮteቾት፣ ኮምክር እና ከውጤት ጋር ይመጣልናል። በሁለቱ ዓመታት መጠናቀቂያ ላይ የመዝጊያ ፈተና (final exam) ተዘጋጅቶ ይመጣና የእኛ መልስ አሁንም ለፈታኞቹ ተልኮ ተገምግሞ ውጤቱ ይላካል።

ት/ቤቱ "International Baccalaureate (IB)" የተባለ ሥርዓተ-ትምህርት ይጠቀም ነበር። በወቅቱ የIB ካሪኩለም ውስጥ ሥነ-ጽሑፍ በ190 ቋንቋዎች እንደሚሰጥ ይነገር ስለነበር፣ እኔ አፋን ኦሮሞ አስጨምሬበት 191 አደረሰኩት። ይኸም በሕይወቴ ውስጥ በአልህ ፈጽሜ ካሳካሁትና ከምኮራበት ትግል አንዱ ነው።

ሲንጋፖር መሄዴ መደበኛ ትምህርትን ጨምሮ የአካባቢውን እናየዓለም ሀገራትን ባሕል፣ ኢኮኖሚ እናፖለቲካዊ ሁኔታ አንድረዳ ሰፊ ዕድል ከፈተልኝ። ከመቶ በላይ ሀገራት ተውጣጥተው የተለያየ ቋንቋ፣ እሴት፣ማንነት እናባሕል ካላቸው ተማሪዎች እና አስተማሪዎች ጋር በልጅነት ዕድሜ አንድ ዶርም መኖር እና መማር የሌሎቹን ፀባይ መረዳት ብቻ ሳይሆን የራስንም ማስተካከል ይጠይቅ ነበር። ከተለያየ ባሕል የመጣን ሰዎች መጀመሪያ ሰንቀላቀል የተራራቀ ፀባይ እናባሕርይ ሰላለን ቁጥብነት ይታይብናል። ከጥቂት ጊዜ በኋላ ልዩነቱ አየጠበበ፣ የዘር፣ የሀይማኖት እናየባሕል ድንበር አየተናደ የሰዎች ፀባይ እና ባሕርይ ብቸኛው የመቀራረቢያ መሰፈርት እየሆነ ይመጣል።

## 4.6.ቸንጉርጉሯ እስያ

በአዳሪ ት/ቤት (boarding school) ከተለያዩ ሀገራት ዜጎች ከማገኘው ልምድ በተጨማሪ ደቡብ ምሥራቅ ኤሽያ (Southeast Asia) ውስጥ ወደሚገኙ ሀገራት በመጓዝ ምጣኔ ሀብታቸውን እናባሕላቸውን ለመማር እሞክር ነበር። ሲንጋፖር በእነዚህ ሀገራት መሀል ስላለች በአቅራቢያው ያሉ ብዙ ከተሞች በአጭር ርቀት ላይ ይገኛሉ። በተለይ ከመጀመሪያው ሴሚሰተር በኋላ የማገኘውን የዕረፍት ጊዜ በሙሉ ሌላ ሀገር በመጎብኘት አሳልፍ ነበር። በአካባቢው የሚገኙ ሀገራት ተመሳሳይ የመሬት አቀማመጥ፣ ተቀራራቢ ባሕል እናየተፈጥሮ ሀብት ቢኖራቸውም ውስጣዊ ፖለቲካ እናምጣኔ ሀብታቸው ሰፊ ልዩነት ነበረው። በመጀመሪያው ጉብኝቴ ይሀንን ልዩነት ሰለተገነዘብኩ ምክንያቱን ለማወቅ በተደጋጋሚ ስመለለስ ቆይቻለሁ።

ይሀን ጥያቄ ከአውሮፓ እናከአሜሪካ ለመጡ አስተማሪዎች ሳቀርብ የማገኘው መልስ «ትልቅ ምጣኔ ሀብት ያላቸው ሀገሮች የፖለቲካ ሥርዓታቸው ዴሞክራሲያዊ ሲሆን፣ ወደኋላ የቀሩት ደግሞ ከአምባገነናዊ ሥርዓት ሰላልተላቀቁ ነውን የሚል ነበር። መልሱ በተወሰነ መልኩ ትክክል ይመስላል። ለምሳሌ ማሌዥያ እናኢንዶኔዥያን ከወሰድን በብዙ ነገር ቢመሳሰሉም ማሌዥያ ለዓመታት የቆየና እየዳበረ የመጣ ዴሞክራሲያዊ ሥርዓት አላት። ምጣኔ ሀብቷም በጣም አድጓል። በተቃራኒው ጎረቤቷ ኢንዶኔዥያ ለብዙ አሥርት-ዓመታት በአምባገነናዊ ሥርዓት ሥር ታፍና ከርማ እኔ ሲንጋፖር በነበርኩበት ወቅት ወደ ዴሞክራሲ ለመሸጋገር ገና እየተፍጨረጨረች ነው። የምጣኔ ሀብት ዕድገቷም እንደ ፖለቲካዋ ቀጭጯል።

የሁለቱን ሀገሮች ሁኔታ በማነጻጸር የዴሞክራሲ ዕድገት ምጣኔ ሀብትን እንደሚያፋጥን፣ እንዲሁም አምባገነንነት ደግሞ እንደሚያቀጭጭ መረዳት እንችላለን። ነገር ግን አዚያው አካባቢ ተመሳሳይ የፖለቲካ ሥርዓት እያላቸው በምጣኔ ሀብታቸው ተቃራኒ የሆኑትን እናገኛለን። ለምሳሌ ቬትናም እናላኦስ፤ ሁለቱም በአምባገነናዊ የኮሚኒስት ፓርቲ ይተዳደራሉ። ቬትናም ምጣኔ ሀብቷ በሚያስገርም ፍጥነት አያደገ ሲሆን፣ ላኦስ ከዛሬ ሰልሳ መት በፊት የነበረችበት ላይ የቆመች የምትመስል ደሀ ሀገር ናት።

ሰለዚህ ለሀገራት የምጣኔ ሀብት መልማት እናወደኋላ መቅረት የፖለቲካ ሥርዓት መለያየት በቂ ምክንያት እንዳልሆነ ተረዳሁ። ከዚሀ በመነሳት የሀገራቱን መሪዎች ማንነት፣ የሚከተሉትን የምጣኔ ሀብት ፖሊሲ፣ በሕዝባቸው መካከል ያለውን ግንኙነት እናሌሎችንም ለመረዳት መጽሐፍ ማንበብ እንዲሁም ተመላልሼ መጎብኘትን መረጥኩ። ሲንጋፖር በቆየሁባቸው ሁለት ዓመታት ሁሉንም የደቡብ ምሥራቅ አሰያ ሀገራት ለመጎብኘት የተገኘውን ዕድል ሁሉ ተጠቀምኩበት። ከእነዚሀ ሀገራት ውስጥ ብዙ ጊዜ ተመላልሼ ያየኋቸው ማሌዥያ እና ታይለንድ ነበሩ፤ ለሲንጋፖር ሰለሚቀርቡ በትንሽ ወጪ መሄድ ይቻላል።

የሀገራቱን የውስጥ ሁኔታ ለማወቅ ባለኝ ፍላጎት ተገቢውን ፈቃድ እናወጪ ለማግኘት ትምህርት ቤቴ ከእኔ ከሚጠብቀው ከበጎ አድራጎት አገልግሎት ጋር አቀናጅቼ ሳከናውን ነበር። ለምሳሌ

ታይላንድ ውስጥ ከቤተሰቦቻቸው ታፍነው በወሲብ ንግድ (Sex Trafficking) ውስጥ የወደቁ ሕጻናትን በማዳን ላይ ከሚሠራ መንግሥታዊ ያልሆነ ድርጅት (NGO) ጋር በመሆን በበጎ አድራጎት (Volunteer) ሥራ ላይ እሳተፍ ነበር። በጉልበት ወይም በአዘዋዋሪዎችነተታለው ለወሲብ ንግድ የተዳረጉ ሕጻናትን ፖሊስ ሲያሰጥላቸው፡ እኛ ከፖሊስ ጣቢያነበማምጣት ድርጅቱ ሕጻናቱን ለማሳደግ እናለማሰተማር ወዳዘጋጀው ማቀያ (orphanage)እናደርሳለን። ማሳደጊያው በዋና ከታማዋ ባንኮክ የሚገኝ ቢሆንም፣ ሕጻናቱን ገጠር ከሚገኙ ፖሊስ ጣቢያዎች ሰለምናመጣ ሀገሪቷ ውስጥ በመዞር ማኅበራዊ ሕይወቱን፣ ምጣኔ ሀብቱን እና ፖለቲካውን ለመረዳት ጥሩ አጋጣሚ ሆነኝ።

ከሲንጋፖር በመኪና ወደተለያዩ የማሌዥያ ከተሞች መሄድ ሰለሚቻል እናየማሌዥያ ዜጎች የሆኑ ጓደኞች ሰላሉኝ በየሁለት ሳምንቱ እንሄዳለን። ማሌዥያ አንድ ሀገር ነባር ባሕል እና ማንነቱን ሳይለቅ መዘመን እንደሚችል ትልቅ ማሳያ ናት። በከተማ እናበገጠር ውስጥ ተዟዙሬ አንዳየሁት ቤት እናመኪናዎቻቸው ከአውሮፓውያኑ ጋር ተመሳሳይ ቢሆንም፣ ባሕላቸው እና ማኅበራዊ መሰተጋብራቸው የድሮ መሠረቱን አልለቀቀም።

አንዴ ከሌሎች ተማሪዎች ጋር ለመስክ ጥናት ወደ አንድ የማሌዥያ የገጠር ሰፈር ሄደን አሥቂኝ ነገር ገጠመኝ። የተቀበሉን ገበሬዎች ሙስሊም መሆናቸውን ስለተረዳሁ፣ «አሰ-ሰላሙ አለይኩም» በማለት ሰላምታ አቀረብኩላቸው። አነሱም ሰላምታዬን ከመለሱልኝ በኋላ ከየት እንደመጣሁ ጠይቀውኝ ተዋወቅን። ከዚያ በኋላ ለእኔ እና ለጓደኛቼ የሚያደርጉልን እንክብካቤ በጣም ጨመረ። ማታ ላይ የመግሪብ ሰላት ሲደርሰ ሰብሰብ ብለው እንዳሰግዳቸው ጠየቁኝ። «አይ ሽማግሌዎቹ ቢያሰግዱ ይሻላል» ብላቸውም አምቢ አሉ። በእነሱ ባሕል መሠረት አንድ ያልተጠበቀ አንግዳ ከመጣ እንዲያሰግድ ማድረግ እንደ መልካም ገድ እንደሚቆጠር ሲነግሩኝ
አጣብቂኝ ውስጥ ገባሁ።

ከዚያ በፊት ሰዎችን አሰግጄ አላውቅም። የተወሰነውን የሰላት ሥነ-ሥርዓት ባውቅም ደፍሬ ሌሎችን ለማሰገድ የሚበቃ አውቀት አልነበረኝም። ይሀን ችግሬን ለጓደኛቼ ሳሰረዳ «አንክብካቤያችንን አንዳናጣ እንደምንም ብለሀ አሰግድ» ብለው ገፋፉኝ። እኔም ፈራ- ተባ አያልኩ ከተሰለፉት ሰዎች ፊትለፊት ቆሜ አጠር አጠር አድርጌ አሰገድኳቸው። በስተመጨረሻም ዱዓውን በአፋን ኦሮሞ ሳደርግ ቅር ሳይላቸው አሚን እያሉ ተቀበሉኝ።

ማሌዥያ ነባር (native) የማላይ ብሔር እናየእንግሊዝ ቅኝ ገዢዎች ለጉልበት ሥራ አምጥተው ካሰፈሯቸው የቻይና ዝርያ ያላቸው ሕዝቦች በተጨማሪ ቁጥራቸው አነስ ያሉ ሕንዶች ይኖሩባታል። የቅኝ ግዛት ከፋፍሎ በመግዛት ሰልቱ ቻይኖቹን አሰጠግቶ ነባሮቹ ላይ መድሎ ይፈጽም ስለነበር በኢኮኖሚ ቻይኖቹ ከማላይ የበለጠ ተጠቃሚዎች ሆነዋል። ይሀ ሁኔታ ሀገሪቷ ከቅኝ ግዛት ነጻ እንደወጣች በሁለቱ ብሔሮች መካከል ብጥብጥ ፈጠረ። ማላዮች የሀገር ባለቤት እኛ ነን በማለት በፓለቲካ ያገኙትን የበላይነት ወደ ኢኮኖሚ ጥቅምም ማሸጋገር ተመኙ። ቻይኖቹ በበኩላቸው እኛም አዚሀ ከመጣን ብዙ ትውልድ ስለሆነን ከእናንተ እኩል የዜግነት መብት ሊኖረን ይገባል አሉ። ያፈሩት ንብረት ይወሰድብናል የሚል ፍርሀት ሰላደረባቸው በትጥቅ የተደገፈ አመጽ ጀመሩ። ከፍተኛ ግጭት ውስጥ ለመግባት ቋፍ ላይ የደረሰችን ሀገር የመጀመሪያው መሪዋ ቱንኩ አብዱረህማን አዳናት።

ማላዮቹ ሲደርስባቸው ከነበረ መድሎ በመነሳት የሚያነሱትን የኢኮኖሚ እኩልነት ጥያቄ

ከቻይኖቹ የንብረት ባለቤትነት መብት (property right) ጋር የሚያመጣጥን አዲስ ማኅበራዊ ውል በማውጣት፤ ማላዮች የሀገሪቷ ታሪካዊ ባለቤት (historical ownership) ፣ ቋንቋቸው ብሔራዊ ቋንቋ (national language) ፣ ሀይማኖታቸው (እስልምና) ብሔራዊ ሀይማኖት (official religion) እንዲሆን ተደረገ። ቻይኖቹ ደግሞ ሀብት የማፍራት፣ ያፈሩትን ያለመነጠቅ እንዲሁም ሀይማኖታቸውን በነጻነት የመከተል መብት እንዳላቸው አወጀ። እንግሊዝኛን የሥራ ቋንቋ በማድረግ የብሔሮች የጋራ መጠቀሚያ ሆነ።

ይህንን ተግባራዊ ለማድረግ የሁለቱ ብሔሮች የትብብር ፓርቲ (coalition) በመመሥረት፣ አመራርቹ ለራሳቸው ሥልጣን ሲሉ የሚደጋገፉበትን እናየሚቀራረቡበትን አደረጃጀት አወጣ። "Barisan Nasional" በመባል የሚታወቀው ይህ ኅብረት የሁለቱ ቡድኖች ልሂቃን የሚደራደሩበት መድረክ ሆኖ በማገልገል ከግራ እናቀኝ ያለውን ብሔርተኝነት ለማቀዝቀዝ እና የግጭት አደጋን ለመቀነስ ረዳ።

ይህ ስልት አንጻራዊ ሰላምን በማረጋገጥ ሀገሪቷ ላሳየችው የምጣኔ ሀብት ዕድገት ከፍተኛ ሚና ተጫውቷል። ቱንኩ የብሔር ግጭትን ለመቀነስ ፖለቲካዊ ብቻ ሳይሆን የምጣኔ ሀብት ስልትም አሰቀምጧል። ከላይ እንደተጠቀሰው የእንግሊዝ ቅኝ ግዛት በነባሮቹ ላይ ትልቅ መድሎ ስላደረሰ፣ በነጻነት ማግሰት አስከፊ ድህነት ውስጥ ነበሩ። በማላይ እናበቻይና መካከል ሰፊ የሊኮኖሚ መበላለጥ (disparity) ተፈጠረ። ማላዮች በሕዝብ ብዛት 70% ቢሆኑም ነጻ ሲወጡ በኢኮኖሚው ውስጥ ያላቸው ድርሻ ከ10% በታች ነበር። ትልቁ ድርሻ የተያዘው በአንግሊዝ ቅኝ ገዥዎች እናበቻይኖቹ ነበር። ይህን ለመቅረፍ ማላዮች በኢኮኖሚ ክፍፍል፣ በመንግሥት ሥራ እናበትምህርት ዕድል ልዩ ድጋፍ (affirmative action) እንዲያገኙ "bumiputra" (ባለሀገር) የሚባለው ፖሊሲ ተግባራዊ ተደረገ።

ይህ ሲሆን ግን ቻይኖች፣ እንዲሁም ሕንዶች አሰቀድመው ያፈሩት ንብረት እንዳይነካባቸው ዋስትና ተሰጣቸው። መንግሥት የቻይኖቹ እናየሕንዶቹ ንብረት ሳይነካ ማላዮችን በልዩ ጥቅም የማሳደግ ፖሊሲ ሥራ ላይ ለማዋል ሁለት ሰልቶችን ተጠቀመ። እንደኛው፡ በቅኝ ገዢዎች አጅ የነበረው ንብረት ወደ ማላይ እንዲተላለፍ ማድረግ ሲሆን፣ ሌላኛው ደግሞ፣ ኢኮኖሚውን በፍጥነት በማሳደግ አብላጫው ድርሻ ለማላይ እንዲያዘነብል በማድረግ ነበር። ብዙ ጊዜ የኢኮኖሚ አኩልነት ችግር ባለባቸው ሀገሮች እንደ መፍትሔ ሥራ ለይ የሚውለው የሀብት ክፍፍል (redistribution of wealth) ነው።

ቱንኩ ግን ከአንድ ብሔር ተቀብሎ ለሌላው መሰጠት ግጭት ይፈጥራል ብሉ ሰለሠጋ የተሻለው መፍትሔ ኢኮኖሚውን ማሳደግ ነው አለ። በዚህም «ዳቦውን ማሳደግ» (enlarging the economic pie) የሚል ሐሳብ ተጠቀመ። ሐሳቡ በጊዜው በነበረ ዳቦ ቁራሽ መጠን ላይ ከመጣላት ይልቅ የዳቦውን ሰፋት በማሳደግ ለእያንዳዱ ሰው የሚደርሰው ቁራሽ ከበፊቱ የበለጠ እንዲሆን ማድረግ ማለት ነው። መጀመሪያ ለይ እናሳ የዳቦ ቁራሽ የነበራቸው ሰዎች፣ ዳቦው ሲሰፋ የአነሱ ቁራሽ መጠንም ዕለሚያድግ የሌላውን ሰው ድርሻ መንካት ሳይጠበቅባቸው ፍላጎታቸውን ሊያሟሉ ይችላሉ። ያለውን ምጣኔ ሀብት ከማከፋፈል ይልቅ ወደፊት ኢኮኖሚውን አያሳደጉ ክፍፍሉን ማሰተካከል፣ የብሔር ግጭቶችን በመቀነሰ የትናንቱ አድሎ ያስከተለውን ጉዳት ለማከም ይጠቅማል።

ቀጥለው የመጡት መሪዎች በተለይ ለሀያ ሁለት ዓመታት ሥልጣን ላይ የቆየው ማህቴር ሙሐመድ ኢኮኖሚውን በፍጥነት በማሳደግ፣ የቱንኩን ሐሳብ እና እቅድ ሥራ ላይ ከማዋል አልፎ ብሔሮች መካከል የነበረውን የገቢ መበላለጥ ለማጥበብ ችሏል። በጥቅሉ የማሌዥያ መሪዎች የፖለቲካ እና የኢኮኖሚ ፖሊሲዎቻቸው ተመጋጋቢ እንዲሆኑ ማድረግ ችለዋል። የፖለቲካ ውሳኔዎቻቸው ግጭትን በማስወገድ ለኢኮኖሚ ዕድገት አመቺ ሁኔታን ሲፈጥሩ፣ ፈጣን እና ፍትኃዊ ክፍፍል ያለው የኢኮኖሚ ዕድገት ደግሞ የተረጋጋ ፖለቲካ እንዲኖር አስቻላቸው።

ሲሪላንካ ስሄድ የማሌዥያን ስኬት ተቃራኒ አየሁ። እንደ ማሌዥያ ሲሪላንካም ቅኝ ግዛት ሥር የነበረች ሲሆን፣ ቅኝ ገዢዎቹ በከፋፍለህ ግዛ ስልት ተጠቅመው ሲንሃላ እና ታሚል የተባሉ ሁለት የሀገሪቱን ብሔሮች አጋጭተው ሄዱ። ታሚል 12%፣ ሲንሃላ ደግሞ 75% ቢሆኑም፣ የቅኝ አገዛዙ ግን ለታሚሎች በማድላት ሲንሃላዎችን ጎድቶ ባሕልና ቋንቋቸውን ሲጨቁን እንዲሁም ከፖለቲካ ሥልጣንም ሲገፋቸው ቆይቷል። ሀገሪቷ ነጻነቷን ከተጎናጸፈች በኋላ ብዙኀን የሆኑት ሲንሃላዎች የፖለቲካ ሥልጣን ሲይዙ፣ ትላንት የደረሰባቸውን በደል በአዲስ መድሏዊ ፖሊሲ ሊቀርፉ ሞከሩ። የታሚሎችን ቋንቋ ከማገድ አንስቶ በሥራ ቅጥር ላይ ታሚሎችን በማግለል የሲንሃላዎችን የበላይነት ለማረጋገጥ ተንቀሳቀሱ። ይህ መድሏዊ ፖሊሲ የሁለቱን ብሔሮች ግንኙነት የበለጠ አሻክሮ፣ ከጊዜ በኋላ ታሚሎች ወደ ትጥቅ ትግል ለመግባት ተገደዱ። እ.አ.አ ከ1983 ጀምሮ የታሚሎች ነብር (Tamil Tigers) በተባለው ሽማቂ ቡድን እና ሲንሃላዎች በተቆጣጠሩት የሲሪላንካ መንግሥት መካከል ለዓመታት የተካሄደ ጦርነት ከፍተኛ የሕዝብ ዕልቂት እና የኢኮኖሚ ድቀት ስላስከተለ ሁለቱም ብሔሮች ለከፋ ጉዳት ተጋለጡ።

በፈረንጆቹ 2004 ሀገሪቷን ስጎበኝ ደም አፋሳሹ ጦርነት በሰላም እንዲያልቅ ዓለም ጣልቃ ገብቶ፣ ጦርነት ለጊዜው ቆሞ፣ ታሚሎች አካባቢያቸውን ተቆጣጥረው እያሥተዳደሩና የእርቅ ድርድርም እየተካሄደ ነበር። ይህንኑ የሰላም ማስፈን ሂደት ለማገዝ ከሁለቱም ወገን ወጣቶችን በማሰባሰብ እንዲወያዩ ተደረገ። እኔም ውይይቱን እንዳስተባብር ተመርጬ ወደ ሲሪላንካ ሄድኩ። በሁለቱ ብሔሮች ወጣቶች መካከል ያየሁት የእርስ በእርስ ጥላቻ እስከዚያ ጊዜ ድረስ ካየኋቸው የቡድን ኩርፊያዎች ሁሉ አስከፊው ነው። ከዚያ ጋር ሲነጻጸር በሀገራችን የሚስተዋሉ የብሔር ግጭቶች ትንንሽ ቅሬታዎች ይመስላሉ። ከሁለቱ ወገን ለሥልጠና የተመረጡ ተማሪዎችን ወደ ሲንጋፖር ስናመጣ ከመጠላላት አልፈው በአውሮፕላን ወንበር ላይ ጎን ለጎን መቀመጥ እንኳን ይጠየፉ ነበር። ወደ ሲንጋፖር ያመጣናቸውም በሁለቱ ማኅበረሰቦች መካከል ከነበረው መካረር የተነሳ ሀገራቸው ውስጥ መወያየት አስቸጋሪ በመሆኑ ነው። ከሁለት ሳምንት በኋላ ጥላቻ እና መፈራራቱ ረግቦ በመቀራረብና በሰላም ጉዳይ ድርሻቸውን እንዲወጡ ማሳመን ተቻለ።

ሲሪላንካ እያለሁ ታሚሎች የሚኖሩበትን የሀገሪቱን ክፍል ስጎበኝ በዋና ከተማቸው ጃፍና የትግላቸው መሪ ለሕዝቡ ዲስኩር ሲያደርግ አየሁ። ጠርሙስ መሰል ነገር አንገቱ ላይ አስሯል። አስተማሪያችን «አንገቱ ላይ ያሰረው ምንድነው?» ብሎ አስጎብኚያችንን ሲጠይቅ፣ ልጁም ሳይናይድ (Cyanide) እንደሆነ ነገረው።

አንገቱ ላይ ያሰረውም ድንገት ጠላት እጅ ከወደቀ በጥርሱ ነክሶ እራሱን ለማጥፋት መሆኑን በማስረዳት ሁሉም የታሚል ወታደር መርዙን አንገታቸው ላይ ማንጠልጠላቸውን ገለፀልን።
ወደዚያች ሀገር ስሄድ ጦርነት ቆሞ የሰላም እና የእርቅ ተስፋ የነበረ ቢሆንም፣ ብዙም ሳይቆይ

ግን ጦርነቱ እንደገና አገረሸ። የፖለቲካ አመራሩ ከትላንቱ ስሕተት መማር ስላቃተው፣ ሁለቱን ብሔሮች ለማቻቻል የሚያስችል የፖለቲካ ቀመር ማበጀት ባለመቻላቸው ያቺ ለምለም ሀገር ግጭት እና ድህነት ውሰጥ እንድትቀር አደረጓት።

በአጠቃላይ ሲንጋፖር በቆየሁባቸው ሁለት ዓመታት ከሰሜን ኮርያ ውጪ ያሉትን የእስያ ሀገራት ለመጎብኘት ዕድል አግኝቻለሁ። በመልከዓ-ምድራዊ አቀማመጣቸው እና በባሕላቸው ተቀራራቢነት ቢኖራቸውም ያሉበት የኢኮኖሚ ደረጃ ግን በጣም የተራራቀ ሆኖ ይታያል። ሲንጋፖር፣ ጃፓን፣ ደቡብ ኮርያ እና ሆንግ ኮንግ በፈጣን ዕድገት ወደ አንደኛው ዓለም ሲቀላቀሉ፣ ማሌዥያ፣ ሕንድ እና ቻይና እነሱ ላይ ለመድረስ በፍጥነት አየሮጡ ነበር። በተቃራኒው ደግሞ ባንግላዴሽ፣ ሲሪላንካ፣ ኔፓል እና ላኦስ አሁንም ድህነት ውስጥ እየዳከሩ ይገኛሉ። ለዚህ ልዩነት አንዱ እና ዋነኛው መንስዔ ሀገራቱ ፓለቲካቸውን በተለይ ደግሞ በሕዝቦቻቸው መካከል ያለውን ማኅበራዊ እና ኢኮኖሚያዊ ግንኙነት ሊያሥተዳድሩበት የመረጡት የፖለቲካ ሰልት እንደሆነ ተረዳሁ። ከቅኝ ግዛት ነጻ እንደወጡ የገጠሟቸው የፓለቲካ መሪዎች ብስለት እና ብቃት አንዲሁም ድክመት ትልቅ ሚና አንዳለውም መገንዘብ ቻልኩ።

ሀገሮቹን እየጎበኘሁ የስኬት እና የውድቀታቸውን መንሰዔ ሳውጠነጥን ከሀገሬ ጋር ማነጻጸሬም አልቀረም። በጊዜው የተገነዘብኩት ነገር ቢኖር በሀገራችን የሚታዩ ችግሮች በሌሎች ሀገራትም አንደሚሰተዋሉና የእነሱን ስሕተት እና ሰኬት በጥንቃቄ በማጥናት መማር ከቻልን፣ ስሕተቶቻቸውን አያረምን፣ ለዕድገት ያበቃቸውን ፖሊሲ አና ሰልት ከተላመድን የሀገራችንን ችግሮች ቀርፈን የተሳካ ዘላቂ ሰላም አና ልማት መገንባት እንደምንችል ተሰፋ መሰነቅ ጀመርኩ።

የእሰያ ሀገራትን ለማወቅ ካለኝ ጉጉት የተነሳ ሳደርግ የነበረው ጉዞ ሕይወቴን ለፍጻሜ ያቃረበ ክሰተትም ገጥሞኝ ነበር። እ.አ.አ በዲሴምበር ወር 2004 ለመሰክ ጥናት ከሌሎች ተማሪዎች ጋር ወደ ሰሜናዊቷ የታይላንድ ከተማ ቻንገማይ ተጉዘን ለቀናት ከቆየን በኋላ ወደ ዋና ከተማዋ ባንኮክ አቀናን። እቅዳችን በማግሰቱ ወደ ቱሪስት መስህብዋ የፑኬት ደሴት በመሄድ የ2003ን የፈረንጆች አዲስ ዓመት እዚያ ማሳለፍ ነበር። ሆኖም ሌሊቱን ባንኮክ ውስጥ ሰንጨፍር ስላመሸን ጠዋት ከእንቅልፍ መንቃት አቅቶን አውሮፕላን አመለጠን። ከእንቅልፍ ሰነቃ ብዙ ያመለጡ የሰልክ ጥሪዎች አየሁ። ከደዋዮቹ ለአንዱ ጓደኛዬ መልሼ ስደውል «በሕይወት አለሀ ግን» በማለት ጠየቀኝ። እኔም «ምነው ምን ሰምተህ ነው?» አልኩት። ልጁም «እንዴ የት ነው ያለኸው? እሰቲ ቴሌቪዥን ክፈት?» አለኝና ሰከፍት ሱናሚ የሚባል የባሕር ማዕበል የእስያ ሀገራትን ማጥለቅለንቁንና መአት ሰው መሞቱን ተረዳሁ።

በሱናሚው ማዕበል ክፉኛ ከወደሙት ውሰጥ እኛ ልንጓዝባት የነበረችው የፑኬት ደሴት አንዷ ስለነበረች፣ እኛም ለአደጋው የተጋለጥን ሰለመሰላቸው ነበር ብዙ ሰዎች ሲደውሉ የቆዩት። እኛ ልንጓዝበት አቅደን በነበረው በረራ ሄደው ፑኬት የደረሱ ጎብኚዎች ለአደጋው ተጋልጠው ብዙዎች ሲሞቱ፣ እኛ ግን ፈጣሪ በአንቅልፍ አሳቦ በረራውን ሰላሰመለጠን ተረፍን። በማግሰቱም ከዓለም አቀፍ የእርዳታ አሰተባባሪ ድርጅት ጋር በመሆን በሱናሚው ክፉኛ ወደ ወደመችው የኢንዶኔዥያዋ ባንዳ አቼ ከተማ በማምራት የነፍስ አድን ድጋፍ ሥራ ላይ ተሰማራሁ። እዚያም ከአንድ ቀን በፊት ሲታኮሱ የነበሩ አማጺያን አና የመንግሥት ወታደሮች በጋራ ሆነው የተጎዳውን ሕዝብ ከየፍርሰራሹ ለማውጣት ሲረባረቡ ደርሰን ተቀላቀልን። ከአንድ ዓመት በኋላ መንግሥት እና አማጺያን ለ30 ዓመታት ሲያካሄዱ የነበረውን ጦርነት በሰላም ሰምምነት ሰለቋጩት፣ ሱናሚው በአደጋ ታጅቦ የመጣ መልካም ዕድል ተብሎ ይወሳል።

## 4.7.ከተማሪነት ወደ ወጣት አመራርነት ጉዞ

በመቀጠል የወጣቶች አመራር ኮንፈረንሶች ላይ ለመሳተፍ ወደ ካናዳ እና ኔዘርላንድስ (ሆላንድ) ሄድኩኝ። የሲሪላንካ ወጣቶችን በማሰልጠን ላይ ያዳበርኩትን ልምድ መሠረት በማድረግ ወደ ካናዳ፣ ብሪቲሽ ኮሎምቢያ ግዛት ቪክቶሪያ ከተማ በማቅናት "Pearson Youth Leadership Summit (PYLS)" በተባለ የወጣቶች ሰብሰባ ላይ ተሳተፍኩ። ወጣቶቹ ከካናዳ አና ከሌሎች ሀገሮች የተውጣጡ ሲሆን፣ ሥልጠናው የወጣቶችን የአመራርነት ብቃት ለማሳደግ ያለመ ነበር። በተለይ ብዝሃነት (Diversty) ማስተናገድ በሚቻልበት ሁኔታ ላይ በንድፈ-ሐሳብ አና በተግባር የታገዘ ሥልጠና ለአንድ ወር ተሰጠን።

አጋጣሚው የሰሜን አሜሪካ ነባር ሕዝቦች የሆኑትን፣ "native" ወይም "Aborigines" በመባል የሚታወቁትን ለመጀመሪያ ጊዜ በአካል እንድመለከት ዕድል ሰጠን። የአሜሪካ እና የአውሮፓ ስደተኞች ሰሜን አሜሪካ ሲመጡ እነዚህን ሕዝቦች ከመሬታቸው በማጽዳት የተቆጣጠሩ ቢሆንም፣ እኔ ስሄድ የካናዳ መንግሥት እና ማኅበረሰብ በሕዝቡ ላይ ለተፈጸመው ታሪካዊ ወንጀል ተፀፅተው በይፋ ይቅርታ ከመጠየቅ አልፎ፣ አዲሱ ትውልድ ታሪኩን እንዲያውቀው እየጣሩ ነበር። እኛንም እስከ ቀዬአቸው በመውሰድ ታሪካቸውን እና የደረሰባቸውን በደል ከእነሱ አንደበት እንደንሰማ ሁኔታዎችን አመቻቹልን። በሕዝቦች ላይ በተከታታይ መንግሥታት የተፈጸሙ ታሪካዊ ወንጀሎችን መካድ ወይም ትክክል አድርጎ ማቅረብ ከተለመደበት ሀገር ሰለመጣሁ የካናዳ ድርጊት አጅጉን አሰገረመኝ፣ አሰደሰተኝም።

በመቀጠልም ለተመሳሳይ የወጣቶች አመራር ሥልጠና አሠልጣኝ ሆኜ ኔዘርላንድስ ሄድኩ። ሥልጠናው ለሀገሬው ወጣቶች አና ለሰደተኞች የታቀደ ነበር። በወቅቱ አውርፓ ውሰጥ በፈረንጆች፣ በጥቁሮች እና በአረብ ሰደተኞች መካከል ያለው ግንኙነት እየከረረ መጣ። በአውሮፓ ከተሞች ውሰጥ የሚገኙ ስደተኞች ከሀገሬው ነዋሪ በተገለለ ሰፈር (ghetto) መኖር ልማድ ሆነ። ወጣቶቻቸው በድህነት አድገው ለሱሰ እና ለተለያየ ወንጀል አየተጋለጡ የሥራ ዕድል ያጣሉ። ይህ ሁኔታ በነባር ፈረንጆች እና ስደተኞች ግንኙነት ላይ ውጥረት በመፍጠር የአውሮፓ ሀገራት መንግሥታትን አሰጨነቀ። እኛም ከሁለቱ ወገን ለተውጣጡ ወጣቶች ብዝኃነትን ማሰተናገድ (diversity management) ሚያሰችል ክህሎት እንዲያዳብሩ ሥልጠና ልንሰጣቸው ወደዚያ አቀናን።

ከአሠልጣኞቹ መካከል ጥቁር አኔ ብቻ ነበርኩ። የደረሰን ዕለት ሸንት ቤት ሄጄ ሰመለስ አንድ ጎልመስ ያለ የአረብ መልክ ያለው ሰው አሰቁሞ የሆነ ነገር አንዳመጣለት አዘዘኝ። እዚያ ካሉት ጥቁር የጉልበት ሠራተኞች አንዱ እንደሆንኩ ማሰቡ ገባኝና ሄጄ አመጣሁለት። ከጥቂት ሰዓታት በኋላ አዘጋጆቹ ለምሳ ስንሰበሰብ ምግብ ይዞ መጣ፣ ለካ ሰውዬው የነበርንበት የኮንፈረንሰ ማዕከል አዲስ የተቀጠረ ዋና ምግብ አዘጋጅ (ሼፍ) ነው። አዘጋጆቹ መሀል ተቀምጬ ሳወራ አይቶ በድንጋጤ ያመጣልንን ምግብ አሰቀምጦ ሄደ። ትንሽ ቆይቶ ተመለሰና ጠዋት ሰለሆነው አንድ በአንድ ተናግሮ ይቅርታ ጠየቀኝ። ክሰተቱ ዘረኝነትን ለመጀመሪያ ጊዜ በግልጽ ያየሁበት ነበር። መሰል ዘረኝነት አሜሪካ ከሄድኩ በኋላ በተደጋጋሚ አጋጥሞኛል።

ሲንጋፖር በቆየሁባቸው ሁለት ዓመታት የክፍል ትምህርት ብቻ ሳይሆን የተለያዩ ሀገሮችን በመጎብኘት ልምድ እያካበትኩ በዚህ መልኩ አሳለፍኩ። ትምህርት በሌለበት እና በማልጓዝበት የዕረፍት ጊዜ የበጎ አድራጎት ሥራ ላይ እሳተፍ ነበር። የትምህርት ሥርዓቱ ሶስት ነገሮችን ማሟላት ይጠይቃል። ፈጠራ (Creativity)፣ ድርጊት (Action) እና አገልግሎት (Service) ናቸው። ቀዳሚው ለችግርም ሆነ ማኅበረሰቡን ለሚያጋጥም አደጋ ፈጠራ የታከለበት መፍትሔ ማሳየትን አንድንለማመድ ይጠበቃል። እኔም ያጋጠመኝን ችግር ለመፍታት የሚጠበቅብኝን አሟላሁ።

ሲንጋፖር ገና እንደሄድኩ ወደ ውበት ሳሎን ሄጄ ጸጉሬን አንዲያስተካክሉልኝ ጠየኳቸው። ከእኔ በፊት ያስተካከሉላቸውን ሰዎች ፎቶ ግድግዳው ላይ ሰመለከት አንድም ጥቁር ሰው አጣሁ፡ ፈረንጆች እና እስያዎች ብቻ ናቸው። ጸጉር አስተካካዩን «የእኔን ጸጉር ማስተካከል ትችላለህ?» ስለው «አዎን አለኝ። እሺ ብዬ ቁጭ አልኩ፡ ከጨረሰ በኋላ ጸጉሬን ስመለስከተው አይጥ የሮጠበት አስመሰለው። የሀገሪቱ ጸጉር ቢቶች የጥቁር ሰው ጸጉር በትክክል ማስተካከል እንደማይችሉ ሰለተረዳሁ ማሳደጉን መረጥኩ። ከጥቂት ወራት በኋላ አፍሮዬ በጣም ሰላደገ ትልቅ ማበጠሪያ አሰፈለገኝ። ስለዚህ የሙያ ትምህርት የሚሰጥበት ዎርክሾፐ ገብቼ ማበጠሪያ ለመሥራት ባደረኩት ሙከራ፣ መልኩ ባያምርም አንድ ማበጠሪያ መሥራት ቻልኩ። ይህም ችግር ፈቺ ፈጠራ ተደርጎ ተያዘልኝ።

በአገልግሎት በኩል ደግሞ የአእምሮ ሕመምተኞች የሚኖሩበት ቦታ በሳምንት አንዴ የበጎ አገልግሎት ሥራ ላይ እሳተፍ ነበር። በሀገራችን የአእምሮ ሕመምተኞች ላይ የተዛባ ግንዛቤ ስላለ፣ መጀመሪያ አካባቢ ሥራው በጣም ከበደኝ። ሰለ አእምሮ ሕመም ምንነት ቀስ በቀስ እየተማርኩ፣ እንዲሁም ሕመምተኞች ጥሩ ክብካቤ እና እያያዝ ከተደረገላቸው ሊሻላቸው እንደሚችል አየሁ።

ሌላው የበጎ አድራጎት ሥራ ገንዘብ በማሰባሰብ ወደ ኢትዮጵያ በመላክ ችግረኞችን መርዳት ነበር። ለዚሁ ዓላማ በማሰብ የባሕል ትዕይንት አዘጋጅቼ ብዙ ሰው ተገኝቶ ዳጎሰ ያለ ገንዘብ አዋጣልን። በአዲስ አበባ በሚገኝ አንድ የተራድዖ ድርጅት አማካኝነት 15 ለሚሆኑ ሕጻናት የሦሰት ዓመት የመኖሪያ እና የመማሪያ ቁሳቁሰ መሸፈን ቻልኩ። የሁለት ዓመቱን ትምህርት ጨርሼ ወደ ሀገር ስመለስ እነዚያን ተረጂዎች በአካል አግኝቼ ድጋፉ መድረሱን አረጋገጥኩ።

ሲንጋፖር እያለሁ እዚያ የሚኖሩ ኢትዮጵያውያን ቁጥራቸው ትንሽ ነበር። በምማርበት ት/ ቤት አንድ ክፍል የሚቀድመኝ እና ኦሮሚያ ውሰጥ የተወለደ ብሔሩ ትግሬ የሆነ ተማሪ ነበር። መጅመሪያ እንደደረሰኩ ጥሩ ጓደኝነት ቢኖረንም፣ ከወራት በኃላ የኦሮሚያ ዋና ከተማ ከፊንፊኔ ወደ አዳማ በመቀየሩ ምክንያት የተማሪዎች ተቃውሞ ሲካሄድ ተቃውሟቸውን አጣጥሎ ሊሳለቅ በመሞከሩ ኃይለኛ ጥል ውስጥ ገብተን ሳንቀራረብ እሱም ተመርቆ ሄደ።

ዶክተር አሰፋ እንደሻው የተባለ ኢትዮጵያዊ የሕግ ፕሮፌሰር በአንዱ ዩኒቨርሲቲ ያሰተምር ዕለነበር ፈልጎ አገኘኝና ተዋወቅን። በ1560ዎቹ የኢትዮጵያ የተማሪዎች ንቅናቄ እንዲሁም ቀጥሎ በተመሠረቱት የፖለቲካ ድርጅቶች ውስጥ ተሳታፊ ሰለነበር፣ ስለተማሪዎች ትግል እና በዘመኑ ሰለነበሩት የኢሕአፓ፣ የመኢሶን እና የመሳሰሉ ፓርቲዎች ፖለቲካ ጥልቅ መረጃ ሰለነበረው ብዙ ጊዜ አግኝቼ አውርቼዋለሁ።

ከሁሉም በላይ የተቀራረብነው የአንድ ትልቅ ባንክ ማናጀር ሆኖ እዚያው ይሠራ ከነበረ ትውልደ ኢትዮጵያዊ የካናዳ ዜጋ ጋር ሲሆን፣ ስሙም ግዮን ሸዋንግዛው ይባላል። ከእሱ ጋር

ተዋውቀን ወዲያው ተቀራረብን። በብሔሩ አማራ፣ ሀይማኖቱ ካቶሊክ ሲሆን ትውልዱ ሐረርጌ ነው። ሲበዛ ሚዛናዊ አስተሳሰብ ያለው ሰው (Open-minded) ነው። ከሀገር ከወጣ ሦስት አሥርት-ዓመታትን ስላሰቆጠረና የሀገራችንን ሁኔታና ወቅታዊ ፖለቲካ ብዙም ስለማይከታተል ከእኔ ለመሰማት ጉጉት ነበረው። ብዙ ጊዜ ቅዳሜ ጠዋት ተኝተን በሳይክል ወደ ባሕር ዳርቻ እንሄዳለን። ወቅቱ ለ1997 ዓ.ም ምርጫ ከፍተኛ ዘመቻ የሚደረግበት ሰለነበረ ያሉኝን ወቅታዊ መረጃዎች አጠናቅሬ አካፍለዋለሁ። እሱም ባቀረብኩለት ነገር ላይ ሐሳቡን እየሰጠ ሰፊ ውይይት እና ክርክር እናደርጋለን። ከእሱ በፊት ሰለ ኦሮም ፖለቲካ ያወራኋቸው አማራዎች የእኔን አቋም እና አመለካከት ለመስማት ትዕግሥት ሰለሌላቸው የዚህ ሰው ፍላጎት እና ትዕግሥት በግልጽ እንዳወራው ጋበዘኝ። በማቀርበው ሐሰብ ባይሰማማም ያለውን ጥያቄ እና የተቃውሞ ሐሳቦች በትሕትና ያቀርባል።

አንድ ቀን አባታቸው ፓይለት የሆኑ ልጆች እሱ ጋር መጥተው አስተዋወቀን። በወሬያችን መሀል ዩኒቨርሲቲ ሰንገባ ምን ማጥናት እንደምንፈልግ ሦሰታችንንም ጠየቀን። ከሁለቱ መካከል ወንዱ ሐኪም መሆን እንደሚፈልግ ሲናገር፣ እኔ ደግሞ የፖለቲካ ትምሀርት ለመማር አሜሪካ የመሄድ ፍላጎት እንዳለኝ ነገርኩት። በዚሀ ጊዜ ልጁ «ፖለቲካ መማር ምን ይጠቅምኸል? ለምን እንደ ሰታንደርድ ያለ ዩኒቨርሲቲ የመሄድ ዕድል አግንተሀ ፖለቲካ በመማር ታባክናለህ?» አለኝ በመገረም። እኔም «አንተ ጤና ለመማር ማቀድህ ጥሩ ነገር ነው። ሀገራችን ብዙ የጤና ባለሙያ ትፈልጋለች ነገር ግን በሀገራችን ውሰጥ ላለው የጤና ጉድለትም ሆነ የማኅበረ-ኢኮኖሚያዊ ችግር ምንጩ የፖለቲካው መበለሸት እና መቀጨጭ ነው። የአንድ ሀገር ፖለቲካ ካልተሰተካከለ የጤና፣ የትምሀርት እና የምጣኔ ሀብት ፖሊሲ አይሳካም። አንተ ጤና ተምረሀ ሃምሳ ሺሀ ሰው ልታገለግል ትችላለሀ። እኔ ፖለቲካ ተምሬ የአሥተዳደር ችግር መፍታት ከቻልኩ ሃምሳ ሚሊየን ሰዎችን መርዳት እችላለሁ» አልኩት። እኔ እና ግዮን ከረጅም ጊዜ በኋላ ካናዳ ስንገናኝ ይህን ንግግር አስታወሰኝ፡ ከዚያ በኋላ የሚያውቁኝን ሰዎች ሲያገኝም ያንን ታሪክ ይነግራቸዋል። ከግዮን ጋር የመሠረትነው ወዳጅነት እና ሳምንታዊ ውይይት የኦሮሞን ትግል ዓላማ ለሌሎች ለማሰረዳት መከተል የሚገባኝን የአቀራረብ ዘዴ እንድፈትሽ እና እንዳሰተካክል አሰተምሮኛል።

ሲንጋፖር ኦሮሞ የሆነ ሰው ካለ ብዬ መፈለጌ አልቀረም። «ሲንጋፖር ወይም እዚያ አካባቢ ካላችሁ እንተዋወቅ» ብዬ በኢንተርኔት አሰራጨሁ፣ ነገር ግን ማንም አልነበረም። ከጎረቤት ሀገር ታይላንድ አድማሱ ቡልቶሳ የተባለ ሰው አለሁ አለኝ። በሰልክ ከተዋወቅን በኋላ ባንኮክ ሰሄድ እንገናኝ ነበር። ለከፍተኛ ትምሀርት ሄዶ ኑሮውን እዚያው መሥርቷል። ስለ ሀገራችን ፖለቲካ ብዙ ጊዜ ሰለምናወራ የፕሮፌሰር ሙሐመድ ሐሰን እና የፕሮፌሰር አሰፋ ጃለታን መጻሕፍት ገዝቶ ላከልኝ። በተጨማሪም ፍላጎቴን አይቶ ያኔ የኦሮሞ ልሂቃን የፓለቲካ መወያያ ድረ-ገፆች ወደሆኑት ONET እና ONA የኢሜይል ቡድን (email distribution network) አስገባኝ። ወቅቱ ኦነግ ውሰጥ ክፍፍል ተፈጥሮ ኦሮሞዎች በአንጃ ተከፋፍለው ክፉኛ የሚወጋገዙበት ነበር። ONET እና ONA ውሰጥ ሰዎች እርሰ በእርሰ የሚያደርጉትን ዘመቻ አይቼ በጣም ደነገጥኩ። እዚያ ላይ የሚጽፉ ሰዎች የብዕር ሰም ሰለሚጠቀሙ ማንነታቸውን ማወቅ አይቻልም። ይሀ ደግሞ ሰዎች እንደፈለጉ እንዲሰዳደቡ እና ሰም ለመጠፋፋት መንገድ እንደከፈተ ተረዳሁ። በእነዚያ ድረ-ገፆች ላይ ያየሁት ሹኩቻ የኦሮሞ ትግል ካሰብኩት በላይ አደጋ ውሰጥ እንዳለ አመላከተኝ።

ትግሉ አደጋ ውስጥ መግባቱ ብቻ ሳይሆን ውጪ የሚኖረው ማኅበረሰባችን ለከፍተኛ መበታተን መጋለጡን በመረዳት፣ ከሲንጋፖር ጨርሼ ለዩኒቨርሲቲ ትምህርት አሜሪካ ወይም አውሮፓ ከሄድኩ ትግሉን እና ማኅበረሰቡን በምን መልኩ መርዳት እንደምችል ማሰብ ጀመርኩ።

በዚሀ መልኩ የሁለት ዓመቱን የሲንጋፖር ትምህርቴን ወደ ማገባደዱ ስቃረብ ለተጨማሪ ትምህርት ዩኒቨርሲቲ ማፈላለግ ጀመርኩ። እያደጉ ካሉ ሀገራት፣ በተለይ ከአፍሪካ፣ የሚመጡ ተማሪዎች ትልቁ ሕልማቸው እንደምንም ብለው ወደ ምዕራባውያን ሀገራት መሄድ ነው። ለዚሀ ደግሞ በቀላሉ ይቀበሉኛል ብለው ወደሚያስቡት አነስ ያሉ ኮሌጆች ማመልከቻ ያስገባሉ። አማካሪዎች (admission councilor) ይሀን ሰለሚያውቁ መሰል ኮሌጆችን እንድንመርጥ ይገፋፉናል። የአደጉት ሀገራት ተማሪዎች ማመልከቻቸውን ትልልቅ ዩኒቨርሲቲዎች ሲያስገቡ ሰላየሁ አማካሪዬ ጋር በመሄድ እኔም እንደሌሉቹ ማመልከቻዬን ወደ ትልልቅ ዩኒቨርሲቲዎች በመላክ መሞከር እንደምፈልግ ነገርኳት። ያገኘሁት ምላሽ ግን ትልልቅ ዩኒቨርሲቲዎች ተቀባይነት የማግኘት ዕድሌ ጠባብ ስለሆነ አነስተኛ እና መለስተኛ ኮሌጆችን ብሞክር እንደሚሻለኝ ነበር። «ዋናዎቹን ብጠይቃቸው ምን እጎዳለሁ?» ብይ ጠየኩኝ። እሷም «ላይቀበሉህ ወይም ሰኮላርሺፕ ላይሰጡሀ ይችላሉ» አለችኝ። «ካለመቀበል ውጪ ሌላ ቅጣት የለውም አይደል?» ሰላት «የለውም ብላ መለሰች። «ከታዋቂዎቹ ዩኒቨርሲቲዎች መሞከር ከፈለክ በተጓዳኝ መጠባበቂያ (safety/backupscholls) እንዲሆኑህ አነስ ላሉትም ላክ። ዋናዎቹ ካልተቀበሉህ ባዶ እጅህን እንዳትቀር ዋስትና ይሆኑኸል» ብላ ምክር ብጤ ጣል አደረገች።

እኔም መፃፍ ያለበትን ነገር በሙሉ ካጠናቀርኩ በኋላ ለሰባት ታዋቂ ዩኒቨርሲቲዎች እና ከመለሰተኛዎቹ ደግሞ ለሦሰቱ ማመልከቻ አስገባሁ። ከጥቂት ወራት በኋላ በአውሮፓ፣በካናዳ እና በዩናይትድ ሰቴትስ የሚገኙ ሁሉም ዩኒቨርሲቲዎች (ትልልቆቹና መለስተኛዎቹም ጭምር) ከሙሉ ስኮላርሺፕጋር እንደሚቀበሉኝ አሳወቁኝ። የተቀበሉኝ ታዋቂ ዩኒቨርሲቲዎች በአውቅና አና በትምህርት ጥራት ሰለሚቀራረቡ ለመምረጥ አስቸገረኝ። መጨረሻ ላይ ሞቃታማ አየር ስለምወድ ካሊፎርኒያ ወደሚገኘው ሰታንፎርድ ለመሄድ ወሰንኩ።

ዩኒቨርሲቲ ለመሄድ ከወሰንኩ በኋላ የአሜሪካ ቪዛ ለማግኘት ወደ ሀገሬ መመለሰ ነበረብኝ። ወደ ኢትዮጵያ ተመልሼ ቪዛ ሰጠይቅ መጀመሪያ እምቢ ብለው በኋላ ግን ዩኒቨርሲቲው ባደረገው ጫና ቪዛ ተመትቶልኝ የመጀመሪያ ዲግሪዬን ለመማር ነሐሴ 1997 ዓ.ም ወይም በፈረንጆቹ 2005 ወደ አሜሪካ አቀናሁ።

# ክፍል አምስት - ዲያስፖራ

## 5.1.አሜሪካ

ነሐሴ 1997 ዓ.ም ከአዲስ አበባ ተነስቼ ወደ አሜሪካ በመሄድ ሰሜን ካሊፎርኒያ በሚገኘው ሳን ፍራንሲስኮ አየር ማረፊያ ደረስኩ። ከዚያም ታክሲ ይዤ ወደ ስታንድፎርድ ዩኒቨርሲቲ ካምፓስ ሄድኩ። የግቢው ስፋት ብቻውን ከአንድ ከተማ ጋር ይስተካከላል። በሦስት ሺህ ሦስት መቶ አሥር ሄክታር መሬት ላይ የተንጣለለ ሲሆን፣ ፓሎ አልቶ የተባለች አነስ ያለች ከተማ አጠገብ ይገኛል። የካሊፎርኒያ ግዛት ዓመቱን ሙሉ ለኑሮ ምቹ የሆነ የአየር ፀባይ አላት። በአሜሪካ ምሥራቃዊ ክፍል (East Coast) ከሚገኙት ዩኒቨርሲቲዎች ይልቅ ሰታንፎርድን የመረጥኩትም አንዱ በአየር ሁኔታው ነው።

ስታንፎርድ ዩኒቨርሲቲ የካሊፎርኒያ ገዢ እና ታዋቂ ባለጸጋ በነበረው Leland Stanford እና Jane በተባለች ባለቤቱ በ1885 ተቋቁሞ በ2891 ሥራ ጀመረ። በሕፃንነቱ ለሞተባቸው ልጃቸው መታሰቢያ ያቋቋሙት የግል ትምህርት ተቋም ነው። በአሜሪካ ከሚገኙ ምርጥ ዩኒቨርሲቲዎች አንዱ ሲሆን፣ እኔ በምማርበት ጊዜ ከአሥራ ስድስት ሺህ በላይ ተማሪዎችን በተለያዩ የትምህርት ዘርፎች እያሰተማረ ነበር። በየዓመቱ ሃምሳ ሺሀ ተማሪዎች የመጀመሪያ ዲግሪያቸውን በዩኒቨርሲቲው ለመማር የሚያመለክቱ ሲሆን፣ ተቀባይነት አግንተው የሚሳካላቸው ከአምስት በመቶ በታች ናቸው።

ዩኒቨርሲቲው የኮምፒዩተር እና ኢንደርሜሽን ቴክኖሎጂ (Information Technology (IT)) ምርምሮች እንዲስፋፉ ባደረገው ትልቅ አስተዋጽኦ ይታወቃል። አንደ ጉግል (Google)፣ ፌዝቡክ፣ HP እና ሌሎች ኩባኒያዎች የሚገኙባት የዓለም የIT ማዕከል "Silicon Valley" ፤ በዚሁ ዩኒቨርሲቲ ድጋፍ የተመሠረተች ሲሆን እዚያው አጠገቡ ትገኛለች። በአሁኑ ወቅት ዓለምን የተቆጣጠሩት ብዙዎቹ የIT ኩባንያዎች በዩኒቨርሲቲው ተማሪዎች የተጀመሩ ናቸው። ዩኒቨርሲቲው ተማሪዎች ከገቡ ጀምሮ በተለያየ መንገድ በፈጠራ እና ኢንተርፕረነርሺፕ ጠንካራ አንዲሆኑ ሰለሚያበረታታ ሰኬታማ ሲሆኑ፣ የተቋሙን ጥናት እና ምርምር ለማገዝ ከፍተኛ ገንዘብ ይለግሳሉ። በዚህ ምክንያት ስታንፎርድ በጣም ሀብታም ከሆኑ የትምህርት ተቋማት ዉስጥ አንዱ ነው።

ይህ የዩኒቨርሲቲው ባለጸጋነት በረከቱ ለእኔም ተርፎ ማመልከቻዬ ተቀባይነት አንዳገኘ ሙሉ ሰኮላርሺፕ ማግኘቴ ተነገረኝ። ከዩኒቨርሲቲው የቀድሞ ተማሪዎች መካከል አንዱ እኔን ጨምሮ ለሃምሳ ዓለም አቀፍ ተማሪዎች ሁሉንም ወጪ ሸፈነልን። እኔ በገባሁብት ዓመት

በዩኒቨርሲቲው ለመማር የሚያስፈልገው ወጪ ወደ ሰልሳ ሺህ የአሜሪካ ዶላር አካባቢ ይመሰለኛል። አብዛኞቹ ተማሪዎች በራሳቸው ወጪ የሚማሩ ናቸው፡ የተወሰኑት ደግሞ ገሚሱን በእርዳታ (financial aid) ገሚሱን ደግሞ በብድር ይከፍላሉ። እንደ እኔ ላሉ ጥቂት ተማሪዎች ሰኮላርሺፑ ሙሉ የት/ቤት ክፍያ፣ የኑሮ ወጪ፣ መጻሕፍት እና የአውሮፕላን መጓጓዣ ትኬትን ይሸፍናል።

ልክ ደርሼ ዶርም እንደተመደብኩ የመጀመሪያው ሥራዬ ሳይክል (bicycle) መግዛት ነበር። ግቢው በጣም ትልቅ ከመሆኑ የተነሳ ከዶርም ወደ ክፍል እንዲሁም በክፍሎች መካከል ያለሳይክል ለመድረሰ ጊዜው ያጥራል። በቀጣይ ሥራ መፈለግ ነበረብኝ። ለትምህርቴ የሚያሰፈልገውን ወጪ ሁሉ ዩኒቨርሲቲው የሚሸፍን ቢሆንም፣ ሀገር ቤት ያሉ ቤተሰቦቼን ለመርዳት ገንዘብ ያስፈልገኝ ነበር። በሳምንት እሰከ 30 ሰዓታት መሥራት ይፈቀዳል። የዩኒቨርሲቲው ፖሊስ ተማሪዎችን መቅጠር እንደሚፈልግ ማሰታወቂያ ሰላየሁ አመልክቼ ተቀጠርኩ። ሥልጠና ከወሰድኩ በኃላ ከትምህርቱ ጋር እንዳይጋጭ ማታ፣ ቅዳሜ እና እሑድ መሥራት ጀመርኩ። ሥራው ከፓሊሶች ጋር በመተባበር የጥበቃ ሥራ ማከናወን ነበር። የፓርኪንግ ሕግ ለሚጥሱ መኪናዎች ትኬት መስጠት፣ የካምፓስ ዝግጅቶች ሲኖሩ ጥበቃ ማድረግ፣ አደንዛዥ ዕፅ ለተማሪዎች የሚሸጡትን ተከታትሎ መያዝ የመሳሰሉትን ያካትታል።

ማታ ማታ በተለይ በሳምንቱ መጨረሻ ብዙ ፓርቲዎች በዩኒቨርሲቲው ግቢ ውሰጥ ሰለሚካሄዱ በሰከሩ ሴት ተማሪዎች ላይ አደጋ እንዳይደርስ አጅበን ወደ ዶርማቸው ማድረስ ፈታኙ ሥራ ነበር። ይሳደባሉ፣ ያስታውካሉ፣ ሊሰሙን ይሞክራሉ። ሆኖም በማግሰቱ ተጸጽተው ይቅርታ ይጠይቃሉ።

በዚያ የፖሊስ ሥራ ብዙ አሰደንጋጭ እና አሥቂኝ ገጠመኞች ነበሩኝ። አንዱ ሥራችን ሰክረው መኪና የሚነዱ ሰዎች አደጋ እንዳያደርሱ መከላከል ነበር። ለዚህ ደግሞ ቅዳሜ፡ እሑድ እና የኳሰ ግጥሚያ ባለበት ቀን ብዙ ሰዎች ሰለሚጠጡ፣ አነዳዳቸው ያጠራጠረንን ሾፌሮች እያስቆምን መስከር አለመስከራቸውን እንፈትሻለን። ፍተሻውም ከመኪና በማስወረድ በቀይ መስመር ላይ ሚዛናቸውን ጠብቀው መራመድ መቻላቸውን ማረጋገጥ፣ ከፍ ካለ ደግሞ በእጅ በሚያዝ መሳሪያ እንዲተነፍሱ በማድረግ የአልኮል መጠን መለካትን ይጨምራል።

አንድ ቀን የሆነ ጎደኛዬ ፍቅረኛውን አሳፍሮ መኪና እየነዳ ወደ ካምፓስ እየገባ ሳለ አየሁት። ሳይረን አሰጮኽን ካሰቆምነው በኋላ፣ ባልደረባዬ ሄዶ ከመኪናው አስወርዶ ሚዛኑን ጠብቆ በአንድ አግሩ እየዘለለ እንዲሄድ አዘዘው። ጓደኛዬ አልጠጣም ኖሯልና ያለምንም ችግር የታዘዘውን ፈጸመ። ፖሊሱ ቀጥሎ ልጂ ፍቅረኛውን ትከሻው ላይ ተሸክሞ በመሰመሩ ላይ እንዲራመድ አዘዘው። ልጁም ግራ ገብቶት የትዕዛዙን ሕጋዊነት ተከራከረ። ፖሊሱም ትዕዛዙን ተቀብሎ ልጅቷን ካልተሸከማት ወደ ፖሊስ ጣቢያ እንደሚወስደው አስፈራራው። ልጁ ትዕዛዙን በማክበር እና ባለማክበር መካከል እያንገራገረ አያለ ሳቄን መቆጣጠር አቅቶኝ ተቀምጬ ከነበረበት የፖሊስ መኪና ውስጥ ድምጽ ሳሰማ ጓደኛዬ ሰላየኝ፣ ሄጄ ትዕዛዙ የቀልድ እንደነበረ ነገርናቸው።

አንድ ምሽት እኔና አንድ የፖሊስ መኮንን በመኪና እየተዘዋወርን እያለ አንድ መኪና በፍጥነት አለፈን። የሳይረን መብራት እና ድምፅ ከፍተን ሰንከተለው አቆመ። የሾፌሩን መንጃ ፈቃድ

ተቀብለን መረጃውን ወደ ኮምፒዩተር ማስገባት እንደጀመርን ሌላ አደጋ እንደደረሰና በፍጥነት ወደቦታው መድረስ እንዳለብን ታዘን መታወቂያውን መልሰንለት ሄድን። በኃላ ስንሰማ ያ ሰውዬ
ተሰናብቶን 15 ደቂቃ ባልበለጠ ጊዜ ውስጥ ሌሎች ፖሊሶች አስቁመውት ማንነቱን ሲያረጋግጡ በሕግ የሚፈለግ መሆኑን ተረድተው ሊይዙት ሲሞክሩ ተኩስ ከፍቶ ሁለት ፖሊሶችን እንደገደለ አወቅን። እኔና አብሮኝ የነበረው ፖሊስ ማንነቱን ለማወቅ ሰናደርግ የነበረውን ምርመራ አቋርጠን ባንሄድ ኖሮ ሟቾቹ እኛ እንደነበርን ስንረዳ ደነገጥን። እንዲህ ዓይነቱ ግድያ በፖሊሶች ላይ ከፍተኛ ጥርጣሬ በመፍጠር፣ ሾፌሮችን ሲያስቆሙ ያለበቂ ምክንያት እንዲተኩሱ ምክንያት እንደሆነ ተገነዘብኩ። "መኪና ሰታሰቆሙ ንጹሕነቱን እስክታረጋግጡ ድረስ ማንኛውንም ሾፌር እንደ አደገኛ ወንደለኛ መቁጠር አለባችሁ" በማለት የጣቢያው አዛዥ ሁሌ የሚናገረውን አስታወሰኝ። በአጠቃላይ ያ የፖሊስ ሥራ የጸጥታ ተቋማትን እና የሰዎችን አሰራርና አስተሳሰብ ከውስጥ ለመታዘብ ስላስቻለኝ፣ ለወደፊት የግል ኑሮና የትግል ሥራ የጠቀመኝን ግንዛቤ ለማግኘት አግዞኛል።

ስታንፎርድ ሰገባ አንዱ ፈተና መማር የምፈልገውን የትምህርት ዓይነት መምረጥ ነበር። እስከ ሦስተኛ ዓመት ድረሰ ዋናውን ትምህርት (major) መወሰን ሰለማይጠበቅ ተማሪው የፈለገውን ተመዝግቦ መማር ይችላል። እንደሌሎች ሀገሮች የመጀመሪያ ዓመት ተማሪዎች የማኅበራዊ (social) እና የተፈጥሮ (natural) ሳይንስ በሚል አይከፈሉም። ዓላማው ተማሪዎቹ የተለያየ ኮርሰ ወስደው፣ በሂደት በቂ ግንዛቤን መሠረት በማድረግ ችሎታቸውን እና ፍላጎታቸውን በሚሰማማ መልኩ ሙያቸውን እንዲወሰኑ ዕድል መስጠት ነው።

ተማሪዎች ዋናውን ትምህርት ባይወስኑም ጊዜያቸውን ለመጠቀም እና ሰኬታማ ለመሆን የሚወስዱትን ኮርሶች ዝርዝር አስቀድመው አዘጋጅተው ይመጣሉ። ለእንዲህ ዓይነት ቅድመ ዝግጅት የሚያማክር ሰው ያስፈልጋል። አብዛኞቹ ተማሪዎች የተማሩ ቤተሰቦች ወይም የቅርብ ዘመዶች ሰላሏቸው፣ ሲመጡ ሰለ ዩኒቨርሲቲ ትምህርት በቂ ምክር አና ግንዛቤ ጨብጠው ነው። እኔ ግን የዩኒቨርሲቲ ልምድ ያለው ቤተሰብ እና ዘመድ ይቅርና አንድም የማውቀው ሰው አልነበረኝም። ይህ ደግሞ መውሰድ ያለብኝ ኮርስ እና ቅደም ተከተላቸው ላይ ቀድሜ እንዳልዘጋጅ አደረገኝ። ገና ሲንጋፖር እያለሁ የፖለቲካ ትምህርት ላይ ለማተኮር ብወሰንም የቱን ኮርስ እንደማስቀድም አና እንደማስከትል ስላልገባኝ፣ በመቶዎች የሚቆጠሩ ኮርሶች የተካተቱበት ማውጫ ሲሰጠን ርዕሱ የሳበኝን እንብቤ አና ተመዝግቤ ትምህርቴን ጀመርኩ።

ኮርሶቹን በእቅድ እንዳልወስድ ያደረገኝ የግንዛቤ አጥረት በጣም ጎዳኝ። ለምሳሌ ግንዛቤ ያላቸው ተማሪዎች በአንድ ሴሚሰተር ከባድ እና ቀላል ኮርሰ ሚዛናዊ በሆነ መልኩ ቀላቅለው በመውሰድ ሸክማቸውን ቀነሱ። እኔ ግን ደሰ ያለኝን ሰለምመዘገብ ከባድ ኮርሶችን እራሴ ላይ አበዛሁ። የመጀመሪያውን ዓመት በዚህ መልኩ ስጎዳ ቆይቼ በሚቀጥሉት ዓመታት ማስተካከል ቻልኩ። ዋናውን ትምህርቴን እስከ ሦስተኛ ዓመት ለመወሰን ባልገደድም ከመጀመሪያው ሴሚስተር ጀምሮ ከፖለቲካል ሳይንስ ዲፓርትመንት ጋር ቁርኝት ፈጠርኩ።

የስታንፎርድ የፖለቲካ ዲፓርትመንት ዓለም ላይ ከፍተኛ ዝና ያለውና ፕሮፌሰሮቹም የተለያዩ ጥናቶች እና መጻሕፍትን በማሳተም በቀዳሚነት የሚጠቀሱ ናቸው። የፖለቲካ ሳይንስ ኮርስ የሚያስተምሩኝን ፕሮፌሰሮች ቶሎ በመቅረብ በትምህርት ክፍለ ጊዜ ብቻ ሳይሆን በዕረፍት ጊዜያቸው ቢሮ እየሄድኩ ከእነሱ መማሩን ተላመድኩ። ክፍል ውስጥ ያልገባኝን በደንብ እንዲያብራሩልኝ እና ተጨማሪ መጻሕፍት እንዲጠቁሙኝ እጠይቃቸዋለሁ። እነሱም ፍላጎቴን

በመመልከት ዩኒቨርሲቲያችን ውስጥ እና ከዚያ ውጪ በሚደረጉ የተለያዩ ኮንፈረንሶች እና ሴሚናሮች እንድሳተፍ ሁኔታዎችን አመቻቹልኝ።

የሁለተኛ ደረጃ ተማሪ ሳለሁ የሚስበኝ የትምሀርት ዓይነት ሂሳብ እና የተፈጥሮ ሳይንስ ሲሆን፣ ዕድሜዬ እየገፋ ሲሄድ ግን በኦሮሞ ትግል ውስጥ ያለኝ ተሳትፎ እና ፍላጎት እየጨመረ በመሄዱ የታሪክ፣ የፍልስፍና፣ የምጣኔ ሀብት እና የባሕል መጻሕፍት ማንበብ ጀመርኩ፡ በዚህም ለፖለቲባ ያለኝ ፍላጎት ከፍ አለ። ወደ ሲንጋፖር ሄጄ የተለያዩ ሀገራትን ጎብኝቼ ጥሩ ግንዛቤ ካገኘሁ በኋላ ወደ ሀገሬ ተመልሼ ሕዝቤን ለማገልገል ያለኝ ፍላጎት እያደገ መጣ።

ሲንጋፖር ስማር ለሁለት ዓመታት ሙሉ ስኮላርሺፕ እንደተሰጠኝ እንጂ የገንዘቡ መጠን ስላልተገለጸ አንድ ቀን የት/ቤቱ ርዕሰ-መምሀርት ጋር ሂጄ ለስኮላርሺፕ የተመደበልኝ ገንዘብ ስንት እንደሆነ ጠየኳት። እሷም ነገሩ ስላልገባት «ለምን ማወቅ ፈለክ? ወስደሀ ትምሀርቱን መተው አሰብክ? ያንተኑ ወጪ ለመሸፈን ይውላል አንጂ በእጅሀ አይሰጥሀም› ብላ ቀለደች። «አይ የትምሀርቴን ዋጋ ለማወቅ ፈልጌ ነው። እኔን ለማሰተማር የወጣውን ወጪ አውቄ ተመጣጣኝ ኃለፊነት ለመወጣት አአምሮዬን ለማዘጋጀት ነው» ሰላት ነገረችኝ። አጠገቧ ሆኜ እኔን ለሁለት ዓመት ለማስተማር የሚወጣብኝን ገንዘብ ወደ ሀገራችን ብር ስመነዝረው፤ በወቅቱ በአካባቢያችን አሥር የገጠር አንደኛ ደረጃ ት/ቤቶችን መገንባት አንደሚችል ነገርኳት። እሷም «እንግዲሀ የትምሕርትሀን ወጪ ስላወክ ለኃለፊነትህ ተዘጋጅ» ብላኝ ተለያየን።

ዩኒቨርሲቲ ስገባ የትምሀርት ወጪዬ በብዙ አጥፍ አንደሚጨምር ገመትኩ። ለትምህርቴ የሚወጣውን ብዙ ገንዘብ ዋጋውን ልመልስ የምችለው ስመረቅ ምን ብሰራ ነው? ብዬ ማሰብ ደመርኩ። ስኮላርሺፕ የሰጡኝ ሰዎች ከእኔ የሚጠብቁት ክፍያ የለም፣ ፍለጎታቸው ተምሬ እራሴን እና ማኅበረሰቤን እንዳገለግል ነው። ከዚሀ ወጪ ጋር የሚሰተካከል ፋይዳ ለሕዝቤ ማበርከት የምችለው ምን ተምሬ፣ በምን ሞያ ብመረቅ ነው? ብዬ ራሴን ጠየቅሁ። ለራሴ የመስሰኩት መልስ «የወጣሁበት ሕዝብ ትልቁ ችግር ጭቆና ስለሆነ በትግላቸው ውሰጥ ተሳትፌ ተገቢውን መሥዋዕትነት በመክፈል አንድ ሰንዝርም ብትሆን ፈቅ ባደርግ ነው» የሚል ነበር።

በኦሮሞ ሕዝብ ትግል ውሰጥ ተጨባጭ ለውጥ ለማምጣት የፓለቲካ እውቀት ማካበት አስፈላጊ መሆኑን አመንኩ። ወደ ስታንፎርድ ያመራሁት ይህን እውቀት በተወሰነ መልኩ የፖለቲካ ትምሀርት በመማር ማግኘት እንደምችል በማሰብ ነው። የሰነቅኩትን ዓላማ ለማሳካት ገና በመጀመሪው ሴሚስተር ዴቪድ ሌይቲን (David Laitin) እና ጀምስ ፌሮን (James Fearon) የተባሉ ዕውቅ ምሁራን የሚያስተምሩትን "Ethinic Conflict" የተባለ ኮርስ ተመዘገብኩ። በወቅቱ ሁለቱ ምሁራን በብሔሮች ግጭት በዓለም አቀፍ ደረጃ በግንባር ቀደምትነት የሚታወቁ ተመራማሪዎች ነበሩ። የቀድሞዋን ሶቪየት ሕብረት (USSR) እና ዩጎዝላቪያን ያፈረሱ የብሔሮች ግጭት ጉዳዮችን በማጥናት ብዙ ጽሑፎችን አሳትመዋል።

ፕሮፌሰር ዴቪድ ሌይቲን ሶማሊያ ሰለኖረና ጥናትም ያካሄድ ስለነበረ፣ እንዲሁም ኢትዮጵያንም በተወሰነ ደረጃ ሰለሚያውቃት ተቀራረብን። የመጀመሪያ ቀን ቢሮው ሄጄ ፖለቲካ መማር እንደምፈልግ ስነግረው አላበረታታኝም። በፓለቲካ የተመረቁ ተማሪዎች ጥሩ ክፍያ ያለው ሥራ እንደማያገኙ ነገረኝ። ዓላማዬ ከተመረኩኝ በኋላ አሜሪካ ቆይቼ ሥራ መያዝ ሳይሆን ሀገሬ ገብቼ መታገል እንደሆነ ስነግረውና ውሳኔዬ ጠንካራ መሆኑን ሲረዳ ራሱ

ከሚያሰተምረው በተጨማሪ ሌሎች መውሰድ ያሉብኝን ኮርሶችና ልተዋወቃቸው የሚገቡ መምህራንን ጠቆመኝ። ማንበብ ያለብኝን ተጨማሪ መጻሕፍትም ወረቀት ላይ ጽፎ ሰጠኝ።

በክረምት ላይ ወደ ኢትዮጵያ ሄጄ በአርባጉጉ ተከሰቶ የነበረውን ግጭት ያጠናሁት በዚሁ ምሁር አማካሪነት ነው።

አንደኛ እና ሁለተኛ ዓመት ላይ ከኮመን ኮርስ (Common course) በተጨማሪ የብሔር ግጭት የችግር ምንጭ፣ ምክንያት፣ አካሄድ እና ውጤት ላይ የሚያተኩሩ ኮርሶችን ከወሰድኩ በኋላ ለግጭቶቹ መፍትሔ ወደሚጠቁሙት ተሸጋገርኩ። ለዚህ ደግሞ የዲሞክራታይዜሽን (Democratization) ምሁር የሆነውን ፕሮፌሰር ለሪ ዲያመንድ (Larry Daimond) አማካሪዬ አደረኩ። ፕሮፌሰሩ ብዙ መጻሕፍትን የጻፈ ተመራማሪና አሜሪካ እና ሌሎች ሀገራት ውስጥ የጥናት ተቋማት (Think Tank) በማቋቋም እና በመምራት ትልቅ ልምድ ያለው ነው። እሱም ፍላጎቴን በመረዳት በሚቀጥሉት ሴሚስተሮች መውሰድ ያለብንን ኮርሶች እና ማንበብ የሚጠበቅብኝን መጻሕፍት ጠቆመኝ። እሱ የሚያሰተምረውን ኮርዕ ከጨረሰኩ በኋላ በየሳምንቱ መጻሕፍት እየጠቆመኝ አንብቤ ትንታኔ በመጻፍ፣ መልሰን ተገናኝተን አንድንወያይበት ሁኔታዎችን አመቻችልን።

በተጨማሪም በሁለተኛው ዓመት ክረምት ላይ ወደ ኢትዮጵያ ሄጄ ጥናት እንዳደርግ የምርምር ገንዘብ ድጋፍ (researchgrant) እንዳገኝ ረዳኝ። በኢትየጵያ ፓርቲዎች የሚመሠረቱበትን እና የሚፈርሱበትን አካሄድ (party formation and fragmentation) ካጠናሁ በኋላ በአዘጋጀሁት ጽሑፍ ላይ ተመርኩዞ ወደ እንግሊዙ ኦክስፎርድ ዩኒቨርሲቲ ሄጄ ለአንድ ሴሚስተር ምርምሬን እንድቀጥል አደረገ። ኦክሰፎርድ ዩኒቨርሲቲ ረጅም ዕድሜ ያለውና ከእንግሊዝ የትምህርት ተቋማት በእውቅናው የመጀመሪያው ረድፍ ላይ የሚገኝ ሲሆን፣ የሀገሪቷ መሪዎች እና ምሁራን የሚቀረጹበት ነው። ኦክስፎርድ ሌሎች ተቋማት ውሰጥ የማይገኙ የመጻሕፍት ክምችት ስላለው፤ እኔ ደግሞ በኢትዮጵያ ውሰጥ የብሔሮች የግጭት ታሪካዊ አመጣጥን ማጥናት ስለፈለኩ ወደዚያው ተላኩ። ኦክስፎርድ ዩኒቨርሲቲ ሄጄ ከአሥራ አራተኛ አስከ አሥራ ስድስተኛ ክፍለ ዘመን ሰለነበረው የብሔሮች ግጭት ያሉ ማሰረጃዎችን ማንበብና መተንተን ላይ አተኮርኩ።

መደበኛ ኮርሶችን ከመውሰድ ባሻገር ኢትዮጵያ ውሰጥ ያለውን የግጭት ታሪክ፣ ባሕል እና ፖለቲካ ለመረዳት ስል ከንጋት እስከ እኩለ ሌሊት ቤተ-መጻሕፍት ማሳለፍን የሙጥኝ አልኩ። የኢትዮጵያን የግጭት መንስዔና ሥነ-ልቦና ለመረዳት ብዙ ጊዜ አንደሚደረገው የምኒሊክን ዘመቻ ወይም የ1260ዎቹን ክስተት መመልከት ብቻውን በቂ እንዳልሆነ፣ ወደኋላ ተመልሰን ከአሥራ አራተኛው እስከ አሥራ ስድስተኛው ክፍለ ዘመን የነበረውን አመለካከት፣ መሥተጋብር እና አካሄድ ማሰተዋል እንደሚያሰፈልግ ተረዳሁ። በዚህም ዛሬ የምንሰማቸው አብዛኞቹ ትርክቶች ከአምስት መቶ ዓመት በፊትም እንደነበሩ አየሁ። ያገኘኋቸውን መጽሐፎች እና ጽሑፎች ማንበቡ ብዙ ጊዜ ስለወሰደብኝ በአንድ ሴሚሰተር ቆይታ ስመጥሯን የለንደን ከተማ መጎብኘት የቻልኩት ለአንድ ቀን ብቻ ነበር።

## 5.2. የጥቁር ሕዝቦች ታሪክ ጥናት እና የኦባማ ምርጫ

በሚቀጥለው ሴሚስተር ወደ ስታንፎርድ ከተመለሰኩ በኃላ ሰለ ጥቁር አሜሪካውያን የትግል ታሪክ ኮርሶችን መማር እና ማጥናት ጀመርኩ። ሰለ ማርቲን ሉተር ኪንግ (Martin Luther King Jr) የሕይወት ታሪክ በመጻፍ የሚታወቀው ፕሮፌሰር ክሌይቦርን ካርሰን (Clayborne Carson) የሚያስተምረውን ኮርስ ስወስድ፣ ከጥቁር ሕዝቦች የትግል ታሪክ ብቻ ሳይሆን ከሰላማዊ ትግል ጋርም እንድተዋወቅ ዕድል ሰጠኝ። ፕሮፌሰሩ ኮርሱን ከወሰድኩ በኋላ በሰላማዊ ትግል ታሪክ እና ፅንሰ-ሐሳብ ላይ ፍላጎት እንዳደረብኝ ሰለተረዳ እሱ በሚመራው «Martin Luther King Jr. Research & Education Institute» ተቋም ጥናቴን እንድቀጥል ኢንተርንሺፐ (Internship) ሰጠኝ። የጥቁር ሕዝቦች በ1950ዎቹ እና 60ዎቹ ውስጥ ሰላማዊ የትግል ስልቶችን እንዴት ሲጠቀሙ እንደነበረ ሳጠና የሰላማዊ ትግል ጉዳይ የበለጠ ቀልቤን እየሳበው መጣ።

የጥቁር አሜርካዊያንን የመብት ትግል ጉዟቸውን ሳጠና፣ በተለይ እንደ ማርቲን ሉተር ኪንግ (Martin Luther King) እና ማልኮም ኤክስ (Malcom X) ባሉ ሰዎች አመራርነት በ1950ዎቹ አና 60ዎቹ የተካሄደውን የመብት ትግል ንቅናቄ ( Civil rights movement) የተሻለ በመረዳት ለኦሮሞ ትግል የሚጠቅም ልምድ ለማግኘት እሞክር ነበር።

ወቅቱ ባራክ ሁሴን ኦባማ (Barack Obama) ለአሜሪካ ፕሬዝዳንትነት ወደ ውድድር የገባበት ነበር። የምረጡኝ ዘመቻው በተለይ በወጣቶች ላይ የፈጠረው መነሳሳት ለትግል ያለኝ ፍላጎት የበለጠ እንዲጨምር አደረገው። ኦባማን ለመጀመሪያ ጊዜ ያወቅኩት እ.አ.አ. በ2007 ንግግር ለማድረግ ወደ አካባቢያችን በመጣበት ወቅት ነበር። ንግግሩን ካዳመጥን በኋላ አንድ አንጋፋ ፕሮፌሰር "ይሀ ሰው ለፕረዝዳንትነት የሚበቃ ነው። ፕሬዝዳንት ልናደርገው ይገባል" ብሎ ሲናገር አዛውቱን ስላሰደመመው ጥቁር ሴናተር የበለጠ የማወቅ ጉጉት አደረብኝ። ከዚያም ኦባማ ገና አፍላ ወጣት እያለ የጻፈውን "Dream from My father" የተሰኘውን መጽሐፍ ፈልጌ አነበብኩ።

ከወራት በኋላ ኦባማ የዴሞክራቲክ ፓርቲን ወክሎ በእጩነት ለመመረጥ አንደሚወዳደር በማስታወቅ ቅስቀሳ ወደ ማድረጉ ገባ። የቀድሞ ተወዳጁ ፕረዝዳንት ቢል ክሊንተን (Bill Clinton) ባለቤት አና በራሷም ጠንካራ ሴናተር የሆነችው ሂላሪ ክሊንተን (Hillary Clinton) የመሳሰሉ ተፎካካሪዎች ስለነበሩ መጀመሪያ ላይ ኦባማ የእጩነት ውድድሩን ያሸንፋል ብሎ የገመተ ሰው እምብዛም ነው። የምረጡኝ ዘመቻው እየበረታ ሲመጣ ግን የኦባማ ተቀባይነትም እየጨመረ መጣ። በዚህም የሀገሪቱ ሕዝብ ዓይን፣ ጆሮ፣ ትኩረት እና ምኞቱን በኦባማ ላይ አደረገ። በተለይ እኛ ተማሪዎች ዘመቻውን ለማጠናከር በሁሉም ዘርፍ ተረባረብን። ኦባማም የዲሞክራቲክ ፓርቲን የእጩነት ፉክክር በድል አጠናቅቆ፣ የሪፐብሊካን ፓርቲን ተወካይ ጆን ማኬንን (John Mccain) በሀገር አቀፍ ደረጃ በማሸነፍ የመጀመሪያው ጥቁር ፕሬዝዳንት ሆነ።

የኦባማ የምረጡኝ ዘመቻ እና ድል በዓለም ዙሪያ የፖለቲካ መነቃቃትን ያመጣ ክስተት ነበር። አንድ ክፉኛ የተጨቆነ ሕዝብ ከረዥም ትግል በኃላ በባርነት የገዛችው ሀገር ላይ የራሱን ተወላጅ ፕሬዝዳንት ማድረግ መቻል ትልቅ ተስፋን አጫረ። ለእኔ ደግሞ የፖለቲካ ግንዛቤይን ያጎለበተ እና የትግል ተነሳሽነቴን ያበረታታ ክስተት ሆነ። በምረጡኝ ቅስቀሳ ወቅት የኦባማ ተፎካክሪዎች የዘር እና በሀይማኖት ጉዳይ በማራገብ የመመረጥ ዕድል ሊነፍጉት ሞክረዋል። እሱ ግን ከማንነቱ ሳይሸሽ እና የወጣበትን ማኅበርሰብ ሳያሰከፋ እንዲሁም የተፎካከሪዎቹን ማንነት አንቋሾ ነጮችን ሳያሰበረግግ ፣ የሁለቱንም ወገን ድጋፍ በማግኘት ለማሸነፍ የተጠቀማቸውን ስልቶች በቅርበት በመከታተል ጥሩ ግንዛቤ ጨበጥኩ12። ከሁሉ በላይ ወጣቶችን የሚስብ ራእይ እና ሐሳብ በመጠቀም የፖለቲካ ስሜታቸውን አነሳሶቶ በማደራጀት፣ የፖለቲካ ለውጥ ማምጣት እንደሚቻል የነበረኝን ተሰፋ የበለጠ አጠናከረ። አንችላለን፤ (Yes We Can) የሚለው የኦባማ መፈክር ዓይኔ እያየ ሲተገበር ማየቴ እኛ የኦሮሞ ወጣቶችም ጠንክረን ከታገልን እና በስልት ከተመራን ያሰብንበት እንደርሳለን የሚል ተስፋ በውስጤ አጫረ።

የኦባማ መመረጥ ከፈጠረው መነቃቃት ጎን ለጎን በማርቲን ሉተር ኪንግ ኢንስቲቱት ሳጠናው የነበረው የጥቁር አሜሪካኖች እና የሌሎች ሕዝቦች ሰላማዊ ትግል ታሪክ እየመሰጠኝ ስለሄደ የበለጠ ማጥናት እንደምፈልግ ለፕሮፌሰር ካርሰን ስነግረው፣ በዘርፉ ፈር ቀዳጅ ምሁር የሆነው የጂን ሻርፕ (Gene Sharp) መጻሕፍት እንዳነብ እና እንዳጠና መከረኝ። ከሴሚስተር ንባብ በኋላ ያዘጋጀሁትን የጥናት ጽሑፍ በመገምገም፣ ቀጥሎ ማሀተመ ጋንዲ (Mahatma Gandhi) በሰላማዊ ትግል ላይ የሠሩትን ሥራ እንዳጠና ሁኔታዎችን አመቻችቶ ወደ ሕንድ ላከኝ። ዋናው የጥናት አማካሪዬ ፕሮፌሰር ላሪ ዳይመንድ ወደ ሕንድ የመሄድ አቅድ እንዳለኝ ሲሰማ እግረ መንገዴን ሰለ ፌደራሊዝም ሥርዓታቸውም እንዳጠና ሐሳብ አቅርቦልኝ፣ የምርምር ፕሮፖዛል (Research Proposal) እንዳዘጋጅ አዘዘኝና ከሕንዳውያን ተመራማሪዎች (የፌደራሊዝም ምሁራን) ጋር አሰተዋወቀኝ።

በፈረንጆቹ ኦገሰት 2008 ለአንድ ወር ቆይታ በፕሮፌሰር ካርሰን መሪነት ሀያ አምሰት ተማሪዎች ሆነን ወደ ሕንድ አመራን። ሕንድ ድንቅ ምድር እንደሆነች ገና ከአውርፕላን እንደወረዱ ታሰታውቃለች። ከአውሮፕላን ማረፊያ እንደወጣሁ እንግዳ የሆነ ሙቀት ፊቴን ገረፈኝ። ታክሲ ውሰጥ ገብቼ ጉዞ ሰንጀምር ከዚያ በፊት አይቼው የማላውቀው የመኪና እና የሰው ብዛት አጋጠመኝ። አሽከርካሪዎች እጃቸውን ከጥሩምባ ላይ አያነሱም፤ ሁሉም እንደጉድ ያሰጮኻል። መኪኖች በሉበት የሚቆሙ አንጂ የሚሄዱ አይመሰሉም። ሾፌሮች እና መንገደኞች በመስኮት አንገታቸውን አያወጡ ይጯጯኻሉ። ትራፊክ ከተጠራ ለመድረሰ ብዙ ሰዓት ስለሚፈጅ ድንገት መኪና ቢጋጭ ትራፊክ አይጠሩም፤ አዚያው ተነጋግረው ይጨርሳሉ። የሰዎች ብዛት ከመኪናው በሺህ እጥፍ ይበልጣል፡ እግረኛው ከመኪናው ጋር እየተሻሸ እና እየተገፋፋ ይርመሰመሳል። መላው የዓለም ሕዝብ አንድ ቦታ የተራገፈ ይመስላል።

12 የቄሮ ትግል ለድል በተቃረበ ወቅት ሽግግሩን እንዲመራ ለማ መገርሳን የደገፍኩበት አንዱ ምክንያት ልክ እንደ ኦባማ የወጣበት ማኅበረሰብ ድጋፍ ሳይጎድልበት፣ የሌሎችንም አጋርነት ማግኘት የሚያሰችለው ተክለ ሥብዕና ተጎናጽፏል ብዬ ሰላመንኩ ነው። ለማ የኦሮሞን ብሔርተኝነትም ሆነ የኢትዮጵያን ሀገራዊ ትርክት ሳይጻረር ሁለቱንም ለዘብ አድርጎ እና አዋህዶ የማቅረብ ችሎታ ነበረው። ይህ ደግሞ በኦሮሞ የትግል ካምፕ የመከዳት ሰሜት፣ በሌሎች ሕዝቦች ዘንድ የመገለል ሰሜት ሳይፈጥር ሁለቱንም ወደመሃል ማምጣት ሰለሚያሰችለው፣ ለሽግግር ፖለቲካ የሚስፈልገውን ለሁሉም ወገን አስማሚ መሪ (Consensus Leader) የመሆን ብቃት አለው የሚል ተሰፋ ነበረኝ።

መጀመሪያ በዋና ከተማዋ ኒው ደልሂ የሚገኘውን የማሀተመ ጋንዲ ሙዚየም ሄደን ጎበኘን። እንደ ቡድን ከምናደርገው ጉብኝት ጎን ለጎን ፕሮፌሰር ዳይመንድ ቀድሞ ባመቻቸልኝ መሠረት ከሀገሪቱ የፓርላማ፣ የፌደራል ፍርድ ቤት ዳኞች እና የዩኒቨርሲቲ ምሁራን ጋር ስለ ፌደራሊዝም ተወያየን። ከኒው ደልሂ ተነስተን የጋንዲ የትግል ማዕከል ወደነበረችው የጉጀራት ግዛት ሄድን። የእሳቸው ሥራዎች መዘግብት ተከማችቶ መኖሩ ብቻ ሳይሆን በትግሉ ወቅት የዓይን እማኝ የሆኑ፣ አሁን ደግሞ በጋንዲ ሥራዎች ጥናት ላይ የተሰማሩ ይገኛሉ። እንዲሁም በሀገሪቱ ውስጥ በጣም ሲናቁ የነበሩና ጋንዲ ሲታገልላቸው የቆዩት የዳሊት/ሀሪጃን (Dalit/ Harijan) ሕዝቦችም በብዛት ጉጀራት ይኖራሉ። በሕንድ ጉብኝቴ ወደፊት በተከተልኩት የፖለቲካ አመለካከቴ እና አቅጣጫዬ ላይ ተጽዕኖ ያሳደሩ ጥቂት ነገሮችን አገኘሁ።

የመጀመሪያው፣ የጋንዲ ሰላማዊ ትግል እንደ ሕንድ ያለ ሰፊ ሀገርን አንድ ለማድረግ እና ነጻነትን ለማጎናጸፍ ወሳኝ ሚና ተጫውቷል። ሰፊ ሕዝብ አስተባብሮ ለእያንዳንዱ ሰው እንደ ጥንካሬው እና ፍላጎቱ ሚና መስጠት በትግሉ ውስጥ የባለቤትነት ስሜትን ለማላበስ በጣም ጠቃሚ ነው። በተቃራኒው በትጥቅ ትግል ውሰጥ መሳተፍ የሚችለው የማኅበረሰቡ አካል ውስን ነው። ለምሳሌ በወጣትነት ዕድሜ ያሉ ወንዶች ካልሆኑ ዕድሜያቸው የገፋ አዛውንቶች ሊኖራቸው የሚችለው ሚና አናሳ ነው። በሰላማዊ ትግል ግን ሁሉም የኅብረተሰብ ክፍል ማለትም ሴት፣ ወንድ፣ አዛውንት፣ ወጣት ሳይል ሁሉም ሙያተኞች እንዳቅማቸው ካሉበት ቦታ በተለያየ መልኩ በቀጥታ መሳተፍ እንደሚችሉ የጋንዲ ትግል በግልጽ ያሳያል።

በተጨማሪም የትጥቅ ትግል የተማከለ እና የተዋረድ አደረጃጀት (centralized and hierarchical organization) የሚጠይቅ ሲሆን፣ ከፍ ያለ የሕዝብ ብዛት እና የብሔር/የሀይማኖት ብዝኀነት ባለበት ሀገር ውሰጥ ለአድሎ እና መገፋፋት ያጋልጣል። ይሀ ደግሞ የትግል ድርጅቶች መሰነጣጠቅ እና አንጃዎችን በመፍጠር ትግልን አዳክሞ ውጤታማነትን ይቀንሳል። ተሳክቶ ድል ከመጣ እንኳ በማግሰቱ ወደ አምባገነናዊ ሥርዓት ወይም ወደ እርስ በእርስ ጦርነት ሊያመራ ይችለል። ሰላማዊ ትግል ግን በተወሰነ ቡድን የበላይነት የሚመራ የተማከለ አደረጃጀት ኖሮት፣ ውሳኔዎች ከላይ ወደታች የሚፈሱበት ሳይሆን በጎንዮሽ ትሰሰር (horizontal network) ላይ የተመሠረት እና ያልተማከለ ነው።

ይህም የአንድ ቡድን የበላይነት እና የሌሎችን መገፋት በማጥበብ በድል ማግስት ወደ ዴሞክራሲያዊ አሥተዳደር ለመሸጋገር የሚኖረውን ዕድል ያሰፋል።

## 5.3. ሦስቱ የሕንድ ዴሞክራሲ አባቶች

ጋንዲ ከትጥቅ ትግል ይልቅ ሰላማዊ መንገድ መምረጣቸው ግዙፋን የሕንድ ሕዝብ ብዛት ለትግሉ ሸክም ሳይሆን የጥንካሬ ምንጭ እንዲሆን አስችሏል። ከቅኝ ግዛት ለመላቀቅ ሰላማዊ ትግልን መጠቀማቸው፣ ከአሀጉር ጋር በሚሰተካከል መሬት ላይ ቢሊዮን ሕዝብ እና በመቶዎች የሚቆጠሩ ብሔሮችን ይዘው ዴሞክራሲያዊ ሀገር እንዲገነቡ ትልቅ ሚና ነበረው።

የሕንድ ጉዞዬ ከጋንዲ ውጪ በሀገሪቷ የነጻነት ትግል ውስጥ ጠንካራ አመራር ሲሰጡ ከቆዩ የሁለት ሰዎች ታሪክ ጋር እንድተዋወቅ ረዳኝ። አነሱም ጃዋሃርላል ኔህሩ እና ቢ.አር. አምቤድካር ናቸው። ኔህሩ አባቱ የጋንዲ የትግል አጋር ሰለነበር ከሕጻንነቱ ጀምሮ የጋንዲን ሥራዎች በቅርበት ሲከታተል አድጓል። ከፍተኛ ትምህርቱን በእንግሊዝ ካምብሪጅ ዩኒቨርሲቲ ተምሮ ሲመለስ የነጻነት ትግሉ የእውቀት ምንጭ ሆኖ የመራ የሕግ ምሁር ነው። ሴኩላሪዝም፣ ፈደራሊዝም እና ፓርለሜንታዊ ዴሞክራሲ የመሪ ድርጅቱ ዋና መርሆዎች እንዲሆኑ በማድረግ፣ ከነጻነት በኋላ የሀገሪቱ የመጀመሪያ ጠቅላይ ሚኒስትር ሲሆንም ሕገ-መንግሥቱ በዚሁ መሠረት ላይ እንዲጸና አድርጓል።

አምቤከር ደግሞ ዳሊት (Dalit) ወይም ሀሪጃን (Harijan) በመባል ከሚታወቅ ማኅበረሰብ የወጣ ምሁር ነው። ይህ ማኅበረሰብ የተናቀ እና የተገፋ መደብ (lawor caste) ነው። አምቤከር ከቅኝ ግዛት ነጻ ለመውጣት ከሚደረገው ትግል ጎን ለጎን በሕንድ ማኅበረሰብ ውስጥ ያለው የመደብ መድሎ እንዲወገድ በመታገል ይታወቃል። ብዙውን ጊዜ በውጪ ጠላት ላይ ትግል ሲካሄድ ውሰጣዊ ኢ-ፍትኃዊነት እንዲሸፋፈን ሰለሚደረግ ከድል ኋላ ፍትኃዊ የፖለቲካ ሥርዓት መገንባት አዳጋች ነው። አምቤከር በሕንድ ማኅበረሰብ ውሰጥ በእርሱ ቡድንም ሆነ በሌሎች ላይ የሚፈጸምን ኢ-ፍትኃዊነት በነጻነት ትግሉ ወቅት በማጋለጥ እና እውቅና እንዲያገኙ በማድረግ በነጻነት ማግስት ችግሮቹን ሊቀርፍ የሚችል የፖለቲካ ሥርዓት እንዲገነባ አሰችሏል።

የሕንድን የነጻነት ትግል አነዚሀ ሦስት ምሁራን በጋራ የመሩት ሲሆን ከነጻነት በኋላ የተመሠረተው የፖለቲካ ሥርዓትም የእነሱ ሐሳብ ፍጭት እና ትብብር ውጤት ነው። ጋንዲ ከሰለማዊ ትግል ስለት ቀያሽነታቸው በተጨማሪ የነጻነት ትግሉ የሞራል ልዕልና ተምሳሌት እንዲሁም የብሔራዊ አንድነት ምልክት (moral leader and unifying national figure) ሆነው ሲያገለግሉ፤ ኔህሩ ትግሉ የሚመራበት የፖሊሲ እና የስትራቴጂ ሐሳቦች አመንጪ፣ አምቤከር ደግሞ የውሰጣዊ ፍትሕ አቀንቃኝ ነበር። ሦሰቱ መሪዎች ለሕንድ ነጻነት በጋራ ቢሰሩም በብዙ ጉዳዮች ላይ በእውቀት እና በሥነ-ምግባር የተመራ ጠንካራ ክርክር አካሂደዋል። ይህ ክርክራቸው በሌሎች ሀገሮች አንደሚደረገው ልዩነቶችን ለነገ ከማሳደር ይልቅ በሂደት እየፈቱ ወይም የሚፈቱበትን ሰልት እያበጁ በመሄድ ከነጻነት በኋላ ለተገነባው ዴሞክራሲያዊ ሥርዓት መሠረት የጣለ ነው።

በጣም ያስደነቀኝ የሕንድ የነጻነት ታጋዮች ጥንካሬ ከቅኝ ገዥዎች ጋር እየታገሉ ከነጻነት በኋላ በውስጣቸው ሊከሰቱ የሚችሉትን ችግሮች አሰቀድመው በመገመት መፍትሔ እያሰቀመጡ መሄዳቸው ነው። ለምሳሌ የሕዝባቸውን ብዝኀነት በመረዳት የብሔሮች ጥያቄ ከመነሳቱ በፊት እውቅና ይሰጣሉ፣ ጥያቄው ሲነሳ ምላሽ የሚሰጡበትን ዘዴ ያበጃሉ። እ.አ.አ በ1927 የሕንድ ብሔራዊ ኮንግረስ ሰብሰባ ለመጀመሪያ ጊዜ በደቡብ የሀገሪቱ ክፍል ተካሄደ። ከዚያ በፊት በሰሜን ከተሞች ሲካሄድ በሂንዲ ቋንቋ ይደረግ ሰለነበር ከደቡብ የመጡ እና ሂንዲ የማይችሉ ሰዎች በአስተርጓሚ ይሳተፉ ነበር። ደቡብ ላይ የተካሄደውን ሰብሰባ ግን በታሚል ቋንቋ ለማካሄድ ወስነው ጋንዲን ጨምሮ ሁሉም መሪዎች በአስተርጓሚ ተሳተፉ። ይሀም ለደቡብ ብሔሮች ያላቸውን ክብር በማሳየት የኮንገረሱን ተቀባይነት ይበልጥ አሳደገው።

የሕንድ መሪዎች እና ታጋዮች ሀገራቸው ብዙ ብሔር ብሔረሰብ ያቀፈች መሆኗን፣የብሔሮችን ማንነት ማክበር እንዲሁም እራሳቸውን የማሥተዳደር መብት ማጎናጸፍ ግዴታ እንደሆነ አምነው ተቀበሉ። በሌላ አነጋገር ነጻነታቸውን ከመጎናጸፋቸው ከሁለት አሥርት ዓመታት አስቀድመው በፌደራሊዝም ሥርዓት አስፈላጊነት ላይ ተወያይተው መግባባት ብቻ ሳይሆን የመንግሥት ሥልጣን ባይኖራቸውም ፅንሰ-ሐሳቦቹን በተጨባጭ መተግበር ጀመሩ። በነጻነት ማግስት ሕንድ በሰባት ግዛቶች የተደራጀች ሲሆን፣ የሕዝቡን/የብሔሮቹን ጥያቄ መሠረት በማድረግ ከጊዜ ወደ ጊዜ እየተሰፋፋ መጥቶ አሁን ሠላሳ ሰድሰት ክልሎች (ሀያ ሰምንት የራስ-ገዝ እና ስምንት በፌደራል የሚተዳደሩ) ሊኖራት ችሏል።

ጋንዲ፣ ኔህሩ እና አምቤድካር ካራመዱት ጠንካራ አቋም አንዱ ሁሉም ቡድኖች ማንነታቸውን ሳይለቁ አንድ የጋራ ሀገር መገንባት አንደሚቻል ነው። ለዚሀ ደግሞ ቀድመው መሠረት በማስቀመጥ፣ ከነጻነት በኋላ እውን ማድረግ ችለዋል። ከሕንድ ግዛቶች የተወሰኑትን ተዟዙሬ ስመለከት ያላቸው የመልክዓ-ምድር ስፋት፣ የአየር ፀባይ ልዩነት፣ የቋንቋ፣ የባሕል እንዲሁም የቆዳ ቀለማቸው ስብጥር ብዙ ሀገሮችን የጎበኘሁ መስሎኝ ነበር። የምትተዳደረው በአንድ ሀገረ-መንግሥት ሥር ሲሆን፣ ክልሎች የራሳቸውን መንግሥት መርጠው ባወጡት ፖሊሲ ይተዳደራሉ። ለምሳሌ ከክራላ የሚባለው ክልል የሶሻሊዝም ምጣኔ ሀብት ፖሊሲ ሲከተል፡ ጉጀራት ደግሞ በካፒታሊዝም ይተዳደራል፤ ሁለቱም ክልሎች በሕዝባቸው ብዛት የሚወከሉበት የጋራ ፌደራላዊ መንግሥት አካል ናቸው።

በጣት የሚቆጠሩ ብሔሮችን ያቀፉ እና የቆዳ ስፋታቸው ትንሽ የሆኑ ሀገራት በእርስ በእርስ ጦርነት ሲወድሙ፣ ሕንድ ያንን ግዙፍ ግዛት እና ማኅበራዊ ስብጥር አቻችላ ከጊዜ ወደጊዜ እየጠነከረ የመጣ አንድ ሥርዓተ-መንግሥት ማበጀት ችልላለች። ይህም የሆነው የብሔር ብሔረሰቦችን መብት ያከበረ ፌደራሊዝም በመመሥረቷ እና በሕዝብ ይሁንታ በተመረጠ መንግሥት በመተዳደሯ ነው። ለዚሀ ፌደራላዊ እና ደሞክራሲያዊ ሥርዓት እርሾው የተጣለው በቅኝ አገዛዝ ትግል ወቅት መሆኑን ተረዳሁ። በሀገሪቷ ያክናወንኩት የጥናት ጉብኝት የሰለማዊ ትግል ሰልቶችን እና ፌደራሊዝምን ለማጥናት ያለኝ ፍላጎት ይበልጥ እንዲጨምር አደረገ። በቀጣይ ወደ አሜሪካ ተመልሼ ጥናቴን ቀጠልኩ።

# 5.4 ወጣቶችን ማደራጀት

አሜሪካ ስሄድ አሰቀድሜ የማውቀው ሰው አልነበረም። እናም የኦሮሞ ማኅበረሰብ አባላችን ለማግኘት ሙከራ ማድረግ ጀመርኩ። በዚያን ጊዜ እንደ ፌሰቡክ እና ትዊተር ያሉ የማኅበራዊ ትስስር ገፆች ስላልነበሩ ከሰዎች ጋር በኢንተርኔት መገናኘት ያሰቸግራል። ሲንጋፖር እያለሁ የተቀላቀልኳቸው “Onet" እና "ONA" የተባሉ የኢሜይል ትስስር ቡድኖች ሰዎች የሚሰዳደቡባቸው መድረኮች ሰለነበሩ መጠቀም ፈራሁ።

በወቅቱ የኦሮሞ ወጣቶች የተለያየ "ቻትሩም (Chatroom) ይጠቀሙ ነበር። የኢ-ሜይል ትስስር ቡድኖች (e-mail distribution network) ላይ የሚላኩ መልዕክቶች ምሥጢራዊ በሆነ መልኩ ለሰዎች የሚሰራጩ ሲሆን፣ ቻትሩም ግን ለማንም ክፍት ነበር። አንድ መልዕክት ከለጠፍኩ ድረ-ገጹን የከፈተ ሁሉ ያገኘዋል ማለት ነው። አንድ ቀን ኦሮሞዎች የሚጠቀሙበትን የሆነ ቻትሩም ገጽ ከፍቼ «በቅርቡ ሰታንፎርድ ዩኒቨርሲቲ የመጣሁ ተማሪ ስለሆንኩ ከሀገሬ ሰዎች ጋር መተዋወቅ አፈልጋለሁ። ካሊፎርኒያ ግዛት ሳንፍራንሲስኮ አካባቢ የምትኖሩ ኦሮሞዎች ካላችሁ ጻፉልኝ› ብዬ ለጠፍኩ። ወዲያውኑ ንጉሜ ሄዪ፣ ፋጡማ ኢርቦ እና ደረጀ ዳዲ የተባሉ ሦስት ሰዎች ጻፉልኝና ሰልክ ተለዋውጠን በየተራ እየመጡ በአካል አገኙኝ፡ በኋለም ከቤተሰቦቻቸው እና ከማኅበረሰቡ ጋር አስተዋወቁኝ። እንደ አጋጣሚ አብዱሰቡር ኡመር የተባለ የሦስተኛ ዓመት ተማሪ እዚያው ስታንፎርድ ይማር ነበርና መልዕክቴን ከሌላ ሰው ሰምቶ ተገናኝተን ተዋወቅን።

ትምህርቴን ጀምሬ አንደተረጋጋሁ ከሲንጋፖር ይዤ የመጣሁትን እቅድ ወደ መተግበሩ ገባሁ። እዚያ በነበርኩበት ጊዜ ሰሜን አሜሪካ የሚደረገውን የኦሮሞ ትግል እንቅሰቃሴ በተለያዩ ድረ-ገፆች ስከታተል ነበር። በውጭ ሀገራት ያለው ሕዝብ ራሱንም ሆነ ሀገር ቤት ያለውን ትግል እንዲረዳ ከተፈለገ ከፖለቲካ አደረጃጀት በላይ በሲቪክ ማኅበራት ቢደራጅ ይሻላል የሚል አቋም ይዤ ነበር። ምክንያቱም ከትግል ሜዳ የራቀ ሰው ወይም ማኅበረሰብ ትግሉ ውሰጥ በቀጥታ ለመሳተፍ ርቀት ሰለሚገድበው በትግሉ ውስጥ ውጤታማ ሚና ሊጫወት የሚችለው በድርጅት አባልነት ሳይሆን በደጋፊነት ደረጃ ከተሳተፈ ነው ብዩ አምን ሰለነበረ ነው። ውጤታማ ድጋፍ ለመስጠት ደግሞ በተለይ በምዕራባውያን ሀገራት ውሰጥ በሲቪክ ማኅበራት መደራጀት የተሻለ ውጤት አለው። ይህን ሐሳብ አውን ለማድረግ ከወጣቶች መጀመር ፈለኩኝ።

እቅዴ በሲሪላንካ፣ በሲንጋፖር፣ በሆላንድ አና በካናዳ የወጣቶች አመራር ሥልጠና ላይ ተሳታፊ እና አሠልጣኝ ባዳበርኩት ልምድ ላይ በመመሥረት፣ ለኦሮሞ ወጣቶች የአመራር ክኅሎት ሥልጠና መስጠት ነበር። ሐሳቤን ከእኔ በፊት ሰታንፎርድ ለነበረው አብዱሰቡር አዋየሁትና ንድፈ-ሐሳቡን በጽሑፍ አዘጋጅተን ወጣቶች ጋር ለማድረሰ በድረ-ገጽዕች ላይ ለጠፍን፡ በሰዓታት ውስጥ ጽሑፋችንን ካነበቡ ሰዎች ምላሾች መጡ። አሰቀድመው ምላሽ ከሰጡን ወጣቶች መካከል አርፋሴ ገመዳ፣ ደሜ ኦርማ (ሙሐመድ አደሞ) ፣ ሴና ጂምጂኖ፣ ደበላ ተረሳ፣ ኢዶሳ አባገሮ፣ ቂጤሰ ጮሪ እና ሌይላ አባዋሪ ይገኙበታል።

ለጽሑፉ መልስ ለሰጡን ወጣቶች ሐሳቤን ስገልጽላቸው ስለወደዱት የኦሮሞ ወጣቶች አመራር ኮንፈረንስ (Oromo Youth Leadership Conference - OYLC) ወደ ማደራጀት ገባን። ኮንፈረንሱን እውን ለማድረግ የአሠልጣኞች ሥልጠና መስጠት ነበረብን። ለዚህም በሲንጋፖር፣ በሆላንድ እና በካናዳ የወጣቶች አመራር ሥልጠና ያሰለጠኑኝን ምሁራን (ኤክስፐርቶች) ጋበዝኩ። በወቅቱ እነዚህ አሠልጣኞች ሥልጠና ለመስጠት ብዙ ገንዘብ የሚጠይቁ ቢሆንም እኛን በነጻ ሊያገለግሉን ተስማሙ።

ለአሠልጣኞች ክፍያ መክፈል ይቅርና ለሥልጠና አዳራሽ የምናወጣው ገንዘብ እንኳን ስላልነበረን ሥልጠናውን በአርፋሴ አክስት ቤት አዘጋጀን። ቤቱ ሁለት መኝታ ክፍል እና አንድ ሳሎን ነበረው፤ አንዱን ክፍል ለአሠልጣኞቹ፣ ሌላውን ለሴቶች መኝታ፣ ማረፊያውን ክፍል ቀን ቀን ለስብሰባ፣ ማታ ማታ ደግሞ የወንዶች መኝታ አደረግነው። ምግብም እዚያው በማዘጋጀት ወጪያችንን ቀነስን። ወቅቱ እ.አ.አ ማርች 2006 ነበር፡ ለሥልጠናው ከካሊፎርኒያ ወደ ሚኒሶታ ለመጓዝ የሚያስችል ገንዘብ አልነበረኝም። እንደ አጋጣሚ አርፋሴ በአንድ አየር መንገድ ውስጥ ትሠራ ስለነበር፣ እሷ እና አንድ ሌላ ሰው በነጻ የመብረር መብት አለው፤ ነገር ግን ያ ሰው ከእሷ ጋር የመብረር ግደታ አለበት። ይህንኑ ዕድል ለመጠቀም ማታ ከሚኒያፓሊስ ተነስታ፣ እኩለ ሌሊት ሳንፍራንሲስኮ ደርሳ በዚያው አውሮፕላን ተመልሳ ከእኔ ጋር ወደ ሚኒያፖሊስ እንሄዳለን።

ለሁለት ቀናት በቆየው የአሠልጣኞች ሥልጠና ለአሥር አስተባባሪዎች ሥልጠና ሰጠን። ሥልጠናው የማደራጀት ስልት፣ የግለሰብ እና የቡድኖችን ባሕርይ ተረድቶ ለራስ የመጠቀም ክኅሎት እንዲሁም የተፈጥሮ ችሎታን የማጎለበቻ መንገዶች ላይ ያነጣጠረ ነበር። በተጨማሪም ብዝኅነት ያለው ማኅበረሰብን ለመረዳት፣ ለማቻቻል፣ ለማደራጀት አና ለመገንባት የሚያስችሉ ክኅሎቶችን ማዳበር ላይ ትኩረት አደረገ። የጋበዝናቸው ባለሙያዎች በተለያዩ ሀገራት እና ማኅበረሰቦች ላይ ተተግብረው አዋጭነታቸው የተረጋገጡ ስልቶችን እና ጥናቶችን አስተማሩን። ተሳታፊዎቹ ደግሞ ከኦሮሞ ሕዝብ ተጨባጭ ሁኔታ እና ትግሉ ካለበት ደረጃ ጋር በማቆራኘት አተገባበሩ ላይ ሲወያዩበት ከረሙ።

አሥሩ ወጣቶች አስቀድመው ከእኔ የሰሙትን ሐሳብ ከባለሞያዎች ባገኙት ትምህርት ካዳበሩ በኋላ ቁርጠኝነታቸው የበለጠ እየጠነከረ መጣ። ያሰብነውን የወጣቶች ኮንፈረንስ ክረምት ትምሀርት ቤት ሲዘጋ ለማካሄድ አቅደን ወጪያችንን ለመሸፈን መኪና ማጠብ፣፡ አይስክሬም መሸጥ እና ከነጋዴዎች ልገሳ መጠየቅ ጀመርን። በተጨማሪም አርቲሰቶችን በማስተባበር የሙዚቃ ኮንሰርት አዘጋጅተን ገቢ ማግኘት ቻልን። ከጎናችን ከቆሙት የመጀመሪያዎቹ ዘፋኞች መካከል ኤሌሞ አሊ፡ ከማል ኢብራሂም እና ዳግም መኮንን ይገኙበታል።

ክረምቱ ሲመጣ ከዩናይትድ ስቴትስ፣ ከካናዳ እና ከአውሮፓ የመጡ ከመቶ በላይ የሚሆኑ ወጣቶችን ጋብዘን ከሚኒሶታ ዩኒቨርሲቲ የመኝታ ክፍል እና የሥልጠና አዳራሽ ተከራይተን ሥልጠና መስጠት ጀመርን።

እነዚህን ወጣቶች ስንጋብዝ የኦሮሚያን አካባቢያዊ እና ሀይማኖታዊ ስብጥር ባገናዘበ መልኩ ስላደረግን፡ የዶርም ድልደላውም ሆነ የውይይት ቡድን ምደባው ስብጥሩን በሚያንጸባርቅ መልኩ ተከናወነ። ለምሳሌ የመኝታ ዶርም ስንመድብ እነሱ ወይም ቤተሰቦቻቸው ከተመሳሳይ

ዘን የመጡ ከሆነ አንድ ላይ እንዳይመደቡ በማድረግ፣ ከሌላ ዘን ወይም ሀይማኖት ተከታይ

ጋር መደብናቸው። በውይይት ቡድን ላይም በተመሳሳይ መልኩ ሰዎችን የማሰባጠር ስልት ተከተልን።

ሥልጠናው ሦስት ነገሮች ላይ ያተኮረ ነበር። አንደኛው፣ ወጣቶች የትውልድ፣ የመኖሪያ ቦታ፣ የእምነት እና የፆታን ድንበር አልፈው እንዲተዋወቁ እና ትስስር (network) እንዲፈጥሩ ሁኔታዎችን ማመቻቸት። ሁለተኛው፣ የአመራር ክኅሎታቸውን ለማሳደግ የንድፈ-ሐሳብ እና የተግባር ሥልጠና መስጠት። ሦስተኛው፣ የረጅም ጊዜ ልምድ ያላቸውን አንጋፋ መሪዎች፣ ምሁራን እና አርቲስቶች በመጋበዝ ወጣቶቹ በንድፈ-ሐሳብ የተማሩትን ከተጋባዦቹ ልምድ ጋር በማነጻጸር ግንዛቤያቸውን እንዲያሳድጉ ማድረግ ናቸው።

በሥልጠናው ላይ አስፈላጊ ግን አጨቃጫቂ የነበረው ብዝኃነትን ማሰተናገድ (diversity management) ላይ የሰጠነው ሥልጠና ነው። በወቅቱ ኦነግ ውስጥ መሰነጣጠቅ ተፈጥሮ ድርጅቱን በማዳከም ማኅበረሰቡንም በየጎራው ከፋፍሎት ነበር። ሆኖም የዚህ ድርጅታዊ መሰነጣጠቅ እና ማኅበራዊ ክፍፍል ምክንያት እና ዓይነቱ በግልጽ አይወራም። ሁሉም ቀን ሰለአንድንት አብሮ ሲዘምር ይውልና ወደ ቤቱ ሲገባ በሰፈር እና በሀይማኖት ሲተማማ ያድራል። በኢንተርኔት ድረ-ገጾች ላይ ከብዕር ስም ጀርባ ተደብቆ እርስ በእርስ ይረጋገማል። ይህ በአንጃ ተቧድኖ ሰም መጠፋፋት በግለሰብ አመራር የተወሰነ ብቻ ሳይሆን፣ የተወለደበትን ቦታና ሀይማኖት ማጥላላትንም ያካትታል።

የአንጃ መርዝ የወጣቶችን ታዳጊ አእምሮ እንዳይበክል መከላከል ወደፊት ትግሉን በአንድነት እንዲመሩ አስፈላጊ ሆኖ ስለታየን ብዝኃነትን እንዴት ማቻቻል እንደሚያስፈልግ ግንዛቤ ማስጨበጥ ላይ ያተኮረ ሥልጠና ለመስጠት ወሰንን። እንደ ኦሮሞ ያለ በቁጥር ግዙፍ እና ሰፊ መልክዓ-ምድር ላይ የሰፈረ ሕዝብ ሊኖረው ሰለሚችለው ተፈጥሯዊ እና ዘመናዊ ክፍፍሎች እንዲሁም እነዚህ ክፍፍሎች ወደ ጥላቻ እና ግጭት እንዳያመሩ የሚያስችሉ ስልቶች ላይ በምሁራን ሰፊ ገለፃ ተሰጠ።

ዘር፣ ብሔር፣ አካባቢ፣ ጎሳ እንዲሁም ሀይማኖትን መሠረት ያደረገ ቡድናዊ አድሎ መነሻው የተሳሳተ መረጃ (misinformation) ነው። ይህም ሁለት ወይም ከዚያ በላይ ቡድኖች ጎን ለጎን የሚኖሩ ከሆነ፣ በመሬት አቀማምጥ ወይም በአሥተዳደራዊ አከላለል የተነሳ በመካከላቸው ያለው ማኅበራዊ ትስስር እና የመረጃ ልውውጥ ጠንካራ ካልሆነ፣ አንዱ ስለሌላው የሚኖረው ግንዛቤ ግምታዊ/መላምታዊ ይሆናል።

አንድ የማኅበረሰብ ቡድን በሌለው ላይ የሚኖረው ግንዛቤ ከተጨባጭ እውነታ ይልቅ በግምት ላይ የተመሠረተ ሲሆን ወደ ሀሜት፡ ንቀት፣፡ ጥርጣሬ እና ፍርሀት ሊያመራ ይችላል። አነዚያን ሁለት ቡድኖች ሊያገናኝ የሚችል ሀብት (resources) ካለ ደግሞ ፉክክር ብሎም ግጭት ያመጣል። ፉክክር እና ግጭት የአንዱን ቡድን የኃይል የበላይነት ካስከተለ፣ የሁለቱ ግንኙነት የጨቋኝ-ተጨቋኝ ወደመሆን አድጎ የበለጠ መራራቅ፣ ጥላቻ እና ጦርነትን ያስከትላል። ከብዝኃነት ሊመጣ የሚችልን ችግር ለመቅረፍ ከመነሻው በቡድኖች መካከል በተጨባጭ አውነታ ላይ የተመሠረተ ትውውቅ ከመፍጠር መጀመር ያስፈልጋል። ከዚህ በመነሳት የኦሮሞ ወጣቶች አመራር ኮንፈረንሰ (OYLC) የሰጠው የብዝኃነት ሥልጠና ዋና ዓላማ

እነዚህ ወጣቶች በብሔራቸው ውስጥ ያለውን ስፋት፡ ልዩነት እና አንድነት አውቀው ወደፊት መስተጋብሩንም ብስለት ባለው መንገድ እንዲመሩት ለማስቻል ነው።

ከላይ እንዳልኩት ዶርም ስንመድባቸውም ሆነ ክፍል ውስጥ ሲቀመጡ በፊት ከሚያውቋቸው ጋር ሳይሆን ከማያውቋቸ፣ በአካባቢ እና በሀይማኖት ከሚለያዩት ጋር እንዲሆኑ በማድረግ፣ ከለመዱት የምቾት ቀጠና (Comfort Zone) በማውጣት ከእነሱ ለየት ካለው ኦሮሞ ጋር መሥራት እና መኖር እንዲለምዱ ዕድል ፈጠርን።

በዚህ ሁኔታ ለአንድ ሳምንት የሰጠነው ሥልጠና ከጠበቅነው በላይ የተሳካ ሆኖ አገኘነው።

# 5.5 ''Ethopia Out of Oromia''

የኦሮሞ ወጣቶችን የበለጠ ለማደራጀት እንዲያስችለን ተቋማዊ አደረጃጀች አsፈላጊ መሆኑ በኮንፈረንሱ ላይ ተደጋግሞ በመነሳቱ፣ ሐሳቡን ተቀብለን ዓለም አቀፍ የኦርሞ ወጣቶች ማኅበርን [International Oromo Youth Assocition...IOYA] መጨረሻ ላይ መሠረትን። ስሙን የሰየመው ደሜ ኦርማ (ሙሐመድ አደሞ) እንደነበር አሰታውሳለሁ፥ አርፋሴን ለፕሬዝዳንትነት መረጥናት። በሚቀጥሉት ዓመታትም በየከረምቱ ተመሳሳይ ሥልጠና መስጠቱን ገፋንበት። ዛሬ በሰሜን አሜሪካ እና በአውሮፓ ያለውን ማኅበረሰባችንን የሚያንቀሳቅሱ አራማጆች ብዙዎቹ በዚያ ሥልጠና ያለፉ ወጣቶች መሆናቸውን ስመለከት ፕሮጀክቱ ውጤታማ እንደነበር ያሳየኛል።

ዓለም አቀፍ የኦሮሞ ወጣቶች ማኅበር (IOYA) ውስጥ ብዙ ነገሮችን ለመሥራት ሞክረናል። ከእነዚህ ውስጥ አንዱ የተቃውሞ ሰልፎችን ማስተባበር ነበር። አ.አ.አ. በ2006 ለተቃውሞ ሰለፍሁለት መቶ የምንሆን ወጣቶች ከሚኒሶታ ወደ ዋሽንግተን ዲሲ ሀያ ሰዓት በመኪና ተጉዘን የአሜሪካ ውጭ ጉዳይ ሚኒስቴር መሥሪያ ቤት ፊትለፊት ዋሽንግተን ዲሲ እና አካባቢዋ ክሉ የኦሮሞ ማኅበረሰብ አባላት ጋር ድምጻችንን አሰማን። አንዳንድ የአማራ ፖለቲከኞች በተደጋጋሚ የሚቀባበሉት አንድ አባባል በዚያ ሰልፍ ላይ ካሰማሁት መፈክር ተቀንጭቦ የተወሰደ ነው።

ወቅቱ የኢትዮጵያ ጦር ሱማሊያ የገባበት ስለነበር፣ ለረጅም ጊዜ የኦርሞ ትግል አጋር ለሆነው የሰማሌ ሕዝብ አጋርነት (solidarity) ለማሳየት "Ethiopia Out Of Somalia (ኢትዮጵያ ከሱማሊያ ትውጣ) " የሚል መፈክር ይዘን ወጣን። ልጆቹ የያዙትን መፈክር አያየሁ በማንበብ ሳሰተጋባ ቆይቼ "Ethiopia Out Of... » እንዳልኩ መፈክሩን የያዘው ልጅ ተንቀሳቅሶ፣ ሌላ "Oromia.." የሚል መፈክር የያዘ ሰው ፊትለፊቴ ተደቀነ። እኔም የመጀመሪያውን እና ሁለተኛውን መፈክር አንድ ላይ አገጣጥሜ « Ethiopia Out Of Oromia» አልኩኝ። የመጀመሪያው ልጅ ከያዘው መፈክር ውስጥ የመጀመሪያዎቹ ሦስት ቃላት፡ ሁለተኛው ከያዘው ውስጥ አንድ ቃል ተቀላቀሉብን።

ከአፍታ በኋለ ስሕተቱን አርሜ መፈክሩን የተናገርኩ ቢሆንም፣ ከጥቂት ዓመታት በኋላ ስሜ አየታወቀ ሲመጣ ግን መፈክሩን ያዩ ሰዎች የመጀመሪያውን ስሕተት ብቻ ያየዘ ቪዲዮ ቆርጠው በማውጣት «የኢትዮጵያ ሕዝብ (ብሔር ብሔረሰቦች) ከኦሮሚያ ይውጡ» ብሏል በማለት አሁንም ድረስ ስሜን ለማጥፋት ይሞክራሉ።

ቀጥሎ «Ten Thousand March For Oromia » ብለን የሰየምነውን ትልቅ ሰልፍ በሚኒሶታ አዘጋጀን። በዚህ ሰልፍ ላይ ብዙ ሰዎች ከአሜሪካ እና ከካናዳ የተሰተፉ ሲሆን ሰልፉ አስከዚያ ዕለት ድረሰ ካዘጋጀናቸው ሰልሮች በተሳታፊዎች ብዛት ትልቁ ነው። በወቅቱ በቀደሙት ዓመታት ከሠራኋቸው ሥራዎች አንፃር ስሜ በዲያስፖራ የኦሮሞ ማኅበረሰብ ዘንድ መታወቅ

ጀምሮ ነበር። ሰልፉን ለማዘጋጀት ሰንሯሯጥ ጉንፋን ይዞኝ ድምፄ ስለተዘጋ፣ ንግግር እንዳደርግ ተጋብዤ ወደ መድረክ ወጥቼ ስናገር ድምፄ ለራሴም እንኳን አይሰማም ነበር። ሆኖም ሕዝቡ በስሜት ተውጦ ያጨበጭባል። ሴት ነባር ታጋይ እና አዛውንቶች እንባ በጉንጫቸው እየወረደ ሲያጨበጭቡ ስመለከት ሁኔታው በጣም ረበሸኝ። ሕዝቡ ትልቅ የነጻነት ጥማት እንዳለውና ባለፉት ዓመታት በሠራናቸው ጥቃቅን ሥራዎች ተስፋ እየሰነቀ እንደመጣ ተረዳሁ። እነሱ የጣሉብኝን ተስፋ ሊያሳካ የሚችል ዝግጅት እና ብቃት እንዳለካበትኩ ስለማውቅ በሕዝቡ ላይ ያየሁት ስሜት ከባድ ሥጋት ውስጥ ጣለኝ። ስለዚህም በግብታዊነት ሊጨበጥ የማይችል ተስፋ ከመስጠት፣ ብቃቴን አጎልብቼ መመለስ እንዳለብኝ ወሰንኩ።

ከሚኒሶታ ወደ ስታንፎርድ እንደተመለስኩ በዓለም አቀፍ የኦሮሞ ወጣቶች ማኅበር (IOYA) ከነበረኝ ኃላፊነት ለቀኩኝ። ስልክ እና ሌሎች የግንኙነት መንገዶችን ዘግቼ ከትምህርት እያገኘሁ ካለሁት እውቀት በተጨማሪ መጻሕፍት አንብቤ የበለጠ ለማዳበር ውሎዬ ቤተ-መጻሕፍት ሆነ። የሚያስተምሩኝን ፕሮፌሰሮች እና ሌሎቹንም በተገኘው ዕድል ሁሉ በመጠቀም መጠየቁን ተላመድኩት። ወደ ኦክስፎርድ ዩኒቨርሲቲ በመሄድም ጥናቴን አጠናከርኩ። ከአንጋፋ የኦሮሞ ምሁራን እና መሪዎች ጋር በመተዋወቅ ከእነሱ የምሰማውን መረጃ እና ልምድ እንደ ተጨማሪ የእውቀት ምንጭ መጠቀም ጀመርኩ።

## 5.6. በኦሮሞ ጥናት ማህበር መድረክ ላይ

አሜሪካ እንደደረስኩ ወጣቶችን ከማደራጀት በተጨማሪ በአንጋፋው የኦርሞ ጥናት ማሀበር (OSA) ውስጥ ተሳትፎ ማድረግ ጀምርኩ። ይህ ማኅበር የኦሮሞን ትግል በእውቀት ማመንጨት እና ማሰራጨት በኩል ለመደገፍ ታስቦ ውጪ በነበሩ ምሁራን በ1986 ተመሠረተ። በየዓመቱ በኦሮሞ ሕዝብ ታሪክ፣ ባሕል፣ ኢኮኖሚ እና ፖለቲካዊ ትግል ላይ የተሠሩ ጥናቶች የሚቀርቡበት ኮንፈረንስ ያዘጋጃል፡ ጥናታዊ ጽሑፎቹንም በጆርናል መልክ ያሳትማል። በሂደትም ስለ ኦሮሞ ሕዝብ እና ትግል የነበሩ የተዛቡ አመለካከቶች እንዲስተካከሉ ከፍተኛ ሚና ተጫውቷል።

ለመጀመሪያ ጊዜ OSA ስብሰባ ላይ የተሳተፍኩት በ2006 የመጀመሪያ ዓመት የዩኒቨርሲቲ ትምሀርቴን እንደጨረሰኩ ነበር። ዩኒቨርሲቲ ያለሁ ለአንድ ኮርሰ "Internal Challenges to Natonalist'' በሚል ርዕሰ ላይ የጻፍኩት የጥናት ወረቀት (research paper) ጥሩ ውጤት አሰገኘልኝ። ከዚያም የፐሮፌሰሩን የእርምች ሐሳቦች አካትቼ ጽሑፉ በኦሮሞ ጉዳይ ላይ እንዲያተኩር አሻሽዬ ረቂቁን (abstract) ለ OSA አዘጋጅ ኮሚቴ ላኩኝ። ረቂቁ ተቀባይነት ስላገኘ አ.አ.አ. ጁላይ 2006 መጨረሻ በሚኒሶታ ዩኒቨርሲቲ ውስጥ በተካሄደው ስብሰባ ላይ ለማቅረብ ተዘጋጅቼ ወደዚያው አቀናሁ።

ስብሰባው ላይ በርካታ ታዋቂ ምሁራን እና የኦነግ የፖለቲካ መሪዎችን ለማየት ታደልኩ። የጠዋቱ መድረክ አልቆ እኔ የነበርኩበት ቡድን (panel) ለከሰዓት ተቀጥረን ለማቅረብ ተዘጋጀን። የእኔ ጽሑፍ የፓለቲካ ጥናቶች ባሉበት ፓናል ሳይሆን ከሴቶች እና ሕጻናት ጉዳዮች ረድፍ መመደቡን ስመለከት ምናልባት ወጣት ስለሆንኩ እና ስለማያውቁኝ ይሆናል ብየ በትዝብት አለፍኩ። ይባስ ብሉ ከምሳ ስንመለሰ በትልቁ አዳራሽ ሳይሆን በሌላ ትንሽ ክፍል ውስጥ አንድናቀርብ መወሰኑን ነገሩን። የዋናው ኮንፈረንስ አካል ሳይሆን እንደ አንድ ትንሽ ፓናል (breakaway session) እንድናቀርብ መወሰኑን ሳውቅ ንዴቴን መቆጣጠር አቃተን።

ሴት እና ወጣት አቅራቢዎችን ነጥሎ ሰው ወደሌለበት ትንሾዬ አዳራሽ መግፋት ትልቅ ንቀት መስሎ ስለታየኝ በስሜት ብድግ ብዬ ከእኔ ጋር ሊያቀርቡ የተዘጋጁ ሴቶች እና ወጣቶችን አስከትዬ ትልቁ አዳራሽ መድረክ ላይ ወጣሁ። ማይክራፎኑን ከመድረክ መሪው እጅ ቀምቼ «ለወጣቶች እና ሴቶች ያላችሁ ንቀት ያሳዝናል። ቀኑን ሙሉ ስናዳምጣችሁ ውለን፤ አሁን ከትልቁ አዳራሽ ወደ ታች የወረወራችሁን አንድ ሰዓት እኛን ማዳመጥ አቅቷችሁ ነው? ታሳፍራላችሁ። እኛም ይህን አዳራሽ አንለቅም፡ ከፈለጋችሁ እናንተ ውጡ» አልኳቸው። አወያዩም ደንግጦ ከኮሚቴዎቹ ጋር ከተወያየ በኋላ ጥናታችንን ከተቀሩት ልጆች ጋር እዚያው ትልቁ አዳራሽ አንድናቀርብ ተፈቀደልን።

ያቀረብኩት ጽሑፍ " Regionalism out in the open: Its cause and consequence of oromo movement የሚል ሲሆን፡ በኦሮሞ ትግል ውስጥ የአንጃዎች መፈጠር መንሰዔ እና የሚያስከትለው ጉዳት ላይ ያተኩራል። ጽሑፉ በኦሮሞ ትግል ውስጥ

የሚስተዋለው አካባቢያዊነት (ጎጠኝነት) ሁለት መነሻ እንዳለው፡ አንዱ ተፈጥሯዊ ሌላኛው ሰው ሰራሽ መሆኑን በመግለጽ ይንደረደራል። ተፈጥሯዊ ስንል ኦሮሞ ሰፊ ቁጥር እና መልክዓ - ምድር ያለው እንደመሆኑ መጠን በብዙ ጎሳዎች የተደራጀና በአሰፋፈር የተለያየ መሆኑ ነው። እንዲህ ዓይነቱ ተፈጥሯዊ ክፍፍል በራሱ ችግር ባይሆንም ለከፋፋይ የፖለቲካ ኃይሎች ሕዝቡን እንደሚያጋልጥ ይተነትናል።

ሰው ሰራሽ ክፍፍል ስንል ደግሞ የዘመኑ የፖለቲካ አካላት በሕዝቡ መካከል የፈጠሩት ማለት ነው። ይህንንም በሁለት ከፍዩ አቀረብኩ፣ አንዱ ውጫዊ የፖለቲካ ኃይል (ጨቋኝ መንግሥታት) የፈጠሩት ሲሆን፣ ሌለኛው ደግሞ ውስጣዊ ኃይሎች (የኦሮሞ አመራር እና ድርጅቶች) ያመጡት ነው። ጨቋኝ ሥርዓቶች ኦሮሙማን በማዳከም ሕዝቡ ለጋራ ድርጊት (collective action) ኃይል እንዳይኖረው ያዳክሙታል። አንድ ማኅበረሰብ ለጋራ ጥቅሙ በጋራ መሰለፍ የሚችለው የወል ማንነት (collective identity) እና አስተባብሮ ሊያንቀሳቅስ የሚችል ተቋም ሲኖረው ነው። የኦሮሞን ሕዝብ የጋራ እሴቶች በማውደም፣ በማጥላላት ወይም በሌላ በመተካት የወል ማንነቱ እንዲላላ በመደረጉ ለጋራ ዓላማ የመሰለፍ አቅሙ እንዲመናመን ሆኗል። በተጨማሪም ቀድሞ የነበረውን የገዳ አሥተዳደራዊ መዋቅር በማፍረስ የኦሮሞ ጎሳዎችን በታትኖ ከሊሎች ጋር የተጣመረ አሥተዳደር በመመስረት ኦሮሞ የጋራ መዋቅር እንዳይኖረው ተደርጓል። በዚህም የወል ትስስር እያላላ አካባቢያዊ ማንነት እየገነነ መጣ። በሂደት ሰዎች በጋራ ማንነታቸው (በኦሮሞነት) ሳይሆን በአሥተዳደራዊ ግዛታቸው (ሐረርጌ፡ ወለጋ፣ ባሌ፡ ሸዋ ወዘተ) ብለው አራሳቸውን መግለጽ ጀመሩ። በዚህ መልኩ የሕዝቡ የጋራ ማንነት ተሸርሽሮ ከጊዜ ወደ ጊዜ እየተራራቀ በመምጣቱ ለጋራ ጥቅም እና ተግባር ማሰተባበር አዳጋች ሆነ።

ከላይ እንደተጠቀሰው አንድ ሕዝብ ከበደል እና ከጭቆና ለመላቀቅ በጋራ መታገል ያስፈልገዋል። በጋራ ለመታገል ደግሞ በጋራ ማንነት ላይ የተመሠረተ የጋራ ንቃተ-ኅሊና (common consciousness) ማዳበር አለበት። ይሀ ማለት አንድ የሚያደርገው ባሕል፣ ታሪክ፣ የጋራ ቋንቋ እንዳለው ማወቅ እና የተጨቆነውም በጋራ መሆኑን ተገንዝቦ ከዚህ በደል ለመለቀቅ አብሮ መታገል አስፈላጊ እንደሆነ ማመን አለበት። ሰለሆነም የኦሮሞ ትግል የመጀመሪያው ተግባር የፈራረሱ እና የተዳከሙ የወል እሴቶቹን መልሶ ማጠናከር እንዲሁም ጨቋኙ አገዛዝ ኦርሞን በመበታተን የወል ትግል እንዳያደርግ የሚጠቅምባቸውን ስልቶች ማክሸፍ ላይ ማተኮር ነበር። በ1960ዎቹ የሜጫ እና ቱለማ መረዳጃ ማኅበር፣ የተማሪዎች ንቅናቄ ቁቤን የመቅረጽ እንቅስቃሴ፡ የባሕል ትርዒት ማዘጋጀት የመሰሰሉት ሥራዎች ዓላማቸው የተራራቀውን ሕዝብ መልሶ እንዲተዋወቅ፡ እንዲተሳሰር እና ለጋራ ጥቅም እንዲደራጅ ማስቻል ነበር።

የኦሮሞን የወል ማንነት መልሶ የመገንባት እና ሕዝቡን ለጋራ ትግል የማደራጀት ሥራ ስኬታማ ቢሆንም ትግሉን በመሩ ግለሰቦች እና ድርጅቶች መካካል ግጭት በመከሰቱ እንጃዎች እያደር መፈጠር ጀመሩ። በቡድኖች እና በግለሰቦች መካከል የተፈጠረው ፉክክር ወደ ቡድንተኝነት በማደግ የአካባቢያዊነት መልክ አየተላበሰ መጣ። የትግል ድርጅቶች ተመሰርተው ገና ሳይጠኑ ብዙ አመራሮች ሰለተሰዉ (ታደሠ ብሩ፡ መገርሳ በሪ፣ ባሮ ቱምሳ ወዘተ) ትግሉንየመምራት ኃላፊነት በመካከለኛ ደረጃ አመራር (mid-level leadership) ላይ ወደቀ። በዚያ ደረጃ ያሉ መሪዎች ደግሞ ብዝኀነት ያለውን ማኅበረሰብ ለጋ በሆኑ ድርጅቶች ውስጥ በሚፈለገው ልክ አያጣጣሙ ለማስኪድ የሚያስችል ክኅሎት፡ ልምድ እና ተሰሚነት አልነበራቸውም።

አባላቱን እና ሕዝቡን በብቃት ማሰለፍ ያልቻለ አመራር ትግሉን ውጤታማ ማድረግ ስለማይችል ከበታች አመራር ኩርፊያ እና አመጽ ሊገጥመው ይችላል። በችሎታው ውጤታማነት ተገዳዳሪዎቹን መብለጥ ስለሚሳነው፣ ከውስጥ የሚነሳበትን አመጽ ለመቋቋም በሚታመኑለት ሰዎች ራሱን ይከበል። ይህ ታማኝነት በአብዛኛው በአካባቢ ቅርበት እና በጎሳ ትስስር ላይ ስለሚመሠረት በሌሎች ዘንድ ጥርጣሪ እና ቅያሜ ይፈጥራል። ሥልጣን በችሎታ ሳይሆን በታማኝነት፣ ታማኝነት ደግሞ 'በዝምድና' ስለሚሆን የድርጅት ባሕል እየሆን ይመጣል። ዝምድና የሥልጣን ማከፋፈያ መስፈርት መሆኑ የሚፈጥረው ኩርፊያ አንጃነትን (factionalism) በማዋለድ በሂደት የድርጀት መሰንጠቅ ያስከትላል። ጎጠኝነት በኦሮሞ የትግል ድርጅቶች ውስጥ ቀስ በቀስ እየዳበረ መጥቶ፣ የአንጃነት መሠረት ጥሎ ሥር የሰደደው በዚህ መልኩ እንደሆነ አሰረዳሁ።

ጥናቱን በኦሮሞ ጥናት ማህበር (OSA) ስብሰባ ላይ ሳቀርብ ጉዳዩ የሚመለከታቸው በርከት ያሉ የትግሉ መሪዎች እና ምሁራን ቢኖሩም ጥያቄም ሆነ ትችት ያነሳ አልነበረም። ከብዙኀኑ ፊት ለይ ደንጋጤ፣ ንዴት እና ሀዘን ይታያል። ሆኖም ስብሰባው ከተጠናቀቀ በኋላ በቀጣይ ቀናቶች አስተያየቶች ኢሜሌን ማጥለቅለቅ ጀመሩ። ይደርሰኝ የነበረው አብዛኛው መልዕክት ስድብ እና እርግማን ያዘለ ነበር። ኦሮሞን ከፋፈልክ፣ ውስጣዊ ምሥጢር አወጣህ፣ ኦነግን ተቸህ እና የመሳሰሉት ዘለፋዎች ደረሱኝ። የተወሰኑ ምሁራን ግን እንደዚያ ዓይነት ጥናት ደፍሬ በማቅረቤ አድናቆታቸውን ገልጸውልኝ፣ ጥናቱን የበለጠ አዳብሬ ሰፊው ሕዝብ ጋር እንዳደርስ መከሩኝ። ለመጀመሪያ ጊዜ የተቀናጀ የስም ማጥፋት ዘመቻ በኢንተርኔት የተከፈተብኝ ያኔ ነበር።

በወቅቱ ጎጠኝነት ኅብረተሰቡን ከፋፍሎ፣ ኦነግን በአንጃዎች ሰንጥቆ፣ ትግሉን አቅም አልባ ማድረጉን ሁሉም የሚያውቀው ሀቅ ቢሆንም ጉዳዩን በግልጽ መናገር ችግሩን እንደማባባስ ይቆጠራል። ጥናቱን ያቀረብኩት ኅብረተሰባችንን እንደ ምሰጥ ውሰጡን እየበረበረ እና ትግሉንም እያለሸቀ ያለን ችግር በግልጽ አውጥተን ካልተወያየንበት መፍትሔ ሊበጅለት እንደማይችል ስላመንኩ ነው። እየዘነበብኝ የነበረውን የትችት እና የእርግማን ዶፍ ተቋቁሜ ሕዝቡን ማስተማር አለብኝ ብዬ ወሰንኩ። ሰዎች በሚሰባሰቡበት ቦታ (እድር፣ ለቅሶ እና የሀይማኖት ቦታዎች) በመገኘት የጎጠኝነትን መነሻ እና ጉዳት ማስተማሩን ቀጠልኩበት። ያንን ጽሑፍ በ2006 አቅርቤ ከሁለት ዓመት በኋላ ተከድኖ ሲበስል የነበረው ጎጠኝነት በ2008 ፈንድቶ በመውጣት፣ ኦነግ «ለውጥ» እና «ሸኔ» በሚባሉ ሁለት አንጃዎች ተሰነጠቀ። የለውጥ አንጃ በጄነራል ከማል ገልቹ ሲመራ፣ ሾኔ ደግሞ የዳዉድ ኢብሳ አንጃ ነበር።

የ2008ቱ የኦነግ መሰንጠቅ የፖለቲካ ድርጅቱን ብቻ ሳይሆን መሰጊዶች እና አብያተ-ክርስቲያናትን ሳይቀር አመሰ። የጎጠኝነት መነሻ እና መዘዞች ላይ ጥናት ሳቀርብ ያወገዙኝ ሰዎች ክስተቱ ሲፈጠር የምርምር ወረቀቱን እንድልክላቸው መጠየቅ ጀመሩ። የኦሮሞ የትግል ድርጅቶች በጎጠኝነት መሰንጠቃቸው በ2008 የተጀመረ አልነበረም። እ.አ.አ. ኦነግ በ2001 «ሽግግር» እና «ሸኔ» ብለው በተፈራረጁ ሁለት አንጃዎች በተሰነጠቀበት ወቅት ጎጠኝነት የራሱ ሚና ነበረው፣ እንዲሁም በ1980ዎቹ እና በ1990 ለነበሩት ልዩነቶችም የጎጠኝነት አስተዋጽዖ የጎላ ነው። የ2008ቱ የሚለየው ምናልባት የትግል ድርጅቱ አመራር ከሀገር ውጪ ስላለ እና ከኢንተርኔት መስፋፋት ጋር ጎጠኝነት ተካርሮ እና

በግልጽ ወጥቶ ከድርጀቱ ውጪ ያሉ የማኅበረሰብ ክፍሎችን በማሳተፉ ይሆናል። ብዙዎች ለዓመታት በትግል ሜዳ እና በስደተኛ ካምፕ አብረው እንዳለተቸገሩ፣ በወንድማማችነት እና እህትማማችነት አንዳቸው ለሌለኛቸው ነፍሳቸውን እንዳልሰጡ፡ የማታ ማታ የጎጠኝነት ፖለቲካ አጣልቷቸው በአሰዕቀያሚ የስም ማጥፋት ዘመቻ ላይ ተሳተፉ። በአንድ ወቅት 'ሞት እንጂ ምንም አይለየንም' ብለው የተማማሉ ቅደኛሞች፣ ዓይንህን ለአፈር የሚባባሉ ጠላቶች ሆኑ፡ ተጋብተው የተዋለዱ ቤተሰቦች ተበተኑ። በራስ ቋንቋ ፈጣሪን ለማመስን በስንት መሥዋዕትነት የተከፈቱ የእምነት ቤቶች በሀይማኖታዊ አስተምሮ ልዩነት ሳይሆን በአንጃ እና በመንደር መስመር ተከፈሉ። ብዙ አቀንቃኖች ከአንዎቹ ጎን ስለተሰለፉ፣ ድሮ ሞልቶ ይፈስ የነበረው ኮንሰርታቸው በባዶ አዳራሽ ተተካ። ሰብሰባዎች ብዙ ጊዜ የአንካ ስላንቲያ እና የብጥብጥ መድረክ ስለሚሆኑ አብዛኛው ሰው ስብሰባ የተባለ ነገር አርም አለ። ሰርግ እና ሀዘን መድረስ እየከበደ፡ በደሰታ አና በሀዘን አብሮ ለመቆም አንኳ በጎጥ ወደ መመራረጥ ተኪደ።

የ2008ቱ የኦነግ መከፋፈል እኛ ወጣቶቹም ላይ ተጽዕኖ ፈጥሮብናል። ሁለቱም አንጃዎች የሲቪክ ድርጅቶችን ክንፋቸው ለማሰለፍ ከፍተኛ ዘመቻ ያደርጉ ስለነበር፤ ዓለም አቀፍ የኦሮሞ ወጣቶች ማኅበርን (IOYA) ለማማለል ሞክረዋል። ነገር ግን ስለ ጎጠኝነት እና አንጃነት ነገሩ ሳይፈነዳ በፊት፣ ብዝኀነትን በማስተናገድ ሥልጠና ውስጥ በግልጽ ሰለተወያየንበት የፓለቲካ ድርጅቶቹን ያጠፋቸው ወረርሽኝ ወደ እኛ ሳይዛምት ለመከላከል የተሻለ ዝግጅት ነበረን። የተወሰኑ ወጣቶች በአንጃዎቹ ፕሮፓጋንዳ መማረካቸውን ማስቀረት ባይቻልም፣ አብዛኛቻችን ግን አንድንታችንን አጠናክረን በጽናት አለፍነው። በተቃራኒው ከፍፍሉ ማኅበረሰቡ ላይ ሊያደርስ የሚችለውን አደጋ ለመቀነስ ስንሰራ ነበር።

ኦነግ እንደተከፈለ በዲያስፖራ የኦሮሞ ፖለቲካ ማዕከል በሆነችው ሚኒሶታ የሚኖረው ማኅበረሰብ አርሲ፣ ወለጋ፣ ሐረርጌ፣ ሸዋ ወዘተ እያለ ተከፋፍሎ በማኅበራዊ ግንኙነቱ ሳይቀር ወደ መቆራረጥ ደረጃ ደረሰ። ሰርግ አና ለቅሶ እንደድሮው ሁሉም ስለማይገኝበትና በአንድ አካባቢ ሰዎች ብቻ ስለሚሞላ፣ በሌላ አካባቢ ላይ የሚደረግ የሐሰት ወሬ እና ሀሜት ያለ ፍርሀት እና ኀፍረት እንዲካሄድ አስቻለ። የአንኛዎቹ ካድሬዎች የሐሰት ወሬ ያለ አንዳች ማጣራት በማሰራጨት ጥላቻው የበለጠ እንዲስፋፋ ሁኔታዎችን አመቻቸለቸው።

ይህን ስለተረዳን ከሁሉም አካባቢ እና ሀይማኖት የተውጣጣን ውሰን ወጣቶች ሰርግ ብንጠራም ባንጠራም፡ ሟችን ብናውቅም ባናውቅም መሄድ ጀመርን። ሰርግ አለ ከተባለ ያለንን የክት ልብስ ለብሰን ሽክ ብለን በብሩህ ፊት ከድግሱ አንታደማለን፣ ሀዘንም ሲሆን እንደ አካባቢው ወግ አስፈላጊውን ነገር ይዘን እንሄዳለን። የአንጃ ካድሬዎች የሌላ አካባቢ ሰው ይመጣል ብለው ስለማይገምቱ፡ በቡድኖች ላይ ያነጣጠረ ፕሮፓጋንዳን ጮኽ ብለው ያራግባሉ። ከዋኹም ዋሾታችኃል የሚላቸው ሰው ስለሌላ መርዛቸውን ያለከልካይ ይረጫሉ። የእኛ ቡድን ድንገት ሲገባ የአንጃ ወሬው ይቆምና ዝምታ ይሆናል። ቡድናችን ከሁሉም አካባቢ የተውጣጡ ሰዎች ስላሉበት ለቅሶ ቤት የሚሰበሰቡት ሰዎች አንድን አካባቢ ነጥለው ለማማት እና ለመውቀስ ያፍራሉ። አንዳንዴ ለከተማው እንግዳ የሆነ እና የማያውቀን ሰው መጥቶ ሰለ ጎጥ ማውራት ሲጀምር አጠገቡ ያለ ሰው ነካ አድርጎ ዝም ያሰኘዋል።

እኛም ለአጭር ጊዜም ቢሆን የሀሜትን መርዝ ስላስቆምን ደስ ብሉን እንወጣለን።

የሆኑ አዛውንት ሁሌም እንደኛው ለቅሶ እና ሰርግ ይመላለሳሉ። አንድ ቀን በር ላይ አገኙንና «ኦሮሞ በየሰፈሩ ቅሌን ጨርቄን ባለበት እናንተን በየሰፈሩ ምን ያዞራችኃኋል?» ብለው ጠየቁን። እኛም «እርሰዎን የሚያዞሮት ነው እኛንም የሚያዞረን›› ብለን ስንመልስላቸው ሳቅ ብለው ወደ ለቅሶ ቤቱ ገቡ። ጨርሰን ስንወጣ ስታርባክs (starbucks) ወሰዱንና ቡና ጋብዘው ያወሩን ጀመር። ለረጅም ጊዜ በትግል ውሰጥ የቆዩ ሰው ናቸው። ከ1970ዎቹ ጀምሮ አንጃነት እንዴት በትግል ድርጅቱ ውስጥ እንደተወለደ፣ መሪዎች እና ካድሬዎች ኅብረተሰቡን እንዴት እንደሚከፋፍሉ በዝርዝር አጫወቱን። መሰል ችግሮች የብዙ ብሔሮች ትግል ውስጥ እንደሚፈጠር አስረድተውን የሱማሌ ሕዝብ እና የአረብ ሀገራት ያለፉበትን ችግር ውስጣቸው ኖረው ካዩት ልምድ በመነሳት አካፈሉን።ፖፓለቲካ ውስጥ አንጃነት የሚከሰት መሆኑን ጠቁመው የሕዝቡን አንድነት እንዳያፈርስ ጠንክሮ መሥራት እንደሚጠይቅ መክረውን ተለያየን።

በአጠቃላይ የ2008ቱ መሰነጣጠቅ የትግል ድርጅቱን ከማዳከም ባለፈ በውጪ ያለውን ኅብረተሰባችንን ሕይወት አመሰቃቅሏል። በሌላ በኩል ሕዝቡ ከሁኔታው ተምሮ በፍጥነት አገግሟል። መጀመሪያ በጎጠኝነት ተነሳስቶ ከአንጃዎቹ ጋር በመሰለፍ ይፋለም የነበረው ኅብረተሰብ የአንጃዎቹ መሪዎች ወደ ጎጣቸው የተመለሱት ለሕዝቡ ትግል አስበው ሳይሆን በሥልጣን ግጭት እና ፉክክር እንደሆነ ተረዳ። ተራርቀው የነበሩ ሰዎች በሂደት ማኅበራዊ ዝግጅቶች ላይ አብረው መታደም ጀመሩ። የአንጃዎቹ ጎራ ባዶ እየሆነ ቤተ አምነቶች፡የሲቪክ ማኅበራት፣ ሰርግ እና የሙዚቃ ትርዒት በሰዎች ወደ መሞላት ተመለሱ። ሕዝቡን ከፖለቲካ አንጃዎች ይልቅ በሲቪክ ማኅበራት በማደራጀት ውጤታቸው በግልጽ የሚታዩ ፕሮጀክቶች ላይ ማሳተፍ በመቻሉ፣ የአንጃዎቹ ተሰሚነት አሽቆለቆለ።

በ2006ቱ የOSA ስብሰባ ላይ ሰለ ጎጠኝነት መንስኤ እና አደጋዎቹ ሳቀርብ አንዳንድ ሰዎች የሌለን ችግር እንደማሟረት ሲመለከቱት፤ ሌሎቹ ውስጣዊ ምሥጢር እንዳጋለጥኩ አድርገው ቆጠሩት። የአንድ ብሔር ብዝኀነት የሚስተናገድበት ሰልት እና ሰትራቴጂዎች ላይ ለወጣቶች ሥልጠና ስሰጥ «የወጣቶቹን አእምሮ መረዝከው› በማለት የሚራገሙ ብዙ ነበሩ።

ነገር ግን በ2008 የኦነግ መሰንጠቅ ኅብረተሰቡ ላይ ያደረሰው አደጋ ከታየ በኋላ ብዙ ሰዎች በጎጠኝነት ላይ በግልጽ ማውራት አስፈላጊ መሆኑን እያመኑ መጡ። በተለያዩ ከተሞች እየተጋበዝኩ ስለጉዳዩ ማሰተማር ሥራዬ ሆነ። ስለ ጎጠኝነት የምርምር ጽሑፍ በማቅረብ የጀመረው የOSA ተሳትፎዬ በዚያው ቀጥሎ፡ እ.አ.አ. በ2014 የተቋሙ ፕሬዝዳንት ሆኜ ለማገልገል በቃሁ።

በስታንፎርድ ቆይታዬ ቁጥራቸው ያነሰ ኢትዮጵያውያን ተማሪዎች ቢኖሩም፣ ለፖለቲካ ያላቸው ፍላጎትም ሆነ ግንዛቤ እምብዛም ስለሆነ ብዙም አላገኛቸውም። ለምሳሌ አንድ አባቷ በ60ዎቹ የፖለቲካ እንቅስቃሴ ውስጥ ያለፈ ተማሪ ነበረች። ማንነቷን ካወኩኝ በኋላ ስለአባቷ ለዋራት ስሞክር የአኔኑ ያህል እንደምታውቅ፣ ለማወቅም ፍላጎት እንደሌላት ተረዳሁ።

ከተማሪዎች ይልቅ በዩኒቨርሲቲው እና በአካባቢው የሚሰሩ ሰዎች የተሻለ የፓለቲካ ፍላጎች ስለነበራቸው ከእነሱ ጋር መወያየት መረጥኩ። ከእነሱ ውስጥ በአባቱ አርመናዊ ከሆነው ዳዊት ሃይጋዝ ጋር ተዋውቀን በመቀራረባችን ስለኢትዮጵያ እንወያይ ነበር። ኋላ ላይ አበበ ገላው የሚባል ጋዜጠኛ ዩኒቨርሲቲው የአጭር ጊዜ ፌሎውሺፕ ሰጥቶት ሰለመጣ ተቀላቀለን። አበራ መታፈሪያ የሚባል በዩኒቨርሲቲው ሆሰፒታል የሚሰራ እንዲሁም በአካባቢው ባለ ኮሌጅ መምህር የሆነው ዶ/ር ወርቁ ነጋሾ እና ባለቤቱን አካትተን "Standford Ethiopian Group" በሚል ስያሜ የውይይት ቡድን አቋቋምን። በየጊዜው እየተገናኘንም ስለኢትዮጵያ

እንወያይ ነበር። በተለይ ስለኦሮሞ የፖለቲካ አመለካከት የመረዳት ፍላጎት ስለነበራቸው፣ ታሪካዊ አመጣጡን፣ በወቅቱ ያለበትን ደረጃ እና የወደፊት አቅጣጫውን አስረዳቸው ነበር።

በቅርባችን ባለችው ሳን ጆሴ ከተማ የሚኖሩ ሰዎች፣ በኢትዮጵያ እና በኤርትራ መካከል የነበረውን ግጭት ለመፍታት እየሞከሩ ስለነበረ የኛን ቡድን እንቅስቃሴ ሰምተው እንድንሳተፍ ጋበዙን።

ኃላ ላይ በተዘጋጀው ስብሰባ ላይም እንድናገር ተጋብገር የሁለቱን ሀገሮች ግጭት ታሪካዊ አመጣጥ በመዳሰስ የወደፊት መፍትሔ የሚጠቁም ጽሑፍ አቀረብኩ።13 የጽሑፉ ጭብጥም ከድሮ ጀምሮ በኢትዮጵያ እና በኤርትራ ውስጥ የሚንቀሳቀሱ የፓለቲካ ኃይሎች፣ የረጅም ጊዜ የጋራ ዓላማ ማሳካትን ያማከለ ትብብር ከመፍጠር ይልቅ፣ ባላንጣን ለመጣል የሚረዳ ጊዜያዊ ቅንጅት ማስቀደማቸው ዘላቂ ሰላም ለማምጣት ጋሬጣ እንደሆነ ያትታል። ይህ ስለሆነ፡ የኤርትራ እንዲሁም የኢትዮጵያ ተቃዋሚዎች እና የመብት ተሟጋቾች፣ ከአንዱ ሀገር አምባገነን ጋር ወግነው ሌላውን ለመጣል ከመሞከር ይልቅ፣ በሁለቱም ሀገሮች ዴሞክራሲያዊ ሥርዓት እንዲመጣ በጋራ መታገል እንደሚሻል ይመክራል።

ከ"Stanford Ethiopian Group" የውይይት ቡድን አባላት ጋር የነበረኝ ውይይት፣ የኦርሞን ትግል ምክንያት እና ዓላማ በተቻለ መልኩ ለሌሎች ለማስረዳት የረዳኝና ጥሩ ተሞክሮ ያዳበርኩበት አጋጣሚ ነው።

# 5.7.የኦነግ ትችት

ቀደም ባሉት ምዕራፎች ውስጥ እንደጠቀስኩት ከልጅነቴ በኦነግ ለሚመራው ትግል ቅርበት ነበረኝ። በተወሰነ ደረጃም ተሳትፌያለሁ። ዕድሜዬ እና ግንዛቤዬ እየጎለበተ ሲሄድ አንዳንድ የድርጅቱ ስትራቴጂዎች እና አሠራሮች ጥያቄ ይጭሩብኝ ጀመር። በተለይ ድርጅቱ ካለው የሕዝብ ድጋፍ ጋር የተመጣጠነ ውጤት ማስገኘት አለመቻሉ ይከነክነኝ ገባ። ሆኖም እንደ አብዛኛው የኦሮሞ ተወላጅ ኦነግ አንድ ቀን ከችግሮቹ ተላቅቆ ነጻ ያወጣናል የሚል ተስፋ ነበረኝ።

ሲንጋፖር እያለሁ የድርጅቱ አመራሮች እና ልሂቃን የሚከራከሩበትን የኢሜል ቡደን (listsery) ተቀላቅዬ ያየሁት ንትርክ ቅስሜን ሰበረው። በስማቸው ስንመካ የነበሩ መሪዎች የማይመጥናቸውን ነገር ሲጽፉ በማየቴ፡ ድርጅቱ በአንጃ ፖለቲካ ተጠልፎ መሽመድመዱን ተገነዘብኩ። ሀገር ቤት ያለው ሕዝባችን እነዚያ አመራሮች ነጻ ያወጡኛል ብሎ መጠበቁ የአቅሙን ያህል እንዳይፍጨረጨር እንዳደረገው ገባኝ። ስለዚህም ከተቻለ ኦነግን ከወደቀበት ድርጅታዊ ቀውስ በአስቸኳይ ማላቀቅ፡ ካልሆነም የኦሮሞን ትግል ከዚህ ድርጅት መዳፍ ፈልቅቆ ማውጣት አስፈላጊ ስለመሆኑ ጠንካራ አምነት ሰንቄ ወደ አሜሪካ አቀናሁ። እዚያ ስደርስ ይህን ሐሳብ በግልጽ ከማራመድ ይልቅ ውስጥ ውስጡን መሥራት መረጥኩ። ወጣቶችን በማደራጀች ሥራ መጀመሬም የዚህ እቅድ አካል ነበር። በሂደት ግን ድርጅቱን በግልጽ ወደ መተቸት ተሻገርኩ።

እ.አ.አ. በ2009 የአራተኛ ዓመት የዩኒቨርሲቲ ትምህርቴን ለማጠናቀቅ በዝግጅት ላይ እያለሁ በኦነግ የሚመራው ትግል የገጠመውን ቀውሰ እና ምክንያቶቹን የሚተነትን ረጅም መጣጥፍ አቀረብኩ። «Failure : The Journey of the Oromo Liberation Front in the Last Two Decades»[14] የሚል ርዕሰ ነበረው። ለጽሑፉ መንሻ የሆነኝ ባለፉት አራት ዓመታት በፖለቲካ ሳይንሰዕ ዲፓርትመንት ስማራቸው የነበሩ የብዙ ሀገራት የብሔር ንቅናቄዎች እንዲሁም የትጥቅ ትግል ድርጅቶች ጥናት (case study) የሰጠኝ ግንዛቤ ነው። ከፍል ውስጥ እና በንባብ ያገኘሁትን ትምህርት ለሁለት ተከታታይ ክረምት (summer) ወደ ኢትዮጵያ በመመላለስ ከቀድሞ የኦነግ አባላት እና ደጋፊዎች ጋር ቃለ-ምልልስ በማድረግ እንዲሁም ከኦነግ ጋር በተደረገ ጦርነት ውስጥ የተሳተፉ የኦሕዴድ/ ኢሕአዴግ ባለሥልጣናትን በማናገር አዳበርኩት።

በውጭ ሀገራትም የድርጅቱን አንጋፋ ምሁራን እና ባለሥልጣናት በማናገር ተጨማሪ መረጃ አሰባሰብኩ። ጽሑፉን መጀመሪያ ያዘጋጀሁት እየወሰድኩት ለነበረው ኮርሰ እንደ ተርም ፔፐር (term paper) ነው።

14 Mohammed, Jawar ''Failure to Deliver the jouney of the oromo liberation front In the last two decades'' Opride , 29 july 2009, www. Opride.com/2009/07/29/

Failure to- deliver-the journey of-the oromo-libretion-front-in the-last-two-decades/

ሴሚስተሩ ካለቀ በኋላ ለተወሰኑ ሰዎች ስልክላቸው ቢታተም ጥሩ እንደሆነ ሲነግሩኝኮኮርስ ጥናቴ ውስጥ የነበሩትን ሐሳቦች ጨምቄ ለሕዝብ ንባብ በሚመች መልኩ ለማቅረብ ወሰንኩ። ከዚያም ለአንዳንድ የኦሮሞ ምሁራን በመላክ ለሕዝብ ከማቅረቤ በፊት ሐሳባቸውን እንዲሰጡበት ጠየኳቸው።

አብዛኞቹ ምሁራን የጽሑፉን ይዘት ቢወዱትም ኦነግን በዚያ መልኩ መተቸቴ ለፐሮፓጋንዳ እንደሚያጋልጠኝና ለወደፊት የፖለቲካ ሕይወቴም ጥሩ እንዳልሆነ ነግረውኝ እንዳለሰትመው መከሩኝ። በዘመኑ አንዱን እንጃ ደግፎ ሌላውን መርገም የተለመደ ቢሆንም የኦነግን ዓላማ፣ ስትራቴጂ እና ስልት አይደለም መተቸት ጥያቄ ማንሳት ለከፍተኛ የፐሮፓጋንዳ ዘመቻ ስለሚያጋልጥ የምሁራኑ ሥጋት ልክ ነበር። ከጹሑፉ በፊትም ቢሆን የኦሮሞ ጥናት ማህበር (Oromo Studies Association - OSA) ስብሰባ ላይ እና በተለያዩ መድረኮች በማቀርባቸው ሐሳቦች በድርጅቱ ካድሬዎች ዘንድ ስሜ በጥሩ አይነሳም።

አሁን በረጅም ጽሑፍ ትችቴን በቀጥታ ለሕዝብ ማቅረብ ለበለጠ ዘመቻ እንደሚያጋልጠን ጠብቄ ነበር። እንደዚያም ሆኖ በኦነግ የሚመራውን የኦሮሞ ነጻነት ትግል ያዳከክሙችን ምክንያቶች ተንትኜ በጽሑፍ መልክ ለውይይት ማቅረብ መፍትሔ ያመጣለ ብዬ አበክሬ በማመኔ የምሁራኑን ምክር ወደ ጎን ብይ ለመለጠፍ ወሰንኩ። የጽሑፉ ጭብጥ ለኦነግ መከፋፈል እና መዳከም ዋና ምክንያት ባለፉት ሀያ ዓመታት ውስጥ ያጋጠመው ድርጅታዊ ውጤት-አልባነት (organizational ineffectiveness) መሆኑን ያስረዳል። ይህንን የመከራከሪያ ነጥብ የንግድ ኩባኒያን አንደ ምሳሌ በመጠቀም ለማሳየት ሞከርኩ።

አንድ የንግድ ድርጅት ለተቋቋመለት ዓላማ ትርፍ እያስገኘ ከሆነ ባለድርሻ አካላት (shareholders) ስለሚደሰቱ ተሳትፏቸውም ይጨምራል፣ አዳዲስ ባለድርሻዎችንም ወደ ድርጅቱ ይሳባሉ። ይህም ድርጅቱ የሚያስፈልጉትን የገንዘብ፣ የሰው ኃይል እና የሞራል ግብዓቶች ለማሳደግ ዕድል ከፋች ነው።

የግብዓት መጨመር ድርጅቱ የበለጠ እንዲያድግ እና ትርፉ ከዓመት ወደ ዓመት እንዲመነደግ ያሰችላል። እንዲህ ዓይነቱ ሁኔታ ሲከሰት ድርጅቱ የምርታማነት ዑደት ውስጥ ገባ እንላለን። በሌላ አነጋገር የድርጅቱ ውጤታማ መሆን ተጨማሪ ግብዓትን፣ ተጨማሪ ግብዓት ደግሞ የበለጠ ትርፍ ያመጣል ማለት ነው። ትርፋማ ድርጅት ባለድርሻዎችን ደስተኛ በማድረግ በኩባኒያው አመራር ላይ ያላቸው አመኔታ እና ድጋፍ እንዲያድግ ያስችላል።

በአንጻሩ አንድ ድርጅት የታሰበውን ያሀል ትርፋማ መሆን ካቃተው ባለድርሻ አካላት የድርጅቱን የወደፊት ዕጣ ፈንታ ስለሚጠራጠሩ ተጨማሪ ሼር ከመግዛት ይቆጠባሉ። ስለሆነም ድርጅቱን የግብንት እጥረት ያጋጥመዋል፣ በሚቀጥለው ዓመት በቂ ትርፍ እንዳያገኝም ያደርገዋል። ያለውን አዝማሚያ ያጤኑ ባለድርሻ አባላት ተጨማሪ ኢንቨሰዕትመንት ከመስጠት ይልቅ ያላቸውንም ወደ ማስወጣት ይሸጋገራሉ። ሁኔታው ለጥቂት ዓመታት በዚህ መልኩ ከቀጠለ ድርጅቱ ላይ ከትርፍ ይልቅ ኪሳራ መከተሉ አይቀሬ ነው። ከዓመት ዓመት ትርፋማ መሆን አለመቻል ኩባኒያውን የኪሳራ አዙሪት ውስጥ በማስገባት ወደ ተቋማዊ መሽመድመድ (organizational paralysis) ያመራል። እዚያ ደረጃ ላይ የደረሰ ድርጅት ተመልሶ ትርፍ የማግኘት ዕድሉ በጣም ጠባብ ነው።

በተመሳሳይ መልኩ የፖለቲካ ድርጅት ከጊዜ ወደ ጊዜ እያደገ እና ዓላማውን ከግብ ለማድረስ እየተቃረበ ካልሄደ ደጋፊዎቹ በአመራሩ ላይ ያላቸው እምነት ይቀንሳል፤ ደጋፋቸውም ያሽቆለቁላል። ከድጋፍ ይልቅ ትችት ሲበረታ በከፍተኛ አመራሩ መካከል ለመጣው ውድቀት ጣት መቀሳሰር ይጀመርና አንጃነት ይፈጠራል። ጽሑፉ ኦነግን ያጋጠመው እንዲሀ ዓይነት ችግር እንደሆነ በማተት ይጀምራል።

ጽሑፉ የዳሰሰው ሌላው ጉዳይ ኦነግ ውጤታማ ሊሆን ያልቻለበቸው ዋና ምክንያቶች የተበላሸ ድርጅታዊ ባሕል እና በውጭ አካላት ላይ ጥገኛ መሆኑ (external dependency)እንደሆነ ይጠቁማል። ድርጅታዊ ባሕል ስንል በከፍተኛ አመራሩ ውስጥ እንዲሁም በአመራሩ እና በአባላቱ መካከል ያለ ግንኙነት፣ የድርጅት ሥራ የሚመዘንበት መለኪያ፣ ውስጣዊ እና ውጫዊ ችግሮች ሲከሰቱ እና የተለያዩ ጉድለቶች ሲሰተዋሉ መፍትሔ የሚፈለግበትን መንገድ የሚያካትት ነው። የኦነግ ድርጅታዊ ባሕል ከሦስት ምንጮች የሚቀዳ እንደሆነ ጽሑፉ ያስቀምጣል። እነዚሀም የኢትዮጵያ ተማሪዎች ንቅናቄ፣ ኮሚኒዝም/ሰታሊኒዝም እና የአቢሲኒያ ፖለቲካ ናቸው።

ኦነግ ከኢትዮጵያ የተማሪዎች ንቅናቄ ውስጥ ከፈለቁ ድርጅቶች አንዱ ነው። የ1960ዎቹ የተማሪዎች ንቅናቄ ከዚያ በፊት የፖለቲካ ውይይት ባልነበረበት ወይም ባልተለመደበት እና የፖለቲካ ምሀዳሩን አፍኖ ይኖር የነበረ አምባገነናዊ ሥርዓት ባለበት ሁኔታ የተፈጠረ ነው። መጀመሪያ ላይ ጥሩ ውይይቶች ይካሄዱበት የነበረ ቢሆንም በሂደት ግን መካረር፡ መፈራረጅ እና የሜራ ትንተና የንቅናቄው ባሕል እየሆኑ ሄዱ። ይሀም ተማሪዎቹ በዚያ የታዳጊነት ዕድሜ (formative age) አቋምን ማክረር፡ ሜረኛነት እና የአንጃ (factionalism) ፖለቲካን እንዲለማመዱ አደረጋቸው። የወቅቱ ተማሪዎች ቀጥሎ የተወለዱ የፖለቲካ ድርጅቶችን በአመራርነት ሲቆጣጠሩ በተማሪዎች ንቅናቄ ውስጥ ያዳበሩትን የፖለቲካ ባሕል ወደ ተቀላቀሏቸው ፓርቲዎች ይዘው መጡ። ከእነዚሀ ድርጅቶች ውስጥ አንዱ ኦነግ ነው።

ኦነግ በተወለደበት ዘመን ኮሚኒዝም ዓለም ላይ ናኝቶ ለነጻነት በሚደረግ ትግል ውስጥ ተመራጩ ርዕዮተ ዓለም ሆኖ ነበር። እውነትም ኮሚኒዝም እንደ ሐሳብ በተለይ ለጭቁን ብሔሮች እና መደቦች ማራኪ ነው። በሀብታሞች እና በደሆች መካከል ያለውን መበላለጥ በማውገዝ ለሁሉም ሰው አኩልነት ይሟንገታል። ይሀ ደግሞ የብሔር እና የመደብ ጭቆና በደረሰባቸው የሕብረተሰብ ክፍሎች ዘንድ አማላይ እንዲሆን አድርጎታል። በተጨባጭ ሥራ ላይ ሲውል ግን ድርጅቶችን ለአምባንነንነት እና ለአንጀነት ባሕርይ ሲያጋልጣቸው ተስተውሏል። ይሀ የኮሚኒዝም ጉድለት አንደ ሌኒን እና ሮዛ ሉክሰምበርግ ባሉ ቀደምት መሰራቾች መካከል ከፍተኛ ክርክር የተደረገበት ጉዳይ ነው።

በተለይ በኢትዮጵያ ተማሪዎች ንቅናቄ ውስጥ ሲቀነቀን የነበረው የዮሴፍ ስታሊን ኮሚኒዝም ከፖለቲካ ርዕዮተ-ዓለም ይልቅ ለሀይማኖታዊ ቀኖና ይቀርባል። በፖለቲካ ውስጥ ትክክለኛው እና ጥርት ያለው መንገድ አንድ ብቻ ነው ብሎ ስለሚያስቀምጥ ለሐሳብ ልዩነት ቦታ የለውም።

የሐሳብ ልዩነትን እንደ ድክመት እና የትግል እንቅፋት ስለሚመለከት የተለየ ሐሳብ ያላቸውን ሰዎች እና ቡድኖች በጠላትነት ይፈርጃል። ውጤታማነት የሚመነጨው ከድርጅታዊ አንድነት፣ ድርጅታዊ አንድነት ደግሞ ከርዕዮተ-ዓለማዊ ጥራት (deological purity) እንደሆነ ሰለሚታሰብ የተለየ እና ወጣ ያለ አመለካከት (diverse and divergent views) ማስተናገድ እንደ አደጋ ይቆጠራል።

ይህ በተራው ለፍጹም አምባገነናዊነት (totalitarianism) በር ይከፍታል። ከዚህ የተነሳ የኮሚኒዝም/ስታሊኒዝም ርዕየተ-ዓለምን ይዘው የተነሱ ደርጅቶች በአመራራቸው ፈላጭ ቆራጭነት ብሎም ወደ አንጃነት በማምራት ይታወቃሉ።

በ1960ዎቹ የበቀሉ እና በኮሚኒዝም/ስታሊኒዝም የተቀረጹ የኢትዮጵያ የፖለቲካ ድርጅቶችን የመሩ ሰዎች፣ ብዙ ጊዜ ችችቶችን አዳምጠው ድክመታቸውን እና ስሕተታቸውን ገምግመው ከማረም ይልቅ ለትችት ጆሯቸውን የደፈኑ፡ በጥርጣሪ እና በሀሜት ላይ በመመሥረት ተቺዎችን በጠላትነት ፈርጀው ማዕወገድን የሚመርጡ ነበሩ። በዚሀ መንገድ ተቺዎችን በማሰወገድ የተሳካለት መሪ ድርጅቱ ላይ ፍጹም አምባገነናዊነትን ማስፈን ይችል ይሆናል። ነገር ግን ብዙ ጊዜ ተቺዎችን ሙሉ በሙሉ ማስወገድ ስለማይቻል ድርጅቱ በውስጣዊ ሽኩቻ መዳከሙ፡ በሂደትም በአንጃ መከፋፈሉ አይቀርም።

ኦነግ ገና ከውልደቱ የወረሰው አደገኛ ድርጅታዊ ባሕል የሰሜን/የአቢሲኒያ ነገስታት የፖለቲካ ባሕል ነው። የአቢሲኒያ ንጉሣዊ የፓለቲካ ባሕል መሠረቱ ከሀይማኖት/ከመለኮት ጋር የተሳሰረ (thecracy) ሲሆን፣ ሥልጣን ከሰማይ እንደተሰጠ ይቆጠራል። "ንጉሥ አይከሰሰ ሰማይ አይታረሰ በሚለው ነባር አባባል እንደተገለጸው፡ ከበታች ያለው ሹምም ሆነ ሕዝቡ የመታዘዝ ግደታ እንጂ የመጠየቅ መብት የለውም። መሪ አይሳሳትም፡ ከተሳሳተም አይተችም የሚል እሳቤ አለው። በ1960ዎቹ/70ዎቹ ዓ.ም ውስጥ የተፈጠሩ የፓለቲካ ድርጅቶች ምንም እንኳን በንጉሣዊው ሥርዓት ላይ በማመጽ ቢመሠረቱም የአቢሲኒያን ንጉሣዊ የፖለቲካ ባሕል በተወሰነ መልኩ ከመላመድ ማምለጥ አልቻሉም።

በአጠቃላይ ኦነግ አንጃነትን (factionalism) ከተማሪዎች እንቅስቃሴ፡ ፍጹማዊነትን (absolutism) እና አምባንነንነትን (totalitarianism) ከኮሚኒዝም፣ እንዲሁም ተዋረዳዊ (hierarchical) የውሳኔ እና የትዕዛዝ ባሕልን ከአቢሲኒያ ንጉሦች ወርሷል። እዚህን የፖለቲካ ባሕሎች መውረሱ በራሱ ለድርጅቱ ውጤታማ አለማሆን በቂ ምክንያቶች አይደሉም። እንዲያውም በትጥቅ ትግል ላይ የተመሠረተ የፓለቲካ ድርጅት ለሚፈልገው የተማከለ ወታደራዊ አመራር፣ የዕዝ ሰንሰለት እና ጥብቅ ምሥጢራዊነት ጠቃሚ ሊሆኑ ይችላሉ። ታዲያ ለኦነግ ሲሆን ለምን ከጥቅሙ ጉዳቱ አመዘነ ለሚለው ጥያቄ መልሱ ድርጅቱ የተቀበለው የፖለቲካ ባሕል እና አደራጅቶ ሊያታግለው የተነሳው ማኅበረሰብ (constituency) ባሕል ለየቅል መሆናቸው ነው።

የኦሮሞ ሕዝብ ከገዳ ሥርዓት በወረሰው የፓለቲካ ባሕል የተነሳ በእኩልነት የሚያምን (egalitarian) ነው። ውሳኔዎች የውይይት ውጤት በመሆናቸው ከላይ በሚወርድ ቾዕዛዝ ላይ አይመሰረቱም። ሥልጣንም በሕዝብ ይሁንታ የሚመጣ እንጂ ከፈጣሪ እንደወረደ አይታይም። ኦነግ እንደዚሀ ዓይነት የፖለቲካ ባሕል ባለው ማኅበረሰብ ላይ የሐሳብ ፍጹማዊነት እና አምባገነናዊ የውሳኔ አሰጣጥን ለመተግበር ሞከረ። ይሀም ውስጣዊ ተቃርኖን በመፍጠር፣ ድርጅቱ የሚያጋጥሙትን ውጫዊ እና ውስጣዊ ችግሮች ተረጋግቶ በመገምገም፣ ድክመቱን እያረመ እና ጠንካራ ጎኖቹን ይበልጥ እያጠናከረ መሄድ እንዳይችል አድርገው ድርጅታዊ ውጤታማነት (organizational efficiency) አሳጡት። ለዚሀ ነጥብ ጥሩ ማስረጃ የሚሆነው ልክ አንደ ኦነግ ከላይ የተዘረዘሩትን ድርጅታዊ ባሕሎች የወረሱ ድርጅቶች፡ ለምሳሌ ሕወሓት እና ሻዕቢያ ክኦነግ የተሻለ ውጤት ማስመዝገብ የቻሉት ድርጅታዊ እና ማኅበራዊ መሠረታቸው በአብዛኛው ተመጋጋቢ በመሆኑ ነው።

ኦነግ የሚጠበቅበትን ውጤት ማምጣት ያልቻለበት ሌላው ምክንያት አመራሩ ከሚታገልለት ማኅበረሰብ እና መልክዓ ምድር ተነጥሎ በውጭ ኃይሎች ላይ ጥገኛ መሆኑ ነው። ጽሑፉን በፃፍኩበት ወቅት ኦነግ በኤርትራ መንግሥት እና በዲያስፖራው ላይ ጥገኛ ሆኖ ነበር። የድርጅቱ ገቢ እና እርዳታ በአብዛኛው ከውጭ ማኅበረሰብ የሚገኝ ሲሆን፣ አመራሩ ከትግል ሜዳ ርቆ ይገኛል። ይሀም ከድርጅቱ የሚጠበቀው እና አመራሩ የሚፈልገው እንዲቃረኑ አደረገ። አመራሩ ከሚታገልለት ኅብረተሰብ እና ከትግል ሜዳ መራቁ ሊደርስበት የሚችለውን የቀን ተቀን ጫና ሊቀንስለት ቢችልም፡ ተዋጊዎቹ እና ሕዝቡ መሥዋዕትነት ለመክፈል ያላቸውን ሞራል ግን ያወርደዋል።

ጦርነት በዓለም ላይ ከተጀመረ አንሰቶ ወታደራዊ ቴክኖሎጂ ከጊዜ ወደ ጊዜ እየረቀቀ ሄዷል። በእጅ እና በድንጋይ ከመደባደብ አንስቶ በኒውክሊየር እስከ መተላለቅ ደርሷል። ከድሮ ጀምሮ ያልተለወጠ ነገር ቢኖር፣ አንድን ጦርነት ለማሸነፍ የወታደር ስሜት እና ሞራል ያለቸው ሚና ነው። ከሺህ ዓመታት በፊት እና ባለንበት በህያ አንደኛው ክ/ዘመን ወታደሮች አመራር እና አዛዥ መህከለቸው ካለ በቆራጥነት ይዋጋሉ። ምክንያቱም አመራሮች እንደ ሌሎቹ ወታደርች በጦር ሜዳ መገኘታቸው ራሳቸውን ለመሥዋዕትነት ማቅረባቸውን ስለሚያሳይ የወታደርቹን ሞራል ያነሳሳል፤ የአመራሮች በአካል መገኘት ወታደሮች መክከዳትም ሆነ ማፈግፈግን እንዳያስቡ ያደርጋል።

በትጥቅ ትግል ውስጥ በአካል ጦር ሜዳ ያሉ አመራሮች ለራሳቸው ነፍስ ሳይቀር በወታደሮቹ እና በአካባቢው ኅብረተሰብ ላይ ጥገኛ ይሆናሉ። የራሳቸውን ነብሰ ከጠላት አደጋ ለመከላከል ወታደሮቹን በሚገባ ማደራጀት እና በድፍረት ማዋጋት ግዴታቸው ነው። በተጨማሪም ወታደሮቹ የሚያስፈልጋቸውን ትጥቅ እና ስንቅ ማሟላት አለባቸው። አነዚህን ሊያገኙ የሚችሉት ከኅብረተሰቡ በመሆኑ ድጋፉ ቀጣይነት እንዲኖረው ኅብረተሰቡ ነገ ጠላትን አሸንፈው ነጻ ያወጡናል ብሎ ተስፋ ማድረግ አለበት። ተስፋው እንዲተጥል ከጊዜ ወደ ጊዜ ድርጅቱ ድል ሲያደርግ ማየት አለባቸው። አማጺዎችን በመደገፋቸው ከመንግሥት ሊደርሰባቸው ከሚችል ጥቃት አመራሩ እና ድርጅቱ ሊከላከልላቸው ወይም ሊበቀልላቸው እንደሚችል ሊተማመኑ ይገባል። ለዚህ ማሰተማመኛ የሚሆነው በተጨባጭ ሊታይ የሚችል ወታደራዊ እርምጃ ሲኖር ነው። ስለሆነም የኦነግ አመራር ከትግል ሜዳ በመራቁ ወታደራዊ ድል የማግኘት ዕድሉ እየተመናመነ ሄደ።

በተጨማሪም የኦነግ አመራር ከትግል ሜዳ መራቁ ከሀገር ወስጥ የሚገኘው ገቢ እንዲደርቅ እና በዲያስፓራው ላይ የበለጠ ጥገኛ እንዲሆን አድርጎታል። ዲያስፖራው የሕዝቡን ትግል በሙሉ ልቡ የሚደግፍ መሆኑ ጥርጥር የለውም። አብዛኞቹ በደረሰባቸው ግፍ ከሀገር ስለተሰደዱ ትግሉን ለመደገፍ ከፍተኛ ፍላጎት አላቸው። በውጪ ሀገር ያለ እና በሀገር ውስጥ ያለ ሰው ለትግል የሚገፋፋበት ምክንያት ይለያያል። የሀገር ውስጡ የትግል ስሜቱ የሚመነጨው በራሱ ላይ በቀጥታ ከሚደርስ በደል ወይም የሌሎችን ስቃይ በአካል ከማየት ነው። ውጪ ያለው ግን በሌሎች ወገኖቹ ላይ የሚፈጸመውን ግድያ፣ እስራት እና ዘረፋ በመሰማት ከሚመጣ ርሀራኄ(empathy) ይመነጫል። በተጨማሪም ውጪ የሚኖሩ ሰዎች የመረጃ ምንጫቸው ያዩት ሳይሆን ከሌሎች የሚደርሳቸው ዘገባ ስለሆነ ግንዛቤያቸው የተዛባ የመሆን ዕድሉ ሰፊ ነው፡ የሚኖራቸው የፖለቲካ አመለካከትም ከሀገር ቤቱ ሰው ጋር ሲነጻጸር የከረረ ነው።

ከትግል ሜና የራቀ ድርጅት ግንዛቤው በተዛባ እና አመለካከቱ በከረረ የዲያስፖራ ማኅበረሰብ ለይ ጥገኛ ይሆናል ማለት ነው።

እንድ ስትራቴጂ ውጤታማ የሚሆነው በትክክለኛ መረጃ ላይ ተመስርቶ ሲነደፍ ነው። ከትግል ሜዳ ነባራዊ ሁኔታ ይልቅ ውጭ ሀገር ባሉ ሰዎች አመለካከት እና ስሜት የሚመራ ስትራቴጂ እና ፖለቲካዊ ውሳኔ መሬት ላይ ተገቢውን ውጤት አያመጣም።

በአጠቃላይ በጽሑፉ ወሰጥ ኦነግ ገና ከውልደቱ ጀምሮ የወረሰውድርጅታዊ ባሕል፡ ከ1990ዎቹ ወዲህ አመራሩ ከትግል ሜዳ መራቁ እና በውጢ ኃይሎች ላይ ጥገኛ መሆኑ የድርጅቱን ውጤታማነት ከጊዜ ወደ ጊዜ እያያከመው እንደመጣ ለማሳየት ሞከርኩ። ይህም ድርጅቱን በአንዳ የመከፋፈል አዙሪት ውስጥ እንደከተተውና አሁን ባለበት ሁኔታ ሊታከም በማይችል ደረጃ መጎዳቱን በጽሑፌ ውስጥ አጽንዖት ሰጥቼ ለማሳየት ሞከርኩ። በጽሑፉ ድምዳሜ ላይ የቀደመው ትውልድ ትግሉን ከመጀመር አንስቶ ብዙ ውጤት ቢያመጣም አዲሱ ትውልድ የእነሱን አደረጃጀት እና ስትራቴጂ የመከተል ግደታ እንደሌለበት ጠቆምኩ። የተዳከመውን ትግል አጠናክረን ታሪክ ለመሥራት፡ አዲስ አስተሳሰብ እና ስትራቲጂ ማዘጋጀት የእኛ ትውልድ መብት እና ግደታ መሆኑን ተከራከርኩ። ለዚሀም እንደ ማስረጃ በአሜሪካ የነጻነት ትግል ወስጥ ስመጥር የሆነውን የቶማስ ፔይን (Thomas Paine) አባባል “Rights of Man " ከተሰኘ መጽሐፉ ውስጥ ተዋሰኩ።

«Every age and generation must be as free to act for itself in all cases as the ages and generations which preceded it. The vanity and presumption of governing beyond the  Grave is the most ridiculous and insolent of all tyrannies. Man has no property in man ;neither Has any generation a property in the generations which are to follow›› «እያንዳንዱ ዘመን እና ትውልድ፣ አንደቀደመው ዘመን እና ትውለድ ሁሉ፣ ለራሱ የሚቆምበት ነጻነት ሊኖረው ይገባል። በአጽም የመግዛት ከንቱ ምኞት እና ትምክህት፣ ከጭቆናዎች ሁሉ ቂላቂሉ እና አስነዋሪው ነው። ሰው በሰው ላይ ባለቤትነት የለውም፣ የትኛውም ትውልድም በማያስከትላቸው ትውልዶች ላይ ባለቤትነት የለውም››

የኦነግን ትችት የጻፍኩት ለሦሰት ዓላማ ነው። የመጀመርያው፡ እኔ ራሴ በኦነግ የተቀረጽኩ እንደመሆኔ ነጻነት ከሱ ውጪ አይመጣም ብዬ ዓይነን ጨፍኜ፤ ስራመድ ቆይቻለሁ። በሂደት ድርጅቱ አስፈላጊውን ውጤት ማምጣት አቅቶት ከጊዜ ወደ ጊዜ እየተዳከመ እና እየተበታተነ መሄዱ ሞራሌን እየሰባበረው መጣ። ትምሀርት ቤት ባካበትኩት ግንዛቤ እና ከአንጋፋ ታጋዮች ጣገኘታት መረጃ ላይ በመመሥረት፣ ይሀንን ድርጅት ያዳከሙትን ምክንያቶች ተረድቼ መፍትሔ ለመፈለግ አእምሮዬን ማሳመን ነበረብኝ።

ሁለተኛው ምክንያቴ፣ በወቅቱ ውጪ ያለው ማኅበረሰብ ወጣት ሽማግሌ ሳይል ነጻነትን ከኦነግ ብቻ ይጠብቅ ስለነበር የድርጅቱ መዳከም እና ከድል መራቅ ቅስሙን ሰብሮታል። በተቻለ መጠን ትግሉ የሚፋጠንበትን አማራጭ ከመፈለግ ይልቅ የኦነግ አንጃዎችን እና አመራሩን በማማት/በመተቸት ጊዜውን ያባዘናል። ስለሆነም በኦነግ የሚመራውን ትግል አገር ተወርቾ ያሰሩን ችግሮች አጥንቼ ሚዛናዊ በሆነ መልኩ በጽሑፍ በማቅረብ፣ ሕዝቡ በተለይ ደግሞ የእኔ ትውልድ ኦነግን በመጠበቅ ፈንታ አማራጭ መፍትሔ ለመፈለግ አእምሯችንን ክፍት ሊያደርግ ይችላል ብዬ ተሰፋፉ አደረኩ።

ሦስተኛው፣ በወቅቱ የኦነግ አመራሮች፣ አባላት እና አንጃዎች ድርጅቱ ላጋጠሙት ችግሮች ተረጋግተው በማጥናት እና በመምከር መፍትሔ ከመፈለግ ይልቅ መካሰስ፣ መወጋገዝ እና መቋሰል ላይ ተሰማርተው ነበር። ይህ ደግሞ ችግሩን ከመፍታት ይልቅ ይበልጥ አወሳሰቦ ድርጅቱንም እያዳያከመው ሄደ። በድርድቱ ችግሮች ላይ ግንዛቤዬን ሚዛናዊ በሆነ መልኩ ተንትኜ ባቀርብ፣ ምናልባት ከተራ ግለሰባዊ እና አንጃዊ ንትርክ ወጥተው፣ ድርጅቱን ያዳከሙትን መዋቅራዊ እና ስትራቴጂካዊ ምክንያቶች ወደ መገምገም ያመራሉ የሚል ተስፋ አደረብኝ። በተጨማሪም ከእኔ የተለየ መደምደሚያ ላይ ቢደርሱ እንኳን ድርጅታቸውን ወደፊት ማራመድ የሚችሉበትን ሌሎች ሰልቶች እንዲከተሉ የመነሻ ሐሳብ ለማበርከት በመፈልጌ ነበር።

አስቀድሜ ያወያየኋቸው ምሁራን እንደፈሩልኝ ጽሑፉ መታተሙ ሰፊ ለሆነ የስም ማጥፋት ዘመቻ ዳረገኝ። የአንጃዎቹ ካድሬዎች እና ደጋፊዎች እርስ በእርስ የሚያደርጉትን ሽኩቻ ለጊዜው ገታ አድርገው በጋራ ተረባረቡብኝ።

ከዚያ በፊት ስለ ኦነግ የሚጽፉ ወይም የሚናገሩ ሰዎች እንዱን እንጃ መደገፍ፣ ተቃራኒውን አመራር እና ተጠያቂ ማድረግ ላይ አተኩረው ስለነበር የእኔ ኦነግን በጅምላ መተቸት እንዲተባበሩ አደረጋቸው። «ጀዋር ይህን የፃፈው የጠላት ተልዕኮ ወዕዶ ኦሮሞ ያለውን አንድ ተቋም ለማፍረስ ነው።» በማለት ረገሙኝ። ዘመቻ ከከቱብኝ ውስጥ አንድ ሰው የፃፈውን አሰካሁን አስታውሳለሁ። «እኔ ጃዋርን አውቀዋለሁ። በደርግ ዘመን የአብዮት ጥበቃ[15] አባል ነበር፤ ብዙ ኦሮሞዎችን አስፈጅቷል» በማለት አንድ የኢሜል ቡድን ለይ ፃፈ። በቀይ "ብር ዘመን ሕዝብ ላይ ወንጀል ልፈፅም ቀርቶ ወደዚህች ምድር እንኳን እንዳልመጣሁ ለማሳየት የልደት ማስረጃ Birth [Certificate] ለጥፌ ላኩለት።

በኢንተርኔት የሚደረግብኝ ዘመማቻ ቢጧጧፍም፣ ውስጥ ውስጡን ግን የኦነግ መሪዎችን ጨምር ብዙ ሰዎች ጽሑፌን እንዳነበቡት እና ባነሳኋቸው አብዛኞቹ ነጥቦች ባይሰማሙም ደፍሬ መጻፌ ጥልቅ ውይይት ለማድረግ በር የሚከፍት እንደሆነ ይነግሩኛል። ጽሑፉ ኦሮሞ ባልሆኑ ሰዎች ዘንድም በስፋት በመነበቡ ብዙ መልሶች የተለያዩ ድረ-ገፃች ላይ ሲፃፉ ነበር። ለእኔ ጽሑፍ መልስ ከሰጡት መካከል እንዱ ፕሮፌሰር መሳይ ከበደ ናቸው። ፕሮፌሰሩ በኢትዮጵያ ጉዳዮች ላይ በስፋት ስለሚጽፉ እና ተሰሚነታቸውም ከፍ ያለ ታዋቂ ምሁር ስለሆኑ ጽሑፌ ለይ ላቀረቡት ችችት መልስ መስጠት አስፈላጊ ሆኖ ታየኝ። ፕሮፌሰሩም ለመልሴ ምላሽ ስለሰጡ ደጋግመን በመመላለስ ተከራክረናል። ፕሮፌሰሩ የኦነግ ውጤታማ አለመሆን ዋና ምክንያት አንግቦ የተነሳው የፖለቲካ ዓላማ ነው በሚል ሲከራከሩ፡ የእኔ መልስ ደግሞ ከኦነግ ጋር ተመሳሳይ ፖለቲካ የሚያራምዱ እንደ ሕወሓት እና ሻዕቢያ ያሉ ድርጅቶች ውጤታማ መሆናቸው ችግሩ የፖለቲካ ዓላማ አንዳልሆነ ማሳያ ነው የሚል ነበር።

በእኔ እና በፕሮፌሰር መሳይ መካከል የነበረው ክርክር ቀድሞ ኦነግን በመተቸቴ ተደስተው የነበሩ ቡድኖችን አስቀየመ። ምክንያቱም ዱሮውንም የኦነግን ዓላማ ስለሚጠሉ የእኔ ትችት ከእነሱ አቋም ጋር የገጠመ ስለመሰላቸውና ለፕሮፌሰሩ በሰጠሁት መልስ ላይ ከኦነግ ዓላማ ችግር አንደሌለኝ ስለተረዱ ነው። ኦነግን በመተቸቴ ተቀይመው የነበሩ ኦሮሞዎች ደግሞ ከፕሮፌሰሩ ጋር በነበረን ክርክር ግንዛቤ ስላገኙ ሐሳቤ የበለጠ ግልጽ ሆነላቸው።

15 አብየት ጥበቃ በቀይ ሽብር ዘመን ሰው ሲጋዴሉ የነበሩ የደረግ ሚሊሻዎች ናቸው።

በአጠቃላይ ኦነግ ላይ የፃፍኩት ጽሑፍ በኦሮሞ እና በኢትዮጵያ ፖለቲካ ላይ ሐሳቤን በግልጽ ለሕዝብ ማቅረብ የጀመርኩበት ነው። ከኦነግ ቡድኖች ጋርም ለረጅም ጊዜ የቆየ ውዝግብ ውስጥ ከቶኛል። በተጨማሪም የእኛ ትውልድ የኦሮሞን ትግል ከዳር ለማድረስ፣ በብዙ ችግሮች የተተበተበ እና ክፉኛ የተጎዳን ድርጅት ከመጠበቅ ይልቅ አዲስ መፍትሔ መፈለግ እንዳለበት ራሴንም ሆነ ሌሎችን ማሳመን የጀመርኩበት ነው።

# 5.8. ጋብቻ

ለእናቴ ብቸኛ ወንድ ልጅ ስለሆንኩ ለአቅመ አዳም እንደ ደረሰኩ አግብቼ አያት እንዳደርጋት ምኞት ነበራት። ታላላቅ አሀቶቹም ከጥሩ ቤተሰብ የተወለደች ቀንጆ ልጃገረድ ባጋጠማቸው ቁጥር ለትዳር እንዳጫት ሊያሳምኑኝ ሞክረዋል። በአካባቢያችን በልጅነት ማግባት እና መዳር ከመለመዱም የተነሳ አብዛኞቹ አብሮ አደጎቼ የሁለተኛ ደረጃ ትምህርታቸውን እንኳን ለመጨረስ አልታደሉም። ይሀ የልጅነት ጋብቻ በሴቶች ላይ ስለሚከፋ፣ የመጀመሪያ ደረጃ አብረን ከተማርነው ሴቶች ውስጥ ሁለተኛ ደረጃን ማጠናቀቅ የቻሉት ሁለት ብቻ ነበሩ።

እኔም ከስምንተኛ ክፍል ተባርሬ ወደ ሸርሻ ሰመለሰ ዕድሜዬ ለትዳር ባይደርሰም በሐሳቤ ግን ማቀዴ አልቀረም። ጠንክሬ ሰርቼ አንድ ጥማድ በሬ፣ አምስት ጎተራ የበቆሎ ራስ፣ ሦስት ጉድጓድ ማሽላ፣ ሠላሳ እርከን ቡና እና ጫት ሲኖረኝ ቆንድዬ ሚስቶ ጥሎሽ ጥዬ ሳገባ በሐሳብ ይታየኛል። በኋለ ግን ዕድል ወደ ትምህርት መልሳኝ የግብርና ሕይወቴ በመንገድ ላይ ሲቀር ለማግባት የነበረኝ ዕቅድም ታጎለ።

ከሲንጋፖር ስመለስ የጋብቻ ሐሳብ ተመልሶ መጣ። ከሀገር ሳልወጣ በፊት ፍቅረኛዬ የነበረች ልጅ ከሁለት ዓመት በኋለ ስመለስ ከቤተሰቦቼ ጋር ተዋውቃ ጠበቀችን። ቤተሰቦቼ አንዴ በቀጥታ፡ ሌላ ጊዜ በንደኛቼ በኩል አንዳጫትቸ ሲወተወቱኝ ተሰማምቼ ታጨች። አሜሪካ ሄጄ በዓመቱ ተመልሼ ስንገናኝ ባሕሪያችን በአጅጉ ስለተራራቀ ለመግባባት የተወሰነ ሙከራ አድርገን እንደማይሰራ ስናውቅ ተለያየን።

አሜሪካ ሄጄ የኦሮሞ ወጣቶች አመራር ኮንፈረንስ ማቀናጀት ስጀምር ካገኙን የመጀመሪያ ስዎች አንዷ አርፋሴ ገመዳ ነበረች። ቀደም ባለው ምዕራፍ ውሰዋ አንደገለጽኩት ለሰብሰባው ስዘጋጅ በነበረበት ወቅት ለበረራ የምከፍለው ገንዘብ ስላልነበረኝ አርፋሴ ከምትሠራበት የአየር መንገድ ኩባንያ ባላት ነጻ የአየር ትኬት ካሊፎርኒያ መጥታ ትወስደኛለች። ተማሪዎች እና ወጣቶችን ለረጅም ጊዜ በማደራጀት አውቅና እና ልምድ ሰለጎነበራት በስልክም ሆነ በአካል በመገናኘት አብረን ስለምንሠራ ቅርርባችን ጠነከረ። ሆኖም ፍቅር ውስጥ መግባት የትግል ሥራችንን አንዳይጎዳ ስለሠጋን ስሜታችንን ከመከተል ተቆጠብን።

እ.አ.አ. ዲሴምበር 2005 ተዋውቀን ከሁለት ዓመታት በላይ በቅርበት አብረን ከሠራን በኋላ ለስሜታችን ተሸነፍን። አንድ ምሽት ለሥራ ጉዳይ ተደዋውለን ሰናወራ፣ ከዚህ በላይ መደባበቅ እኛን ብቻ ሳይሆን ለሕዝባችን በጋራ እየሰራን ያለነውን ሥራ ሰለሚጎዳ ፍቅራችንን አውጥተን ለመናገር ወሰንን። ግንኙነታችንን ወደ ፍቅር ለማሸጋገር ብንስማማም ሥራችን አንዳይጎዳ በምሥጢር ለመያዝ ተስማማን። ከተገናኘን ጊዜ ጀምሮ ብዙ አብረን ስለምንታይ ግንኙነታችን ወደ ፍቅር ማደጉን የጠረጠረ አልነበረም።

በ2008 ክረምት ለምርምር (research) ወደ ኢትዮጵያ ስመጣ አርፋሴም ቤተሰብ ለመጠየቅ መጣች። አብረውን ከመጡት ጓደኞቻችን ኦብሳ ሐሰን እና መገርሳ ጋር በመሆን

ሐረር እና ድሬዳዋን ጎበኘን። እኔ እና አርፋሴ ለብቻችን በረና ሄደን አያቷን ጠየቅናቸው። አንድ ቀን ዱቡሉቅ ወደምትባል ገበያ ጎራ ስንል፣ ከገበያተኞቹ ውስጥ የተወሰኑት ወደእኛ እየተመለከቱ ስለእኛ ሲያወሩ ሰማን። አንዱ አዛውንት «ልጅቷ የእኛ ትመስላለች፡ ይሄን ከየት አመጣችውን» አሉ። ወደ አዛውንቱ ጠጋ ብዬ እኔም የእናንተው ነኝ, ስላቸው ደንግጠው «እንዴ አፋን በረና ይናገራል?» ብለው ሳቅ አሉ። ተዋውቀን ማውራት ስንጀምር የትውልድ የታዩን በያዝኩት ካርታ map) ላይ አሳየኋቸው። አዛውንቱም «አዚያም የቦርና ሀገር ነው?› ብለው ጠየቁኝ። «አዎ› አልኳቸው።

በእኔ እና በአርፋሴ መካባል ያለው ግንኙነት ምን እንደሆነ ሲጠይቁኝ እጮኛዬ እንደሆነች እና ፈቃድ ለመጠየቅ በረናዎች ጋር እንደመጣሁ ነገርኳቸው። ጎሳዬን ጠይቀውኝ አርሲ መሆንን ስነግራቸው ጥሉሽ መጣል አለብህ ሲሉኝ ችግር እንደሌለው አረጋገጥኩለቸው። ስንት መጣል አንዳለብኝ ስጠይቃቸው «መቶ ከብት› አሉኝ። አንዲቀንሱልኝ ለምኛቸው በሃምሳ ተስማማን። ከብቶቹ የት አንዳሉ ሲጠይቁኝ ቤተሰቦቹ ያሉበትን በያዝኩት ካርታ ላይ አሳይቼ ሄደው መውሰድ አንደሚችሉ ነገርኳቸው። ርቀቱ ምን ያሀል ነው ሲሉኝ ደርሶ መልስ አንድ ወር ይፈጃል አልኳቸውን። «ከብቶቹ ሠላሳ ቀን ሄደው ከነነፍሳቸው አዚሀ ስለማይደርሱ ብር ስጠን› ብለው ቀልደው ተለያየን።

በሀገራችን እና በዓለም ላይ ብዙ ብዓዝም እንደ በረና የዋሀ ሕዝብ አላየሁም። የዋሀነታቸውን ኮሚያሳዩ ነገሮች አንዱ የሕዝብ ማመላለሻ መኪና ውስጥ ያጋጠመኝን አልረሳም። አርፋሴ የሕዝቤን ኑሮ ማየት አለብኝ ስላለች መኪና መከራየት ትተን በሕዝብ ትራንሰፖርት ተጓዝን። አንድ ቀን ከዱቡሉቅ ገበያ ወደ ያቤሉ ለመሄድ አውቶቡስ ተሳፈርን። መኪናው ሞልቶ መሄድ ሲደምር የሆኑ ሰዎች ከኋላ መኪናው ላይ ለመድረሰ ሲፖሯጡ አየን። ሾፌሩ መንዳት ሲቀጥል ውስጥ ያሉ ተሳፋሪዎች የሚሮጡት አስኪደርሱ ድረስ ለመጠበቅ አሰቆሙት። ሁኔታው አሰገርሞኝ አጠገቤ የተቀመጠውን ሰው መኪናው ላይ ለመድረስ የሚርጡትን ታውቋቸኋላችሁ ስለው «አናውቃቸውምጋ አለኝ። ታዲያ ለምን አስቆማችሁ ስለው «አንድን በረና ደጅ ትተን እኛ አንዴት ወደቢታችን አንገባለን?› አለኝ በጥያቄዬ መገረሙን በሚገልጽ እይታ።

ኮቃላ ሲሮጡ የነበሩት ሰዎች ደርሰው ወደ መኪናው ሲገቡ ሁሉም መቀመጫዎች ተይዘው መኪናው ሞልቷል። ቀድመው የነበሩት እየተጠጉ አሰቀመጧቸው። እቃቸውን በፌስታል የያዙ አንድ አዛውንት መጡና «እግርሀን አውሰኝ› አሉኝ። ምን ማለት አንደፈለጉ አልገባኝም። እኔ እና አርፋሴ ለሁለት ሰው በተዘጋጀ ወንበር ላይ ሶስተኛ ሰው ጨምረን ከዳር ላይ ቁጭ ብዬ ነበር። «አግርሀን አውሰኝ› ያሉት ሽማግሌ መልሴን ሳይጠብቁ ጉልበቴ ላይ ፋጭ አሉ። ዞር ብዬ ሳይ ሌሎችም በተመሳሳይ መልኩ ሰው ጉልበት ላይ ተቀምጠዋል። ግማሽ መንገድ እንደሄደን «አሁን ደግሞ አኔ በተራዬ ጉልበትሀ ላይ ልቀመጥ› አልኳቸው። «አንተ ወፍራም ነህ እግሬን ከሰበርከውስ?› ብለው ስቀው ጥያቄዬ አውነት መስሏቸው ሊቀይሩኝ ሲሉ ቀልዴን መሆኑን ንገርኳቸው። በተፈሂርኩባቸው የኢትዮጵያ ክፍሎችም ሆነ በሌሎች ሀገራት ተሳፋሪዎች ሾፌሩ ትርፍ አንዳይጭን ሲቆጡ እንጂ ተጨማሪ ተሳፋሪ እንዲያስገባ ሲጠብቁ አይቼ አላውቅም።

ከአርፋሴ ጋር ከቦርና ወደ ፊንፊኔ ከተመለስን በኋላ አንድ ቀን ከንደኞቼ ጋር አየተጨዋወትን ጥሎሽ ስለጠየቁኝ የቦረና ሽማግሌ አየነገርኳቸው ሳለ አንዱ ጓደኛዬ «‹አንዴ አጮኛህ ናትለካ?»

ብሎ ጠየቀኝ። እኔም እንደ ቀልድ አድርጌ ተንበርክኬ እንድታገባኝ ሰጠይቃት እየቀለደች እሺ አለች። በሚቀጥሉት ቀናት እንደ ዋዛ ያወራነው ነገር ላይ ተነጋግረን ለመጋባት ወሥነን ከቤተሰቦቼ ጋር አስተዋወኳት።

አሜሪካ ከተመለስን በኋላ ከሚቀርቡን ጥቂት ሰዎች በስተቀር የፍቅር ግንኙነታችንን ማንም አያውቅም። በዚህ ምክንያት ብዙ ወንዶች አጠገቧ ሆነ ሊያሽኮረምሟት ይሞክሩ ነበር። ከስታንደርድ ተመርቄ ዋሽንግተን ከተማ እየሠራሁ እያለ ከዚህ በላይ በድብቅ ፍቅር መቆየት ስለማይቻልና ለቤተሰቦቿ ክብር ስንል ሽማግሌ ለመላክ ወሰንን። በስብሰባ ቦታ የማውቃቸውን ሽማሌዎች አነጋግሬ ላኳቸው። ዶ/ር አብዱሰመድ ሙሐመድ (የሰዋሰው ምሁር) የሽምግልናውን ጉዳይ አቀላጠፈልን፤ ብዙ ሽማግሌዎች ወላጆቿን ከኬንያ ጀምሮ ያውቁ ስለነበር የሽምግልናው ጉዳይ ቀላል ሆነ።

አንድ አዛውንት አርፋሴንም ሆነ ቤተሰቧን በቅርበት ስለማያውቁ ወላጆቿ ቤት ሽምግልና ላይ እያሉ በመሀል ወጣ ብለው ደውለው «ልጅቷ አስለም ናት ወይ ክርሰቲያን?» አሉን። እኔም ቆይ አንዴላጣራ ስልኩን አትዝጉት ብዬ ለአርፋሴ ደወልኩና መሰመሩ ላይ ቀላቅያት «አርፉሴ እስለም ነሽ ወይስ ክርሰቲያን?» ብዬ ጠየኳት። እሷም «አብድ ዛሬ ነው የምትጠይቀኝ?» ስትለኝ ሽማግሌውም «አናንተ ጉደኞኛች ናችሁ!» ብለው ስልኩን ዘግተው ወደ ሽምግልናው ተመለሱ።

ሰርግ የመደገስ ፍላጎት ስላልነበረን በቀለበት ሥን-ሥርዓት ለመጋበት ወሰንን። ለካ ለደግሱ የሚጋበዙ ስዎች ቁጥር ከተወሰነ በኋላ ሁለቱ ተጋቢዎች ድርሻቸው ላይ ተደራድረው ይካፈላሉ። በዚህ መሠረት አሀቷ ስንት ሰው መጋበዝ እንደምፈልግ ጠየቀችኝ። አሜሪካ ውስጥ ዘመድ ስለሌለኝ እና ሁሉም ቅደኛቹ ለአርፋሴም ንደኛች ስለሆኑ እሷ መጥራቷ አይቀርምና ፣እኔ መጋበዝ ስለማያሰፈልገኝ የእኔ ድርሻ ዜሮ እንደሆነ ነገርኳት።

በዚያን ጊዜ ዋሽንግተን ዲሲ ያለኝ ሥራ ስለሚበዛ ቀኑ ሳላስበው ደረሰና በችኮላ ትኬት ገዝቼ ወደ ሚኒሶታ ከነፍኩ። ስጣደፍ ለቀለበቱ ቀን ያዘጋጀሁትን ሱፍ ረሰቼ ሄድኩ። ማለዳ አዚያ ስደርስ ልብሱ የለም፣ ለንደኛይ ቂጤሶ ጭሪ ደውዬ ሥነገረው ወዲያው ሄዶ አንድ ሱፍ (Tuxed) ተከራየልኝ።

ፕርግራሙ ደርሶ ወደ አዳራሽ ስንገባ ሌለ ችግር ተፈጠረ፡ ሚዜ አላዘጋጀሁም ነበር። ብቻዬን ስገባ ያዩ ሰዎች የሚዜዎቹስ ሲሉን ነበር ያሰታወሰኩት። ዞር ሰል ቂጤሶ እና ደሜን ስላየሁ ጠራኋቸውና አዚያው ሚዜ አድርጌያቸው ወደ መድረክ ወጣን።

በፕሮግራሙ ላይ ሽማግሌዎች ተነስተው ስለሙሽሮቹ አወሩ። በቅድሚያ የተናገሩት የቦረና ሽማግሌ ናቸው። ሙሽሪትን አሞጋግሰው ከልጅነት እስከ እውቀት ያለው ታሪኳ ምንም ሳይቀራቸው አውርተው ሲጨርሱ «ልጁንም ስብሰባ ላይ እናውቀዋለን ጥሩ ይመስላል› ብለው አበቁ።

የወለጋ ሽማግሌዎችም በተመሳሳይ ሁኔታ ከአያቷ ታሪክ አንስተው ካወደሷቸ በኋላ «ልጁ በማንነቱ ኩሩ እንደሆነ አናውቃለን፡ ወደፊት የበለጠ እንተዋወቃለን»» አሉ። የሐረር እና የአርሲ ሰዎችም ለእሷ መወድስ ሲያሰሙ ውለው እኔን እንደነገሩ አለፉኝ። በዚህ ጊዜ እጀን አውጥቼ የምናገረው አለኝ አልኳቸው። መድረክ መሪው መጥቶ «ምን መናገር ፈለክን?» ሲለኝ

ሁሉም ሰው የሚያወድሰው ሙሽሪትን ብቻ ነው፡ እኔም ራሴን አንዳሞግእ ዕድል ይሰጠኝ» ሰለው ሣቀና ባሕሉ አይፈቅድም አለኝ። የሁሉም አካባቢ ፣ማግገሌዎች ስለ አርፋሴ ተናግረው የእኔን የተዉት ለክፋት ሳይሆን እሷን ከኬንያ ጀምሮ ከልጅነቷ ስለሚያውቋት ሲሆን፣ አኔን ግን በፓለቲካ መድረክ ካልሆነ በግል ስለማያውቁኝ ነበር። አርፋሴ

የተወለደችው በናይሮቢ ኬንያ ሲሆን፣ የቤተሰቦቿ ቤት የኦርሞ ስደተኞች የሚያርፉበት ማዕከል ነበር። በ1980ዎቹ ናይሮቢን የረገጡ ቤተሰቧን የማያውቅ ስደተኛ የለም። ቤተሰቧ ወደ አሜሪካ ከተሰደዱ በኋላም በሲቪክ ማኅበራት ውስጥ ጠንካራ ተሳትፎ ያደርጉ ስለነበር ሽማግሌዎቹ አርፋሴን ከልጅነቷ ጀምሮ ያውቋታል። እኔን ግን ሠለቲካ መድረክ ላይ አዩኝ እንጂ ስለ ግል ኑሮይም ሆነ የጀርባ ታሪኬ የሚያውቁት ነገር አልነበረም። ስለሆነም ስለ አእኔ አሳጥረው ማለፍን የመረጡት ለክፋት አልነበረም።

ከዩኒቨርሲቲ ከተመረቅኩ በኋላ ወደ ዋሽንግተን ዲሲ ሄጄ ስሰራ የነበረውን የሥራ ልምምድ (Intership) እንደጨረሰኩ ወደ ሚኒሶታ ሄጀ ከአርፋሴ ጋር መኖር ጀመርን። እዚያ አንድ ዓመት ከኖርን በኋላ ኮሎምቢያ ዩኒቨርሲቲ ለመማር ወደ ኒው ዮርክ ተዛወርን። ኒው ዮርክ ለሦስት ዓመት (2011-2014) ከኖርን በኋለ OMN ( oromia media network-OMN ሰለተቋቋመ ወደ ሚኒሶታ ተመለስን።

አርፋሴ በኒው ዮርክ የኮሎምቢያ ዩኒቨርሲቲ አሥተዳደር ውስጥ ጥሩ ሥራ ቢኖራትም ተራርቀን እንድንኖር ስላልፈለገች ትታ መጣች። ሚኒሶታ ስንገባ OMNን መምራት እና #Oromoprotests ማሰተባበር ብዙ ጊዜ የሚወሰድ ሥራ ነበር። ለወ ገንዘብ ለማሰባሰብ በሳምንቱ መጨረሻ ሁሌ ወደ ሌሎች ከተሞች እጓዛለሁ። ሚኒሶታ ባለሁበት ቀናትም ቢሮ ውስጥ ነው የምኖረው ማለት ይቻላል። ይሀ ትዳራችን ላይ ከፍተኛ ተጽዕኖ አያሳደረ መጣ። በዚያ ከባድ ሁኔታ ውስጥ አርፋሴ አረገዘች። አንድ ቀን አልትራሳውንድ ተነሰታ ደቶውን ወንበሬ ላይ ስላሰቀመጠች ከውጪ ስገባ አይቼ ሰው ታሞ ራጅ X-RAY) የተነሳ ስለመሰለኝ አዚያው መልሼ «ማነው የታመመው ስላት የምቀልድ መስሏት ተናደደች። በኋላ ንደኛይ ቂጤሰን ጠይቄ ማወቅ ቻልኩ።

አርግዝናው ወንድ መሆኑን አንዳወቅን ስሙን ማን አንበለው እያልን ስንወያይ በፌሰቡክ ለጥፈን ሕዝቡ እንዲመርጥልን ለመጋበዝ ተስማማን። በ24 ሰዓታት ውስጥ ከሀያ ሽ በላይ ስዎች የስም ጥቆማዎችን አደረሱን። ብዙዎቹ የተለያዩ ባሕላዊ ስሞችን ሲሷልኩልንየአንዳንዶቹ ጥቆማ ግን አሥቂኝ ነበር። በወቅቱ ሲሰየሙ ከነበሩ አሥቂኝ ሰሞች መካከል ጥቂቶቹ አባይ ፀሐዬ፣ ምኒሊክ፣ ማሰተር ፐለን ወዘተ አሉበት። አነዚህ ስሞች ያኔ ደጋግሜ ፌሰታዙክ ላይ የምለጥፋቸው ስለነበሩ እኔን መደገራቸው ነበር። ከተጠቆሙልን ስሞች መካከል አንዱን መምረጥ ስለከበደን ኦሮሞ ብለን ልንሰይመው ተስማማን። ለዚሀ ሁለት ምክንያቶች ነበሩን። የመደመሪያው በፌሰቡክ የሰም አወጣጥ ብዙ ኦሮሞዎች ስለተሳተፉ አንዱን ስም ወሰደን እንዱን ማስደሰት እና ሌላውን ማስከፋት ስላልፈለግን ሲሆን፣ ሁለተኛው ልጁ የተለያዩየኦርሞ ጎሳዎች ደም እንዳለበት ለመጠቆም ነው።

የአርፋሴ አባት ከወለጋ ሲሆን፣ ትውልዱ ጨሊያ ነው። አናቷ የማጋ አካባቢ ቦረና ናት። የእኔ አባት አርሲ ሲሆን፣ እናቴ ቱለማ ናት። ይሀንን ድብልቅ ማንነት ለማሳየት ልጃችንን ኦሮሞ ብለን ሰየምነው። ኦሮሞ (ልጃችን) የተወለደው ጁላይ 29 ቀን 2016 (ሐምሌ 22/2008 ዓ.ም) ነው።

አርፋሴ በትዳር ሕይወታችን ውስጥ በምንም ሊተመን የማይችል ትልቅ መሥዋዕትነትከፍላለች። ለትምሀርት ወደ ኒው ዮርክ ስገባ ከአኔ ጋር ለመሄድ ሚኒሶታ የነበራትን ጥሩ ሥራ ለቃለች። እዚያም ሌላ ጥሩ ሥራ አግኝታ እያለ OMNን ለመምራት ወደ ሚኒሶታ ስዛወር ከጎኔ ለመሆን ተመልሳ መጣች። በወቅቱ በተለያዩ ቡድኖች እና ግለሰቦች ይደረግብን የነበረው የዕም ማጥፋት ዘመቻ በአሷም ላይ መደገሙ በጣም ያበሳጨን ነበር። አሁንም ድረስ የማስታውሰው

ከOMN ጋር ተያይዞ እኔ ላይ ሲዘመት፣ እሷ የOMNን ገንዘብ ለግል ጥቅሟ እንዳዋለች ተደርጎም የተነዛው ስም ማጥፋት ነው። በተለይ የሐሰት ወሬውን ሲያካሄዱ የነበሩት አርፋሴን ከልጅነቷ ጀምሮ ከማወቅም በላይ ከገንዘብ ጋር ምንም ንክኪ እንደሌላት በቅርበት የሚያውቁ ሰዎች መሆናቸው ነው።

ሌለው ከሀይማኖት ጋር ተያይዞ የሚነዛብን የጥላቻ ዘመቻ ነው። አንዳንድ ሰዎች የተለያየ ሀይማኖት ተከታይ ሆነን መጋባታችንን በመቃወም ስሜት የሚነኩ ትንኮሳዎችን በኢንተርኔት ይለጥፉ ነበር። እኔና አርፋሴ ለመጋባት ስንወስን የሀይማኖት ጉዳይ ሁለታችንንም አላሳሰበንም። ከሚያስተሳሰረን ኦሮሞነት እና ብሔርተኝነት በተጨማሪ ሁለታችንም የተወለድነው እና ያደግነው የሁለት ሀይማኖቶች ቅይጥ ከሆኑ ቤተሰቦች በመሆኑ የሀይማኖት ልዩነትን በተገቢው መንገድ በማሰተናገድ በሥራም ሆነ በትዳራችን ላይ ተጽዕኖ እንዳይኖረው አድርገናል። በዚህ ምክንያት ሰዎች በማኅበራዊ ሚድያ ላይ ሲነዙብን የነበረውን ሀሜት እና ነቀፌታ ሁሉ መቋቋም ችለናል።

በቁሮ ትግል ወቅት የነበረው ውጥረት እና ጭንቀት ከአርፋሴ ጋር ባለኝ ግንኙነት ላይ ከፍተኛ ተጽዕኖ አሳድሯል። ሕይወቴ ኮምፒዩተር እና ቢሮ መሆኑ በአካል እና በመንፈሰ እያራራቀን መጣ። ለውጡ ሲመጣ አኔ ወደ ሀገር መመለሴ ችግሩን አባባሰውና ትዳራችንን ለማዳን የነበረንን ዕድል አጨለመው። ትዳራችን ባይቀጥልም ለአርፋሴ ያለኝ ክብር አንድም ቀን አልተለወጠም። ከተዋወቅን ቀን ጀምሮ ታማኝነት፣ መከባበር፡ ብሰለት፣ ርሀራሄ እና በራስ መተማመን የማይለወጡ የማንነቷ መገለጫዎች ነበሩ። በነበርኩባቸው ክፉ የውጥረትና የጭንቀት ዘመናት አሷ ከጎኔ መሆኗ ሚዛኔን ለመጠበቅ ወስን ነበር።

ትውስታ በምስል #2




ሲንጋፖር የመጀመሪያዎቹ የትምህርት ክፈለ ጊዜያት።

ሲንጋፖር እያለሁ የትምህርት ቤቱ የመረብ ኳስ ቡድን አባል ነበርኩኝ



ታይላንድ በበጎ አድራጎት ሳስተምራቸው ከነበሩ ሕጻናት ጋር።

ከክፍል ጓደኞቼ ጋር ለመስክ ጥናት ወደ ታይላንድ በሄድንበት ወቅት።



UN Nights በሚባል የባህል ምሽት ላይ የኦሮሞን ጭፈራ ስናሳይ።



ከሁለት ዓመታት የUWCSEA ትምህርት በኋላ የምረቃ ዲፕሎማዬን ከትምህርት ቤቱ ዳይሬክተር ስቀበል፣ ጁን 2005።



የምረቃዬ እለት የአፋን ኦሮሞ ሰልፍቶውት (self taught) መምህሬ ከነበሩት ሚስተር ኬቪን ሞርሊ ጋር።



የምረቃዬ እለት ቤተሰቦች መሳተፍ ስላልቻሉ ከግዮን ሸዋንግዛው ቤተሰቤን ተክቶ አስመረቀኝ። ለምርቃት ሱፍ እንደሚለበስ አላውቅም ነበርና በመጨረሻው ሰዓት ግዮን የገዛልኝን ለብሼ እታያለሁ።



ሲንጋፖር እያለሁ ገንዘብ አሰባስቤ ሳስተምራቸው ከነበርኩት ወላጅ አልባ ሕጻናት በተራድዖ ድርጅት የተዘጋጀውን ደብተር ሳበረክት።



የምረቃችን ምሽት የእራት ግብዣ ላይ ከጓደኞቼ ጋር።

126



ስታንፎርድ የመጀመሪያ አመት ላይ ላርኪን በሚባል ዶርም አብረን ስንኖር ከነበሩ ተመሪዎች ጋር።



ዶርም ውስጥ ጥናት ላይ እያለሁ።




ሁሌም ስለኦሮሞ እናገር ስለነበር በአመቱ መጨረሻ የክፍል ጓደኞቼ Oromummaa የሚል ቲሸርት አሰርተው ሰጡኝ።



ስታንፎርድ ከሌላኛው የኦሮሞ ተማሪ አብዱሰቡር ጀማል እና ሊጠይቀን ከመጣው ቲሾ ጋር።



ስታንፎርድ ሳላሁ ለአንድ ሴሚስቴር ወደ ኦክስፎርድ ዩኒቨርሲቲ በሄድኩበት ወቅት።



ስታንፎርድ የምረቃ እለት ከደረጀ ዳዲ ጋር 2009።

127



ከስታንፎርድ ተማሪዎች ጋር የሰላምዊ ትግልን ለማጥናት ወደ ሕንድ በሄድን ወቅት በታጅ መሀል ፊትለፊት።



ሕንድ እና ደቡብ አፍሪካ በሄድኩበት ወቅት የማህትማ ጋንዲን እና ኔልሰን ማንዴላን ሙዚየም በጎበኘሁበት ወቅት።



የኦሮሞ ወጣቶች አመራር ኮንፈረንስ (OYLC) ተሳታፊዎች በOSFNA ላይ ዝግጅት ስናቀርብ 2006።



OSFNA ንግግር ስናደርግ 2006።




የተቃውሞ ሰልፍ ላይ ወጣቶች የIOYA ባነር ይዘው።



ዕውቁን የቦረና ባህል ምሁር ደበሳ ጉዮን OYLC ላይ በጋበዝንበት ወቅት።




IOYA በዋሽንግተን ዲሲ ባዘጋጀው ሰላማዊ ሰልፍ ላይ ወደኋላ "Ethiopia out of Oromia" ብሏል ተብሎ ስወቀስበት የነበረውን ንግግር ሳደርግ።



የኦሮሞ ወጣቶች አመራር ኮንፈረንስ (OYLC) ተሳታፊዎች በከፊል።




የሕዝበ ሙስሊሙን ትግል ለመደገፍ በተዘጋጀ መድረክ ላይ ንግግር ሳደርግ፣ ዋሺንግተን ዲሲ።



ኮሎምቢያ ሳለሁ OMNን ለመመስረት በጥንስስ ሀሳብ ላይ ለመወያየት የተገናኘን ወቅት። ፎቶው ላይ የሚታዩት ትዕግሥት ገሜ፣ ግርማ ታደሰ፣ አብዲ ፊጤ፣ አርፋሴ እና እኔ ስንሆን ፎቶውን ያነሳው ሙሐመድ አደሞ ነበር።



በOromoFirst ዘመቻ ወቅት ካካሄድናቸው ሕዝባዊ ስብሰባዎች አንዱ።



ኮሎምቢያ ዩኒቨርሲቲ ምረቃ እለት ከአርፋሴ ጋር።




የመጀመሪያው የOromo First ዘመቻ ማስታወቂያ (poster)።

130

# ክፍል ስድስት - ዝግጅት

## 6.1 የሰላማዊ ትግል ጥናት

በ2009 ከስታንፎርድ ሰንመረቅ ብዙ ጓደኞቼ ወደ ሥራ ዓለም ወይም ወደ ከፍተኛ ትምህርት (Graduate School) ለመሄድ ወሰኑ። ምኞቴ በሙሉ ጊዜዬ እና አቅሜ ወደ ትግሉ መቀላቀል ስለነበረ ለመሥራት ወይም ለመማር አላሰብኩም። ፍላጎቴ አስከዚያች ዕለት ድረሰ ባፈራሁት አውቀት ወደ ሀገሬ ተመልሼ መሥራት ነበር። በተለይ በኢትዮጵያ የ2002ዓ.ም ምርጫ እየተቃረበ ስለነበር ወደ ሀገር ተመልሼ የኦሮሞ ፓለቲካ ፓርቲዎችን በሰትራቴጂ እና በምርጫ ዘመቻ እያገዝኩ የኢትዮጵያን ፖለቲካ በቅርበት ማጥናት አሰብኩ። ይህን ሐሳብ ኮሚቀርቡኝ የኦሮሞ ምሁራን ጋር ስወያይበት በወቅቱ ምርጫውን ለማገዝ ወደ ሀገር መመለሰ ብዙም ውጤት እንደማያመጣ ነገሩኝ። በተለይ የታሪክ ምሁር እናበመኢሶን አባልነቱ ለዓመታት ታስሮ የነበረው አቶ ብዙወርቅ ባላ በዚያን ጊዜ ወደ ኢትዮጵያ መመለስ ጠቃሚ አንዳልሆነ ረጅም ጊዜ ወሰዶ ምክንያቶችን በማቅረብ ሊያሳምነኝ ሞከረ።

በስታንፎርድ ዩኒቨርሲቲ አማካሪዬ ፕሮፌሰር ሌሪ ዳይመንድ (Larry Diamond) ወደ ኢትዮጵያ መመለስ ልክ አንዳልሆነ ጠቅሶ ሰላማዊ ትግል ለይ የጀመርኩትን ምርምር  አንዳጠናክር መከረኝ። ከዚያም በሰላማዊ ትግል ላይ ሥልጠና እናምርምር የሚያካሄደውን International Center on Nonviolent Conflict (ICNC) የተባለ ተቋም በማናገር ኢንተርንሺፕ አግኝቼ ወደዚያው እንዳቀና ሁኔታዎችን አመቻቸልኝ። ወደ ዋሽንግተን ዲሲ ተዛውሬ ዩኒቨርሲቲ የጀመርኩትን የሰላማዊ ትግል ጥናት ቀጠልኩበት። በዘርፉ ሰፊ ጥናት ያደረጉት ፒተር ሄክርማን (Peter Heckerman) እናጃክ ዱቫል (Jack Duvall) የሚባሉ ምሁራን የተቋሙ መሥራች እና መሪዎች ሲሆኑ በቀጥታ በእነርሱ ሥር ለመማር እና ለመሥራት ዕድል አገኘሁ። ሁለቱ ሰዎች “A Force More Powerful" የሚል መጽሐፍ ደራሲ እና በጉዳዩ ላይ ዓለም አቀፍ አሠልጣኞች ናቸው። የመሠረቱት እናየሚመሩት ተቋም ለብዙ ሀገራት ታጋዮች ሥልጠና የሚሰጥ እናየሥልጠና ቁሳቁሶችንም የሚያበረክት ነው። አኔም ጥናት በማካሄድ እናለስልጠና የሚሆኑ ነገሮችን በማስተባበር አግዛቸው ነበር።

“ICNC” ከሌሎች የሰላማዊ ትግል ተቋማት ጋርም በቅንጅት ለመሥራት ጥሩ አጋጣሚ ሆኖልኛል፡ ከእነዚህ ውስጥ አልበርት አይንስታይን ኢንሰቲትዩት (Albert Einstein Institute) አንዱ ነው። አልበርት አይንሰታይን ኢንሰቲትዩት የተመሠረተው እና የሚመራው በሰላማዊ ትግል ጥናት ፈር ቀዳጅ በመሆን ለዓለም ባሰተዋወቀው ጂን ሻርፐ

(Gene Sharp) የተባለ ምሁር ነው። በወቅቱ ጂን ሻርፕ ዕድሜው በጣም ቢገፋም ጥያቄዎቼን ሰፊ ጊዜ ወስዶ በትዕግሥት ይመልስልኝ ነበር። «From Dictatorship to Democracy» የተሰኘውን ታዋቂ መጽሐፉን ወደ አፋን አርሞ እንድተረጉመው ፈቅዶልኝ ከዶ/ር አብዱሰመድ ሙሐመድ እናያህያ በሽር ጋር ተርጉመን አሳትመናል።

በ"ICNC" ቆይታዬ ከተለያዩ ሀገራት አንቂዎች (Activist) ጋር የመገናኘትና ልምድ የመለዋወጥ አጋጣሚ ነበረኝ። ከአገኘኋቸው ታጋዮች ውስጥ አንዳንዶቹ የአረብ ሀገራትን ባንቀጠቀጠው የአረብ ስፕሪንግ (Arab Spring) ሕዝባዊ እንቅስቃሴ ውስጥ ትልቅ ሚና ተጫውተዋል። ከተዋወቅኳቸው አንቂዎች ውስጥ ብዙ የጠቀሙኝ "Center for Applied Nonviolent Action and Strategies - CANVAS)" የሚባለውን ድርጅት መስርተው ሲመሩ የነበሩት ናቸው። "CANVAS" የተመሠረተው የሰርቢያ አምባገነን መሪ የነበረውን ስሎቦዳን ሚሎሶቪች በሰላማዊ መንገድ ከሥልጣን ባሰወገዱ አንቂዎች ነው። እነርሱም በራሳቸው ልምድ ላይ በመመሥረት የተለያዩ የትግል ሞዴሎችን ሲያዘጋጁ ነበር።

ከICNC ጋር መሥራቴ ሰላማዊ ትግልን በቀጥታ ከተሳተፉ እና ከመሩ ሰዎች መረጃ እናልምድ እንድወስድ ዕድል ሰጥቶኛል። በኋላም ወደ ምሥራቅ አውሮፓ በመሄድ "የቀለም አብዮት" (Color Revolution) የተባለው ሰላማዊ ትግል ያመጣውን ለውጥ ለማየት ረድቶኛል። አነዚያን ሀገራት በመጎብኘት የተረዳሁት ነገር ቢኖር አምባገነናዊ ሥርዓትን ሰላማዊ ትግል መጣል የዴሞክራሲ ግንባታ ጅማሮ አንጂ ፍፃሜ አንዳልሆነ ነው።

እ.አ.አ. ከ2000-2005 ሲካሄድ የቆየው የቀለም አብዮት ብዙ አምባገነናዊ ሥርዓቶችን አስወግዷል። 2010/2011 የምሥራቅ አውሮፓ ሀገራትን ሰጎበኝ የአብዮቱ ፈንጠዝያ (Revolution Euphoria) አልፎ ትግሉ በአዲሰ መልክ የተጀመረበት ነበር። በአምባገነናዊ ሥርዓቶች አግር የተተኩት አዲሶቹ አገዛዞች እንደሚፈለገው የደሞክራሲ ሥርዓት፣ የኢኮኖሚ ዕድገት እናማኅበራዊ ፍትሕ ማምጣት ስላልቻሉ ትግሉ በአዲስ መልክ ተቀጣጠለ።

ከሀገራቱ አንቂዎች ጋር ካደረኩት ውይይት እናበዓይኔ ካየሁት የተረዳሁት፣ ዘላቂ የዴሞክራሲ ሥርዓት ለመመሥረትና ሌሎች ማኅበራዊ ችግሮችን ለመፍታት፤ አምባገነናዊ ሥርዓትን ማስወገድ ብቻውን በቂ አንዳልሆነና ትግል መቀጠሉ ግድ እንደሆነ ነው። አነዚያ ሀገራት አምባገነናዊ ሥርዓትን ገርሰሰው ከጣሉ ጥቂት ዓመታትን ያሰቆጠሩ ቢሆኑም ሥልጣን የያዙ ኃይሎች የሕዝቡን ተሰፋ እያጨለሙት ነበር። አንዳንድ ሀገሮች ውስጥ አዲሰ አምባገነናዊ ሥርዓት ለመገንባት አየሞከሩ ሲሆን፣ በሌሎች ሀገሮች ደግሞ የሙስና እና የወንጀል መስፋፋት ሕዝቡን አሰመርሮት ታዘብኩ። ይህም 'ጉልቻ ቢለዋወጥ ወጥ አያጣፍጥም' የሚል አመለካከት አንዲሰፋፋ በማድረግ ሕዝቡ ለዴሞክራሲያዊ ሥርዓት ያለውን ድጋፍ እንዲቀንስ እያደረገ መሆኑን አየሁ። አንቂዎቹ ሕዝቡን ዳግም ለትግል ለማነሳሳት ሲሞክሩ "የትላንቱ ለውጥ ምን አመጣልን?' በሚል ሐሳብ ማጣጣል የተለመደ ሆነ።

የምሥራቅ አውሮፓ ጉዞዬ ሰላማዊ ትግልን አሰመልክቶ ያሉ ልምዶችን ለማጥናት ብቻ አልነበረም። ቀጠናው በብሔሮች ጥያቄ (Nationalities Questions) ከአንድ ምዕተ-ዓመት በላይ ሲናጥ የቆየና ብዙ ኢምፓየሮች የተበታተኑበት አካባቢ ከመሆኑ አንፃር፤ የኦሮሞን ትግል እና የኢትዮጵያን ዕጣ ፈንታ በንፅፅር ለመገንዘብም ነው። ካነበብኩት

ንድፈ ሐሳቦች በመነሳት፡ በተለይ ዩጎዝላቪያ እና ሶቪየት ኅብረት (Soviet Union/ USSR) የተመሠረቱበትና በኋላም የፈረሱበት ሁኔታ ብዙ ነገር ሊያሰተምሩኝ ይችላል ብዬ ሰላመንኩም ጭምር ነው። እንደገመትኩትም በየሀገራቱ የሚታየው ተገዳዳሪ ብሔርተኝነት (Competing Nationalisms) ጥልቀቱ የት ድረስ እንደሆነ ሰዎችን በአካል አግኝቼ ሳነጋግር የበለጠ ገባኝ። ከሀገራችን ጋር ያለው መመሳሰልም በጣም አሰገራሚ ነው። ለምሳሌ የሰርቦች ብሔርተኝነት ባሕሪ ያኔ አያቆጠቆጠ ከነበረው የአማራ ብሔርተኝነት ጋር፡ የኮሶቮ ደግሞ ከኦሮሞ ጋር በብዙ መልኩ ይመሳሰላል።

በጉብኝቴ መጨረሻ ላይ አእምሮዬ ውስጥ ተደጋግሞ የሚመላለስ አንድ ጥያቄ ነበር። ዩጎዝላቪያ ውስጥ የዮሴፍ ቲቶ መሞት የብሔሮች ግጭት እና የሀገሪቷን መበታተን አስከተለ። አንዲሁም የኮሚኒስት ፓርቲ ውድቀት የሶቪየት ኅብረትን ውድቀት አመጣ።

«ኢትዮጵያ ውስጥ የመለስ ዜናዊ መሞት ወይም ከሥልጣን መወገድ አሊያም የኢሕአዴግ ውድቀት የኢትዮጵያን መበታተን ያስከትል ይሆን? » የሚል ነበር። ይህ ጉዳይ ያሳሰበኝ ኢትዮጵያም እንደ ዩጎዝላቪያ እና ሶቪየት ሕብረት ሁሉ ሕብረ-ብሔራዊ ፌደራሊዝምን ከኮአምባገነናዊ ሥርዓት ጋር አጣምራ አየተገበረች ያለች በመሆኑ ነው።

የዩጎዝላቪያው መሪ ዮሴፍ ቲቶ የብሔር ጥያቄ አንዳይፈነዳ ጉልበት እና ብልኃትን አመዛዝኖ በመጠቀም ቡድኖችን አቻችሎ ያስተዳድር ነበር። በሶቪየት ኅብረት ደግሞ የኮሚኒስቱ ሥርዓት የተለያዩ ብሔሮች ክልል አንዲኖራቸው ፈቅዶ የባሕል እናየቋንቋ መብትን በማክበር አያባበለ፤ የፖለቲካ ሥልጣኑን ግን በተማከለ መልኩ በኮሚኒሰት ፓርቲ አጅ ጨብጦ በመያዝ ያሥተዳድር ነበር። ይሀ ተጨባጭ ሁኔታ በሁለቱ ሀገራት ውስጥ የብሔሮች ጥያቄ እንደ ረመጥ አሳት ውስጥ-ውስጡን አንዲቀጣጠል ቢያደግርም ለረጅም ጊዜ ሳይፈነዳ ማቆየት ችሏል። ነገር ግን የዮሴፍ ቲቶን ሞት ተከትሎ በሀገሪቷ ብሔሮች መካከል በተፈጠረ የእርሰ በእርሰ ጦርነት አስከፊ ጭፍጨፋዎች ተፈጸሙ፡ ዩጎዝላቪያም ወደ ብዙ ሀገሮች ተበታተነች። በሶቪየት ኅብረት የኮሚኒዝም ሥርዓት እየተዳከመ ሲመጣ ሚካኤል ጎርባቾቭ የተሀድሶ እርምጃዎችን በመውሰድ ወደ ዴሞክራሲያዊ ሥርዓት ለማሸጋገር ሲሞክር ተከድኖ ሲበሰል የነበረው የብሔሮች ጥያቄ ፈነዳ። የእርሰ በእርስ ጦርነት በየቦታው ተቀጣጥሎ፣ ብዙ ብሔሮች ነጻ ሀገር እንዲመሠርቱ አስቻለ።

የሀገራችንን ሁኔታ ሰንመለከት መለስም የብሔር ፈደራሊዝም እናአምባገነናዊ ሥርዓትን አጣምሮ ገነባ። የብሔሮችን ጥያቄ በአግባቡ ከመመለስ ይልቅ ልክ እንደ ቲቶ በአንድ በኩል እያባበለ በሌላ በኩል እየበደለ ሲገዛ ቆያ። ከቲቶ ሞት በኋላ ተተኪው የዩጎዝላቪያ መንግሥት የብሔር ጥያቄዎችን በብልኃት እናበጉልበት አመዛዝኖ ለማሰጠበቅ የሚያስችል ኃይል እና ዘዴ ሰላልነበረው ሀገሪቷ እንደተበታተነችው፣ ኢትዮጵያም መለስ ሲወድቅ ተመሳሳይ ሁኔታ ያጋዋጥማት ይሆን? ብይ ራሴን አጠይቅ ነበር።

ከመለስ በኋላ ኢሕአዴግ ይቀጥላል ወይሰ ይበታተናል? ፓርቲ፣ መንግሥት እናሀገር አንድ በሆኑበት ሁኔታ ፓርቲው እየተዳከመ ከሄደ ሀገሪቷ ትተርፍ ይሆን? በዩጎዝላቪያ እናበሶቪየት የተፈጸመው የብሔሮች ግጭት እናመበታተን በኢትዮጵያ እናበብሔሮቿ አንዳይደርስ ምን መደረግ አለበት? እያልኩ በማሰብ ማጥናቱን አጠናክሬ ቀጠልኩበት። ለቄሮ ትግል ሰትራቴጂ ሰናወጣም እነዚህን ጥያቄዎች ከግምት አሰገብተናል።

በአጠቃላይ በ"ICNC" ያሳለፍኩት ጊዜ በታሪክ እናበንድፈ-ሐሳብ ስማረው የነበረውን የሰላማዊ ትግል ሰትራቴጂ በተጨባጭ ከሥሩ እናሲሠሩ ከነበሩ ሰዎች እንድማርና ግንዛቤዬን አንዳሰድግ ትልቅ ዕድል ፈጥሮልኛል፤ ለወደፊት ሥራ አእምሮዬን አንዳዘጋጅም አግዞኛል። በኋላ ላይ ኦሮሚያ ውስጥ ለተደረገው የሰላማዊ ትግል ዕቅድ መንደፍ የጀመርኩት በዚያ ጊዜ ነበር።

የዋሽግንተን ዲሲ ቆይታዬ ከተለያዩ የአሜሪካ መንግሥት አካላት እናየተባበሩት መንግሥታት ድርጅት (UN) ፣ የዓለም የገንዘብ ድርጅት (IMF)፣ የዓለም ባንክ (World Bank) ከመሳሰሉ የዓለም አቀፍ ድርጅቶች ባለሥልጣናት ጋር አንድተዋወቅ አሰቻለኝ። ዲሲ ብዙ የጥናት ተቋማት (think tank) እና የሰብዓዊ መብት ተሟጋች ድርጅቶች የሚገኙበት ከተማ በመሆኗ ጥሩ ትስስር አንድፈጥር እና ጠቃሚ መረጃዎችን አንዳገኝ አግዞኛል። ይህ ግንኙነት የምዕራባውያን መንግሥታት እና ዓለም አቀፍ ድርጅቶች በማደግ ላይ ባሉ ሀገራት ላይ የሚያራምዱትን አመለካከት እናድርጊት በተጨባጭ አንድገነዘብም ረድቶኛል።

የዋሽንግተን ዲሲ ቆይታዬ ለአንድ ዓመት ብቻ ቢሆንም ሰላማዊ ትግልን በማጥናት ብቻ ያለፈ አልነበረም። በኢትዮጵያ ሰም የሚካሄደውን የአማራ ፖለቲካ ቀረብ ብዬ ለማወቅ ጥሩ ዕድልም ፈጥሮልኛል። ከዚያ በፊት የአማራ ተቋማት እናመሪዎች (elites) ኦሮሞን እናትግሉን አሰመልክቶ ያላቸውን አመለካከት ከመጻሕፍት እያነበብኩ እና ከሚዲያ የሰማሁ ብመጣም በቀጥታ ለማውራት ብዙም ዕድል አላገኘሁም። የኦሮሞን ትግል በተመለከተ አብዛኞቹ የአማራ ምሁራን እናመሪዎች በሚዲያ የሚናገሩት ነገር እኔ ከማየው እውነታ የራቀ ስለነበር ይህን አመለካከት የሚያንፀባርቁት ከመረጃ አጥረት የተነሳ ይመሰለኝ ነበር። በተለይ ሰለ ቁቤ (የአፋን ኦሮሞ ፊደል) ፣የኦነግ ፖለቲካ፣ የኦሮሞ ባሕላዊ እናማኅበራዊ ሁኔታ የሚጽፉት እና የሚናገሩት ከአውነታው እናከተጨባጭ ሁነታ ጋር የሚጋጭ በመሆኑ በቂ መረጃ ካለማግኘት የመጣ አድርጌ አረዳ ነበር። ምናልባት የኦሮሞ ምሁራን ጠጋ ብለው የኦሮሞን ፍላጎት፣ አመለካከት እናየትግል አቅጣጫ ሳያሰረዱ ቀርተው ይሆን? ብዬም አሰብኩ።

ዋሽንግተን ዲሲ የአማራ ብሄር ተወላጆች በብዛት የሚኖሩባት ከተማ ስለሆነች አጋጣሚውን ተጠቅሜ ሰለ ኦሮሞ ያላቸውን የተሳሳተ አመለካከት ምንጩን ለመረዳት፣ ከተቻለ ደግሞ ለማስተካከል ለመሞክር ፈለኩኝ። ብዙዎቹን አንጋፋ የፖለቲካ መሪዎች ከሥራ በኋላ አንዲሁም ቅዳሜ እናእሑድ በማግኘት መወያየት ጀመርኩ። ከኢሕአፓ አንሰቶ እስከ ቅንጅት ድረስ ጠንካራ ተሳትፎ ካለው አንጋፋ ፖለቲከኛ ያሬድ ጥበቡ (ጀቤሳ) ጋር ጥሩ ጓደኝነት ስለመሠረትን፣ ከብዙ ታዋቂ ሰዎች ጋር ተገናኝቼ በማውራት ሐሳባቸውን መረዳት ቻልኩ።

ያሬድ ጥበቡ ሚዛናዊ አስተሳሰብ ያለው ሰው ነው። ከልጅነቱ ጀምሮ ከኦሮሞ ታጋዮች ጋር ቅርርብ ስለነበረው በኦሮሞ ፖለቲካ ላይ የተሻለ ግንዛቤ አለው። ከኦነግ መሪዎች መካከል ከአቦማ ምትኩ ጋር አብሮ ተምሯል። ከተቀሩትም ጋር ይተዋወቃል። በብዙ ጉዳዮች ላይ ባንሰማማም በማንኛቸውም ጉዳዮች ላይ በግልጽ ለመወያየት ብዙም አልተቸገርንም። በአርሱ አማካኝነት በኢትዮጵያ ሰም ከሚንቀሳቀሱ ምሁራን እናመሪዎች ጋር በመተዋወቅ ሐሳባቸውን በቀጥታ ለመረዳት ዕድል አገኘሁ። ኃይሉ ሻውል (የቀድሞ የቅንጅት ሊቀመንበር) ፣ ዶ/ር ብርሃኑ ነጋ፣ ነገደ ጎበዜ (ከመኢሶን መሪዎች አንዱ) እናሌሎችንም ሰዎች በማግኘት ብዙ ተወያየን። በተጨማሪም ዶ/ር ነጋሶ ጊዳዳ እና ሰዬ አብርሃ ከኢትዮጵያ ለጉብኝት ሲመጡ አግኝቻቸው ሰለ ፖለቲካ አመለካከታቸው እና እቅዳቸው መረዳት ቻልኩ።

ከያሬድ ጥበቡ ጋር በመሆን በዋሽንግተን ዲሲ አካባቢ ካሉ የተወሰኑ አንቂዎች ጋር በየሳምንቱ በሰላማዊ ሰልቶች ላይ የምንወያይበትን መድረክ አዘጋጀን። ፕሮፌሰር ላሪ ዳይመንድን ጨምሮ ሌሎች ምሁራንንም እየጋበዝኩ ያስተምሩናል። በኋላ ላይ በቄሮ ትግል ወቅት የአማራ እና የኦሮሞ የፖለቲካ ኃይሎችን ለማሰተባበር የተጠቀምንበት የ 'ኦሮማራ' አባባል እና ሐሳብ ከዚያ መድረክ ተሞክሮ በመነሳት ያሬድ ያፈለቀው ነው።

አንድ ቀን እዚያው ዋሽንግተን ዲሲ በኢትዮጵያ ጉዳይ ላይ የሚወያይ ሰብሰባ ተጋብዝዤ ሄድኩ። ፕሮፌሰር መሳይ መኮንን እና ዶ/ር ብርሃኑ ነጋን ጨምሮ ብዙ ምሁራን ንግግር ለማድረግ ቀርበው ነበር፡ እኔም የጥናት ወረቀት ለማቅረብ ተገኘሁ። መድረኩ ላይ ሆኜ ተሳታፊዎቹን ሰመለከት ብዙ ነገር ታዘብኩ።

አንዲናገሩ የተጋበዙትም ሆኑ ለመሳተፍ መጥተው አዳራሹን የሞሉት ዕድሜያቸው የገፋ ወንዶች ብቻ ናቸው። በእኔ ዕድሜ ያሉ ወጣቶች በጣት ይቆጠራሉ። ሴቶች ከሁለት ወይም ከሦስት አይበልጡም። ሙስሊም ከእኔ እና ዶ/ር ሠዒድ ከሚባል ሰው በቀር አዳራሽ ውስጥ ያለ አይመሰለኝም። አንገታቸው ላይ ከጠመጠሙት ባንዲራ እና የምኒሊክ ፎቶ ያለበትን ሹራብ ከመልበሳቸው በመነሳት ብዙዎቹ የሰብሰባው ተካፋዮች አማራ ሳይሆኑ አንዳልቀሩ ገመትኩ። ይህን ሁኔታ አይቼ በዝምታ ማለፍ አልፈለኩም። በኢትዮጵያ ሰም በተጠራ ሰብሰባ ላይ የሀገሪቷን ኅብረተሰብ የሚያንፀባርቅ ውክልና አለመታየቱ ችግር  እንደሆነ ለማሰገንዘብ ወሰንኩ።

የጥናት ወረቀቴን ለማቅረብ ተራቆ ሲደርሰ «አሰላሙ አሌይኩም› ብዬ ጀመርኩ። ያልተለመደ አና ያልተጠበቀ ስለነበር አዳራሹ ውስጥ የነበሩት ዘረው እርስ በእርሰ ተያዩ። ዳር ላይ የነበሩ አንድ ሁለት ሰዎች «ዋሌይኩም ሰላም» በማለት አፀፋውን መለሱ። አዳራሹ ሰለምታ አሰጣጤ ከፈጠረው ድባብ ሳይላቀቅ «ሰለጋበዛችሁኝ አመሰግናለሁ። የጋበዛችሁኝ ሰለ ኢትየትጵያ መፃዒ ዕድል የሚመክር ስብሰባ አለ ብላችሁ ነው። ነገር ግን መድረኩን እና አዳራሹን ስመለከት ያሉት ሰዎች የኢትዮጵያን ብዝኀነት የሚያንፀባርቁ አይመስለኝም። ሴቶች የታሉ? የሕዝቡ ግማሽ ናቸው፡ አዚህ ግን የሉም። የሀገሪቷ ገሚስ የሆኑት ሙስሊሞችስ? ከእኔ እና ከሁለት ሰው ውጪ ወጣት አላየሁም። ኦሮሞ እና ሶማሌስ የት አሉ? የሀገሪቷን ሕዝብ ብዝኀነት ሳያንፀባርቅ፤ አንድን ቡድን ብቻ ሰብስቦ የኢትዮጵያን ችግር አንፈታለን ብሉ ማሰብ ሀገሪቷን ለተጨማሪ ችግር ከመዳረግ ውጪ መፍትሔ አይሆንም! » በማለት ንግግሬን ጀመርኩ።

ከመድረኩ አዘጋጆች አንዱ የሆነው ነአምን ዘለቀ «አልመጡ ይሆናል አንጂ ሁሉንም ቡድኖች ጋብዘናል» በማለት ችግሩ የአዘጋጆቹ እንዳልሆነ ለማብራራት ሞከረ። እኔም «አናንተ ሁሉንም ከጋበዛችሁ፣ የተለያየ ብሔር አባላት፣ የአምነት ተከታዮች፣ አንዲሁም ሴቶች እና ወጣቶች ቀርተው የአንድ ብሔር ተወላጅ የሆኑ ዕድሚያቸው የገፋ ወንዶች ብቻ ለምን ተገኙ? ብላችሁ አእራሳችሁን ጠይቁ» ብዩ ጽሑፌን ወደ ማቅረቡ ገባሁ።

የዋሽንግተን ዲሲ ቆይታዬ የአማራ ፖለቲካ አንቀሳቃሾች በኢትዮጵያ ሰም የሚያራምዱትን አመለካከት በተሻለ ሁኔታ አንድገነዘብ ሰላሰቻለኝ ወደፊት በምሰራው ሥራ ውስጥ ከአነሱ ጋር ሊኖር የሚገባው ግንኙነት ምን መምሰል አንዳለበት ማቀድ አንድጀምር አድርጎኛል። መጀመሪያ አንዳሰብኩት አመለካከታቸው ከግንዛቤ አጥረት ብቻ ሳይሆን ለኦሮሞ የፓለቲካ ጎራ ካላቸው ንቀት አንዲሁም ትምክህት እንደሚመነጬ ተረዳሁ። ንቀት እና ድንቁርና

አንድ ላይ ሲመጣ የፖለቲካ አመለካከትን እንደሚያሳውር ተገነዘብኩ። መጀመሪያ በሙገሳ ሲቀበሉኝ ሊጠቀሙብኝ እስበው ነበር። በኋላ ላይ በኦሮሞ ትግል እና በኢትዮጵያ ፖለቲካ ላይ ያለኝ አቋም እንደማይለወጥ ሲመለከቱ በጠላትነት ፈርጀው ዘመቱብኝ።

በዋሽንግተን ዲሲ ከኦሮሞ ማኅበረሰብ ጋርም ጥሩ ግንኙነት ነበረኝ። በተለይ በሰሜን አሜሪካ የኦሮሞ ማኅበረሰብ እንቅስቃሴ ውስጥ ግንባር ቀደም የነበሩ አንጋፋ ሰዎች አዚያ ሰለሚኖሩ፣ ከ70ዎቹ እስከ 90ዎቹ የነበረውን የተማሪዎች እንቅስቃሴ ለመማር ትልቅ አጋጣሚ ሆነልኝ። ሉቤ ብሩ፣ በዳኔ ታደሰ፣ ቀበኔ (ቦኒ ሆልኮም) ፣ ጀይሉ ደንቦባ፣ አበራ ተፈራ፣ ደረጀ ቱፋ፣ አባ ከለቻ የመሳሰሉ አንጋፋዎች በሰሜን አሜሪካ ሲደረግ ለነበረው የኦሮሞ ትግል ቤተ-መጻሕፍት ናቸው ማለት ይቻላል። የኦሮሞው ምሁር ሲሳይ ኢብሳ አሜሪካ ከመሄዴ ጥቂት ወራት በፊት በማረፉ ለማግኘት አልታደልኩም። የትግል ጓዶቹ የኦሮሞን የባሕል ማዕከል ገዝተው በስሙ ሰይመው ስለነበር፡ በየሳምንቱ ዓርብ ምሽት ተገናኝተን ሰለ ኦሮሞ ትግል፣ ታሪክ እና ወደፊት ሰለሚሰራው ሥራ አንወያያለን። ማዕከሉም አዛውንቶች እና ወጣቶች የሚሰባሰቡበት የልምድ ልውውጥ ቦታ ሆነ። ዓርብ ምሽት ወደ ፈረንጆቹ የመዝናኛ ቤቶች ይሄዱ የነበሩ ወጣቶች የኦሮሞን ማዕከል የእውቀት እና የመዝናኛ ቦታ አደረጉት። ከድምፃዊ አብዲ ኑረሳ እና ከሌሎች ጋር በመሆን ወጣቶችን የሚማርክ፡ አዛውንቶችን የማይገፋ ማዕከል ለማድረግ ሰራን።

በዋሽንግተን ዲሲ ከቀረብኳቸው ሰዎች ውስጥ በዳኔ ታደሰ አንዱ ነው። ከሀገር ከወጣ ከአርባ ዓመታት በላይ ሆኖታል። የሲሳይ ኢብሳ ጓደኛ እና ዘመድ ሲሆን ውልደቱ ፊንፊኔ ነው። በልጅነቱ ለትምህርት ከሀገር የወጣ ሲሆን፣ የኮሌጅ ተማሪ ሆኖ “Black Panter” (ጥቁር ግስላ) በተባለ የጥቁር ሕዝብ አንቅስቀሴ ውስጥ እንደ ስቶክሊ ካርማይክል (Stokely Carmichael) ካሉ መሪዎች ጋር ሰርቷል።

በሚያዘጋጀው የሬዲዮ ፕሮግራም ከአፍሪካ መሪዎች ለዚያድ ባሬ እና ጁሊየስ ኔሬሬ ቃለ- መጠይቅ አንዳደረገላቸው ነግሮኛል። በዳኔ የኢትዮጵያ ተማሪዎች በሰሜን አሜሪካ ሲያደርጉ በነበረው የፖለቲካ እንቅስቃሴ ውስጥ ሲሳተፍ ቆይቶ፣ በብሔር ጥያቄ ጉዳይ ክፍፍል ሲፈጠር ወደ ኦሮሞ ትግል ገባ። ከሲሳይ ኢብሳ እና ከሌሎች ጋር በመሆን በሰሜን አሜሪካ የኦሮሞ ተማሪዎች ማኅበርን በመመሥረት ፀረ-ኦሮሞ ከሆኑ አካላት ጋር በሚደረግ ክርክር እና ውዝግብ በግንባር ቀደምነት ተካፍሏል። አኔ ሳገኘው ዕድሜው ገፍቶ፣፣ የጤና እክል የገጠመው ቢሆንም ወኔው ሙሉ፡ አእምሮውም ቀልጣፋ ነበር። ቅዳሜ ቅዳሜ ሊንከን የተባለች መኪናውን እየነዳ መጥቶ ከቤቴ ይወስደኝና ካፌ ቁጭ ብለን የጥቁር ሕዝቦችን የትግል ታሪክ ይተርክልኛል። የኦሮሞን ትግል የሚቃረኑ ግለሰቦች ወደሚሰበሰቡበት ሰፈር ይዞኝ በመሄድ አጀንዳ አንስቶ የጦፈ ክርክር ያካሄዳሉ። ክርክሩ ሲሰለቸን ሥጋ ገዝተን ወደ ቤቱ አንሄዳለን፣ ጓደኞቻችንን ጠርተን ፖለቲካ እየተወያየን አንዝናናለን።

በቤቱ ውስጥ ተደርድረው ከሚታዩ በሺህ የሚቆጠሩ መጻሕፍት አንዱን መዝዞ አንዳነብ ያውሰኝና፣ አንብቤ ጨርሼ በሚቀጥለው ስንገናኝ እንወያይበታለን። ያኔ በኢትዮጵያ ፖለቲካ ላይ አጫጭር ጽሑፎች (Articles) በብዛት ጽፌ በድረ-ገጾች እለጥፍ ስለነበር በዳኔ አንብቦ አንዳንድ ነጥቦችን በቀይ ቀለም አሰምሮበት ይጠብቀኛል። ጽሑፉን ምንም ያሀል ቢወደውም አያሞግሰኝም፡ «Where is the fire? It is too soft» ብሎ ይተቻል።ለሚስቱ ጮክ ብሎ «ፋን አሰቲ ያቺን የሚወዳትን ሽሮ በርበሬ በዛ አርገሽ አምጪለት፣ ብዙ

በርበሬ ከበላ ይኼን አልጫ ሳይሆን ቆፍጠን ያለ ጽሑፍ ያዘጋጅ ይሆናል» በማለት ይቀልዳል።

በዳኔ አባትም፣ ጓደኛም ሆነኝ። ዋሽንግተን ዲሲን ለቅቄ ኒው ዮርክ መኖር ስጀምር በየወሩ አነሱ ጋር እየሄድኩ እውላለሁ። ከዚያ በኋላም እንደ አጋጣሚ በዚያ ከተማ በኩል ሳልፍ ጎራ ብዬ ሰላም እላቸዋለሁ። እሱም ዋሽንግተን ዲሲ ሳለሁ እንደሚያደርገው ሁሌ ቅዳሜ ደውሎ ቢያንስ ለሁለት ሰዓት እናወራለን። በዳኔ እ.አ.አ. በ2016 ከዚህ ዓለም በሞት ተለይቶ ነፍሱ ከጓዶቹ ከነ ሲሳይ ኢብሳ ጋር ተቀላቀለች። እኔም በቀብር ሥነ ሥርዓቱ ላይ ተገኝቼ በእንባ ሸኘሁት።

ዋሽንግተን ዲሲ የሄድኩበትን ፕሮግራም ከጨረስኩ በኋላ ወደ ሚኒሶታ ተመልሼ ከአርፋሴ ጋር መኖር ጀመርን። በአንድ ዓመቱ የሚኒሶታ ቆይታዬ ማንበብ እናመፃፍ ላይ አተኮርኩ። “Dhummuugaa" እና "Gulelepost" የተሰኙ ድረ-ገጾችን በመክፈት የሀገራችንን ፖለቲካ የሚተነትኑ ጽሑፎችን ማተም ጀመርኩ። ጽሑፎቹም ብዙ አንባቢ የነበራቸው እና ሰፊ ክርክርና ውይይት የሚካሄድባቸው ነበሩ።

በዚያ ወቅት (2010-2011) አረብ ሰፐሪንግ (Arab Spring) በመባል የሚታወቀው የአረብ ሀገራት አመጽ ሰለፈነዳ ሳጠና የነበረውን ሰለማዊ ትግል በተጨባጭ ሲተገበር ለመመልከት ቻልኩ። በአረብ ሀገራት የዕለት ተዕለት ክሰተቶችን ከሚዲያ እና ከጓደኞቼ የማገኘውን መረጃ በመጠቀም ከተማርኩት ጋር በማነጻጸር አጠና ነበር።

አመጹ የሀገራችንን ሕዝብ እና መንግሥት ቀልብ ሰለሳበ እየተካሄደ ሰላለው ነገር ለማኅበረሰባችን ሊገባ በሚችል መልኩ በማዘጋጀት ሚዲያ ላይ ትንታኔ ስሰጥ ነበር። በተለይ የመለስ ዜናዊ መንግሥት በቅርብ ያሉትን የአረብ አምባገነኖች እየገረሰሰ ያለው የአመጽ ማዕበል ኢትዮጵያም እንዳይደርሰ በመፍራት ሰፊ የመረጃ ዘመቻ እያካሄደ ነበር። የኢትዮጵያ ማኅበራዊ፡ ኢኮኖሚያዊ እና ፖለቲካዊ ሁኔታ ከአረብ ሀገራት በብዙ መልኩ የተለየ እንደሆነም በማሳየት እነዚያን ሀገራት እየናጠ ያለው አመጽ ኢትዮጵያ ውስጥ የመፈንዳትም ሆነ የማሳካት ዕድል እንደሌለው ለማሳመን ሞከረ። የመንግሥትን የፕሮፓጋንዳ ዘመቻ ለማክሸፍ ብሎም ሕዝባዊ አመጽ ኢትዮጵያ ውስጥ ሊሳካ እንደሚችል ለማሳየት “Nonviolent Struggle: Ethiopian Exceptionalism?" የሚል ጽሑፍ ጽፌ አሰራጨሁ።ይህን ሐሳብ አንዳብራራ ብዙ ሚዲያዎች እየጋበዙኝ ሰላማዊ ትግል ኢትዮጵያ ውስጥ ሊሳካ የሚችልባቸውን ምክንያቶች ስተነትንና በየቀኑ የሚከሰቱ ኹነቶችን በፌሰቡክ በኩል ግንዛቤ ሳስጨብጥ ነበር።

የአረብ አብዮት በቱኒዝያ፡ በሊቢያ እና በግብጽ አምባገነን መንግሥታትን በፍጥነት በማሰወገዱ፡ ወደ ዴሞክራሲ የሚያመራ ማዕበል መሰሉ ቢታይም ብዙም ሳይቆይ እንደ ሶሪያ፣ የመን እና ሊቢያ ያሉ ሀገራትን ወደ አስከፊ የእርስ በእርስ ግጭት አስገባ።

የአምባገነን መንግሥታት መውደቅ የዴሞክራሲ ሥርዓትን ይወልዳል ተብሎ ሲጠበቅ ግጭት እና የሀገር መፍረሰን አስከተለ። ይሀ ደግሞ በኢትዮጵያ ለመተግበር ያሰብኩትን የትግል ስልት መልሼ አንድከልሰ አሰገደደኝ። ምክንያቱም አብዛኛው ዜጋቸው በብሔር፣ በሀይማኖት እና በቋንቋ ተመሳሳይ የሆኑባቸው የአረብ ሀገራት በዚያ ሁኔታ ወደ ግጭት ከገቡ፡ የታሪክ ቁርሾ ባላቸው ብዙ ብሔሮች የተንነባቸው ሀገራችን ምን ልትሆን እንደምትችል ሳሰብ አሰፈራኝ።

የትግላችን ዓላማ አምባገነናዊ ሥርዓትን አሰወግደን የብሔሮች አኩልነት እና የግለሰቦች ነጻነትን የሚያረጋግጥ ዴሞክራሲያዊ ሥረዓተ-መንግሥት መገንባት ነበር። ይህ ምኞታችን የሚሰካው ግን ከመንግሥት ለውጥ በኋላም ሀገረ-መንግሥቱ (state) ከቀጠለና ሰላምና መረጋጋትን ማሰፍን ከተቻለ ብቻ ነው።

ሀገረ-መንግሥት ከፈረሰ ሕዝቡ የዴሞክራሲ መብት መጠየቅ ይቅርና ወጥቶ የመግባት እና የሕይወት ዋስትና እንደማይኖረው በአረብ ሀገራት ውስጥ እየሆነ ካለው መገንዘብ ይቻላል። ስለሆነም አምባገነናዊ ሥርዓትን ለመጣል በምናደርገው ትግል የሕዝቦች ግጭት እና የሀገር ውድቀት እንዳይመጣ ጥንቃቄ ማድረግ እንዳለብን ለማሰብ ተገደድን።

ስለዚህም መንግሥትን መገልበጥ (regime change) ዓላማ አድርገን ሰናወጣ የነበረውን ስትራቴጂ በመከለሰ ሥርዓቱን መቀየር ላይ ያነጣጠረ እንዲሆን አደረግነው። አንድን መንግሥት ገልብጦ ለውጥ ማምጣት በተለያዩ ሰልቶች አገዛዙን ሙሉ በሙሉ እንዲወገድ ማድረግ ሲሆን፣ ሥርዓቱን መቀየር ደግሞ ከሥርዓቱ ውስጥ እና ውጪ ያሉ ለውጥ ፈላጊ ኃይሎችን በማሰተባበር አገዛዙ ሳይፈርሰ ለውጥ እንዲያመጣ ማሰገደድ ነው። መንግሥትን ሙሉ በሙሉ መገልበጥ የሀገረ-መንግሥት መፍረሰ አደጋን እንዳያስከትል ሰለሠጋን ሳይወድቅ ለውጥ እንዲያመጣ ማስገደድ ላይ ማተኮርን መረጥን።

የአረብ ሀገራትን ሕዝባዊ አመጽ እየተከታተልኩ እነርሱ የገጠማቸው አደጋ እንዳይደርሰብን መደረግ ስላለባቸው ጥንቃቄዎች ሳሰብ እና ሰጽፍ ነበር። ጎን ለጎን ጥቂት የኦሮሞ ወጣቶችን በማሰባሰብ በሰላማዊ ትግል ሥልት ላይ ሥልጠና ስሰጥ ቆየሁ። የሥልጠናው ዓላማ እነርሱን ማስተማር ብቻ አልነበረም፣ ሀገር ውስጥ ላሉ ታጋዮች ለመሰጠት ላቀድኩት ሥልጠና ልምምድ ለማድረግም ጭምር ነው።

የሥልጠናው ይዘት እና ስልት ኦሮሚያ ውስጥ ላሉ ወጣቶች ሊገባ በሚችል መልኩ መሰጠት ስላለበት መጀመሪያ ሚኒሶታ ካለው ቡድን ጋር ተለማምጄ ሐሳባቸውን ማካተቴ የበለጠ አንዳዳብረው ረዳኝ። አንዳንዶቹ ተሳታፊዎች በኦሮሞ ወጣቶች አመራር ኮንፈረንስ (OYLC) ሥልጠና ላይ የተሳተፉ ሲሆኑ፡ የተወሰኑት ደግሞ በዛው ሰሞን ከሀገር ቤት የመጡ ናቸው። እነዚህን ሁለት ዓይነት ተሳታፊዎች ማሳተፋችን ልምምዱን የበለጠ አጠናከረው። ከልምምዱ በኋላ የተሟላ የማሰልጠኛ ማኑዋል በማዘጋጀት ሀገር ውስጥ ላሉ የተወሰኑ ወጣቶች በኢንተርኔት፣ ጥቂቶችን ደግሞ ወደ ጎረቤት ሀገራት በማሻገር የአሠልጣኞች ሥልጠና መሰጠት ተቻለ።

ከጥናት እና ሥልጠናው ጎን ለጎን ትምሀርቴን ለመቀጠል መዘጋጀት ጀመርኩ። ወደ ትምህርት እንድመለሰ ጫና አድርገው ያሳመኑኝ ዶ/ር ሐሰን ሁሴን እና አቶ ብዙወርቅ ባላ ነበሩ። ከአቶ ብዙወርቅ ጋር ብዙ ጊዜ ተገናኝተን ሰናወራ ወደ ትግል በቀጥታ መግባት እንደማስብ ሰነግረው፣ እርሱ ግን ትምሀርቴን እንድቀጥል ይወተውተኛል። ዶ/ር ሀሰን ትውልዳችን አንድ አካባቢ ስለሆነ ከእኛ በፊት ከፍተኛ ነጥብ አምጥተው ዩኒቨርሲቲ በመግባታቸው ከሚወደሱና ቤተሰቦቻችን እንደ አርአያ እየነገሩ ካሳደጉን ተማሪዎች ውስጥ የሚጠቀስ ነው። በኋላም የኦነግ ወጣት አመራር ውስጥ የሥራ አሰፈፃሚ አባል እና ዋና ጸሐፊ እስከ መሆን ደርሷል። ከራሱ ልምድ በመነሳት ወደ ት/ቤት ተመልሼ ይክተሬት ዲግሪ (PhD) እንድሠራ መከረኝ፤፡ በወቅቱ እርሱም ወደ ትምህርት ተመልሶ ዶክትሬቱን አየጨረሰ ነበር። እኔም ምክራቸውን በመሰማት ለማሰበው ትግል የበለጠ ለመዘጋጀት ወደ ትምህርት ቤት መመለስ እንደሚጠቅማኝ በማመን ወሰንኩ።

እ.አ.አ. በ2011 የኮሎምቢያ ዩኒቨርሲቲ በሰብዓዊ መብቶች ዘርፍ ለሁለተኛ ድግሪ(ማሰተርስ) ተቀብሎኝ ከአርፋሴ ጋር ወደዚያ ተዛወርን። ኮሎምቢያም ልክ እንደ ሰታንፎርድ ታዋቂ ዩኒቨርሲቲ ቢሆንም ካምፓሶቹ ግን የተለያዩ ናቸው። ሰንታንፎርድ ከከተማ ወጣ ብሎ ራሱን የቻለ ትልቅ ግቢ ያለው ነው።

በአካባቢው የምትገኘው ሳንፍራንሲሰኮ ከተማ ሃምሳ አምስት ኪሎ ሜትር የምትርቅ ስለሆነ፣ የተማሪው ማኅበራዊ ሕይወት በአብዛኛው በዩኒቨርሲቲው ግቢ ውስጥ የተገደበ ነው። ኮሎምቢያ ግን የአሜሪካ የንግድ ማዕከል በሆነችው ኒው ዮርክ ከተማ ማንሃታን ግዛት አምብርት ላይ ይገኛል፣ ከተማዋ እና የዩኒቨርሲቲው ግቢ መሀል ምንም ድንበር የለም። የተማሪው እና የከተማው ኑሮ የተቀላቀለ ነው። ይህ ደግሞ እንደ እኔ ገጠር ተወልዶ፣ ውጪ ሀገር ከሄደ በኋላም በትምህርት ቤት ግቢ ውስጥ ተወስኖ ለኖረ ሰው ለመላመድ ያሰቸግራል።

ስታንፎርድ እያለሁ ዶርም ብኖርም በእግሬ ወይም በሳይክል ወደ ክፍል መሄድ አችላለሁ። ኮሎምቢያ ሕዝብ መሀል አፓርታማ ተከራይቼ ሰለምኖር ክፍል ለመድረሰ ሀያ ደቂቃ በባቡር መጓዝ ነበረብኝ።16 በኒው ዮርክ ከተማ መሀል ብዙ የማኅበራዊ እና የመዝናኛ እንቅስቃሴ ቢኖርም አብዛኛውን ጊዜዬን የማሳልፈው ትምህርት ቤት ስለነበር በከተማዋ ሕይወት ለመሳተፍ ዕድል አላገኘሁም። ወቅቱ ከትምሀርቴ በተጨማሪ የወደፊት የትግል ስልት በማውጣት ላይ ብዙ የማሰብበት እና የምጽፍበት ነበር። በተጨማሪም በኢንተርኔት ላይ መጣጥፎችን አወጣለሁ፣ የተለያዩ ሚዲያዎች ላይ በመቅረብ ትንተና እሰጣለሁ። ይሀ ሁሉ ተደማምሮ ለመዝናናት ያለኝን ጊዜና ፍላጎት ሰላሳነሰው ኒው ዮርክ ለሦሰት ዓመታት ብኖርም ከተማዋን በደንብ ሳላውቃት ነበር የወጣሁት።

በወቅቱ ጓደኛዬ ደሜ ኦርማ (ሙሐመድ አደሞ) የጋዜጠኝነት ትምህርት ኮሉምቢያ ለመማር ከእኔ ትንሽ ቀደም ብሎ ሄዶ ነበር። ከጥቂት ጊዜ በኋላ ባይሳ ገመቹ የሚባል ልጅ ከኦሮሚያ መጥቶ ተቀላቀለን። ኒው ዮርክ ከተማ የሚኖሩት ጥቂት ኦሮሞዎች ብቻ ነበሩ። እኛም እነሱ ወዳቋቋሙት ማኅበር በመቀላቀል መንቀሳቀስ ጀመርን።

ወጣቶችን ለማደራጀት መንቀሳቀሰ ሰጀምር፣ በከተማዋ የሚኖሩ የተወሰኑ ልጆችን ትምህርት ከመጀመሬ በፊት አናግሬ ነበር። ከእነሱ መሀል ደበላ ተሬሳ (አሁን ዶክተር) እና ኢዶሳ አባ ገሮ የወጣቶች የአመራር ሥልጠና ለመጀመር ሰጣጣር ብዙ ረድተውኛል። በሂደት የቅርብ ጓደኛሞች ሆንን፣ እኔ እና አርፋሴ ኒው ዮርክ ሰንመለስ በጥሩ ሁኔታ ተቀብለው አስተናግደውኛል።

ደበላ የተማረው ሕክምና ቢሆንም በንባብ የዳበረ ጥልቅ የታሪክ እና የፖለቲካ እውቀት ስለነበረው የሀገራችንን ፖለቲካ የሚተነትኑ ጽሑፎችን በብዕር ሰም ይለጥፋል። ጽሑፎቼንም በማረም ገንቢ ሐሳብ ይሰጠኛል። ኢዶሳ ቤተሰቦቹ የጅማ ሰዎች ቢሆኑም ፊንፊኔ ተወልዶ አሜሪካ ሰላደገ አፋን ኦሮሞ ሲያወራ ይኮላተፋል። አንድ ቀን በሚኒሶታ ብዙ ወጣቶች ሆነን የOSFNA እግር ኳስ ውድድር ስንመለከት አንድ ኣዛውንት ወደኛ መጥተው በመደዳ እየጨበጡን አንድ በአንድ

አናገሩን። የሚያናግሩትን ሰው ዘዩ እያዳመጡ «አንተ የሐረርጌ ሰው ነህ፣ አንተ ወለጋ ቱለማ፣

16 ሲንጋፖር እና ሰታንፎርድ ስማር በካምፓሰ እኖር ስለነበር በእግሬ ወይም በሳይክል ወደ ክፍል ሰለምሄድ፣ኮለምቢያ ሳለሁ ደግሞ ኒው ዮርክ ከተማ ውስጥ የመኪና ባለቤት መሆን በጣም ወጪ ሰላለው መኪና አልነዳም። ኋላ ላይ በትግሉ ወቅት ሁሌም በሰልኬ ወይም በኮምፒዩተር ላይ አቀርቅሬ ሰለምገኝ መኪና ብነለአደጋ እንደምጋለጥ በመሥጋት፡ ጓደኞቼ ተራ በተራ ያጓጉዙኝ ነበር።ሀገር ቤት ከተመለሰኩ በኋላም በሾፌር መንቀሳቀስ ግድ ሆነ። ከዚህ የተነሳ አሳካሁን መንጃ ፈቃደ የለኝም።

በረና፣ አርሲ› አያሉ ሄደው ኢዶሳ ጋር ደረሱ። ኢዶሳ ሲኮላተፍ ሰምተው «አንተ አቢሲኒያ ነህ» ብለው ሁላችንንም አሳቁን።

ሌላው በኒውዮርክ ከተማ የተዋወኩት አብዱሰላም አባ ጀበል ይባላል። ብዙ መጽሐፍት የሚወጣው ድንቅ ታሪክ ያለው ሰው ነው። ውልደቱ ጅማ ሲሆን በልጅነቱ ከሀገር ወጥቶ በአረብ ሀገራት፣ በሶማሊያ እና በኬንያ ያሳለፋቸው ተደምጠው የማይጠገቡ ክፉና ደግ ገጠመኞች አሉት። በሄደበት ሀገር ሁሉ እንደ ሌላው ስደተኛ እጁን አጣጥፎ በእርዳታ ከመኖር ይልቅ በተለያየ ሥራ ራሱን ያሥተዳድራል። ቤቱ ዩኒቨርሲቲ ግቢ አጠገብ ስለሆነ ብዙ ጊዜ አብረን እናሳልፋለን። የአርሱን ታሪክ መስማት በጥናት ለተጨናነቀ አእምሮዬ ፋታ ሰለሚሰጥ ፈልጌ አገኘዋለሁ። እኔ መጀመሪያ ወደ ኒውዮርክ ሰሄድ፡ አሱ አውሮፕላን ማረፊያ ውስጥ ይሰራ ነበር።

አንድ ቅዳሜ የዕረፍት ቀናችን ስለነበረ ደረቅ ጫት ገዝተን እየቃምን እንደወትሮው ታሪኩን በምርቃና መሀል እየሰማሁ «በጉልበት ሥራ ከእጅ ወደ አፍ የሆነ ኑሮ የምኖረው አስከመቼ ነው? » በማለት ተነጫነጨ። አሱን ለማበረታታት ያሀል መሠራት የሚችሉ የንግድ ሥራ ዕድሎችን ጠቃቀስኩለት። በመሀል ተነስቶ ጥሩ ጣዕም ያለው ጁስ ሠራልን። የጀመርነውን ወሬ ለመቀጠል በማሰብ «የሚገርም ጁስ ነው የምትሠራው፤ ለምን ጁሰ ቤት አትከፍትም? » አልኩት። ሐሳቤ ጁሰ የመሥራት ችሎታውን ለማድነቅ አንጂ ጁስ ቤት ለማሰከፈት አልነበረም። እሱ ግን አስቀድሞ እያሰበበት እንደነበር ነገረኝና ጁሰ ቤት ለመክፈት የሚያሰፈልጉ ነገሮችን፣ የገንዘብ መጠን፣ የዕቃ ዓይነቶች እና ፈቃድ ከኢንተርነት ላይ አያየን በመጻፍ አቅድ ማውጣት ጀመርን።

ለሴሚሰተር ከትምህርት ቤት ከሚሰጠን ገንዘብ ለመነሻ እንዲያውለው ልሰጠው ቃል ገባሁለት። ይህንን ያልኩት አሱን ለማበረታታት ስለነበር ምርቃናው ሲጠፋ በነጋታው የምንረሳው መሰሎ ታየኝ። አብዱሰላም ግን በጠዋት ተነሰቶ ያወራውን ሥራ ላይ ለማዋል ተሰማራ። ከጥቂት ቀናት በኋላ ስንገናኝ ከባንክ ብድር አስፈቅዶና ለጁሰ የሚሆን ቤት ተከራይቶ እያስተካከለ ጠበቀኝ። ይሀ ሰው በትምህርት ከአንደኛ ደረጃ ያልዘለለ መሆኑን ልብ በሉ፤ አንግሊዝኛ የሚናገረው ትንሽ ትንሽ ነው። በምርቃና ያወራነውን ሐሳብ በባለሙያ ወደ ፕሮፖዛል አሰቀይሮ፤ ለባንክ ብድር የሚያሲዘው ንብረት ሳይኖረው፣ በሐሳቡ ብቻ ሰው ዋስ እንዲሆንለት አሳምኖ ብድር አሰፈቀደ።

ብዙ ነጋዴዎች ለመከራየት የሚሻሙበትን ከፍተኛ ገበያ ያለው ቦታ ከተከራየ በኋላ በሳምንታት ውስጥ ሰዎች ተሰልፈው የሚገዙበት ጁሰ ቤት ከፈተ። “Oasis Jimma Juice” ብሎም ሰየመው። ጁስ ብቻ ሳይሆን በራሱ የአዘገጃጀት መመሪያ (recipe) የተሰሩ የተለያዩ ለጤና ተሰማሚ ምግቦች እና ጭማቂዎችን በማዘጋጀት በከተማው ነዋሪ ዘንድ ትልቅ ተወዳጅነትን አገኘ። አክተሮች እና ታዋቂ ሰዎች ወደ እርሱ እየጎረፉ በተለያዩ ሚዲያዎችም መጋበዝ ጀመረ። እንግሊዝኛዋን አየሰባበረም ቢሆን ቃለ-ምልልሰ ይሰጣል። በዚህ ጓደኛዬ ሰኬት በጣም ኮራሁ። ፕሮፌሰሮች እና የክፍል ጓደኛቼን አንዲሁም ሊጠይቀኝ የሚመጡ አንግዶችን ወደ ጁስ ቤቱ ስወሰዳቸው ከፍተኛ ኩራት ይሰማኛል። አሊ ቢራ እና ሀጫሉ ሊጠይቁኝ በመጡበት ወቅት ወደዚያች ጁስ ቤት ወስጃቸው በአብዱሰላም የስኬት ታሪክ በጣም ተደመሙ።

የአብዱሰለም ጥረት እናሰኬት ብዙ ነገሮችን አስተማረኝ። አንድ ሰው ሐሳብና ምኞቱን ለማሳካት በደንብ አሰቦ፣ አቅዶ እና በቆራጥነት ጠንክሮ ከሠራ፤ ማንኛውንም ችግርና አንቅፋት በማሸነፍ ራአይውን እውን ማድረግ እንደሚችል በተጨባጭ አሳየኝ። በጊዜው ሕዝቤን ከጭቆና ነጻ

ለማውጣት ከፍተኛ ፍላጎት አድሮብኝ ስለነበር፡ አብዱሰላም ዓይኔ እያየ ሰኬታማ መሆኑ እኔም እያሰብኩት ያለውን ትግል የበለጠ እንድገፋበት ሞራል ሆነኝ።

ኮሎምቢያ በሰብዓዊ መብት የማስተርሰ ትምህርት በምከታተልበት ወቅት መርሐ-ግብሩ እንደ ሕግ፣ ፖለቲካ፣ ታሪክ እና ኢኮኖሚክሰ ካሉ ዲፓርትመንቶች ኮርሰ እንድወስድ ስለሚፈቅድ በአጋጣሚው ለትምህርት ፍላጎቴ ይጠቅማሉ ብዬ ያሰብኳቸውን ጠንካራ ምሁራን አፈላልጌ መተዋወቅ ቻልኩ።

ከእነዚህ ምሁራን መካከል የፖለቲካ ምሁሩ አልፍሬድ ሰቴፋን (Alfred Stefan) እና የአፍሪካ ጥናቶች ምሁር የሆኑትን ማህሙድ ማምዳኒ (Mahmoud Mamdani) አማካሪዎቼ አደረኩ። በ2012 የማስተርስ ትምህርቴን ለመጨረሰ ስቃረብ የPhD መርሐ-ግብር አንድጀምር መከሩኝ። የድጋፍ ወረቀት ጽፈውልኝ አዚያው ኮሎምቢያ ጀመርኩ። በ2014 መጀመሪያ ላይ OMNን አቋቁመን፣ ትግሉ ሀገር ቤት ፈንድቶ ሙሉ ጊዜዬን ለትግሉ ለማዋል እሰካቋረጥኩበት ጊዜ ድረሰ ስማር ቆይቻለሁ።

በኮሎምቢያ ከመደበኛ ትምሀርቴ በተጨማሪ የወደፊት የትግል ስልት እና ሰትራቲጂ በመጻፍ ላይ አተኮርኩኝ። በሰታንዳርድ ጀምሬ ዋሽንግተን ዲሲ ስኖር ያጠናከርኩትን የሰላማዊ ትግል ጥናት፣ ምሥራቅ አውሮፓ እና ሕንድን በመጎብኘት ያገኘሁትን ልምድ፣ ከአረብ ሀገራት አብዮት ካሰተዋልኩት ኹነቶች ጋር በማጣጣም በቁሮ ለተመራው #OromoProtests እንቅሰቃሴ የሰትራቴጂ መሠረት የሆነ ሰነድ አሰናዳሁ። ረጅሙን እና ውሰብሰቡን ጥናት ወደ ቅድመ ስልታዊ የትግል ሜዳ ዳሰሳ (Strategic Estimate) በአርባ ሁለት ገጽ ጨምቄ አዘጋጀሁ።

ቅድመ ትግል ስልታዊ ዳሰሳ ማለት አንድ ትግል ሊካሄድበት የታሰበበትን ማኅበራዊ፣ ፖለቲካዊ፣ ኢኮኖሚያዊ እና የኃይል አሰላለፍ የመሰሰሉትን ነባራዊ ሁኔታዎች በመገምገም አቅጣጫ የሚያሰቀምጥ ጥናት ነው። በዚሀ ጥናት ውስጥ ልትታገሉለት ያለማቸሁትን ኅብረተሰብ ያስከፉ ነገሮች፤ በትግል እና በጨቋኙ ሥርዓት መካከል ያሉ አከራካሪ ጉዳዮች፡ የትግል እና የጨቋኙን ጎራ ጥንካሬና ውስንነት፡ እንዲሁም የሦሰተኛ ወገን ኃይሎችን አሰላለፍ በተጨባጭ መረጃ ላይ ተመሰርቶ መተንተን ያሰፈልጋል። ዝርዝር የትግል አቅድ (Operational Plan) የሚወጣው በቅድመ ትግል ስልታዊ ዳሳሳ ላይ ስለሆነ ጥራት እና ጥልቀት ያለው መረጃ እንዲሁም ከፍ ያለ ምሁራዊ ሥራ ያስፈልገዋል። በአጭሩ ሰልታዊ ዳሰሳው የታሰበው ትግል የሚመራበትን ዋና ዋና መርሆዎች የያዘ ሰነድ ነው።

ይህንን መርሀ በመከተል የኦሮሞን ሕዝብ፣ የትግሉን ጎራ፣ የኢሕአዴግን መንግሥት፣ የኢትዮጵያን የፓለቲካ ኃይሎች እንዲሁም የዓለም አቀፉን ማኅበረሰብ ሁኔታ በመገምገም፡ የቅድመ ትግል ዳሰሳውን “Transforming the Oromo Movement: Reconciling Organizational Stagnation and Evolutionary Progress" በሚል ርዕሰ አዋቀርኩት።

ጽሑፉ አስከዚያች ዕለት የኦሮሞ ትግል ያለፈበትን ሂደት ከተመለከተ በኋላ ያሉትን ድክመቶች እና ጥንካሬዎች በመመዘን ትግሉ ወደፊት ሊያራምዳቸው የሚገቡ የሰትራቴጂ አማራጮችን ያሰቀምጣል። በተለይ ከ1983 ዓ.ም በኃላ በኦሮሞ እና በኦሮሚያ ውስጥ የተከሰቱ ሦስት ጉልሀ ማኅበራዊ፣ ኢኮኖሚያዊ እና ፖለቲካዊ ለውጦች ተዳሰውበታል። እነዚህ ለውጦችም በራስ ቋንቋ መማር እና መሥራት (mother tongue literacy) ፡ የኦሮሚያ ቢሮክራሲ መመሥረት

(bureaucratization) እና የከተሜነት መሰፋፋት (urbanization) ናቸው።

ይህንን ከግንዛቤ በማሰገባት ለወደፊት የምንከተለው ሰትራቴጂ እነዚህ ሁኔታዎች የፈጠሩትን መልካም ዕድሎች (comparative advantages) መጠቀም እንዳለበት ያመለክታል። የትጥቅ ትግልን ጥንካሬ እና ድክመት በመመዘን፣ ከደረስንበት ነባራዊ ሁኔታ በመነሳት የኦሮሞ ትግል ሰላማዊ የትግል ሰትራቴጂን ቢላመድ የተሻለ እንደሆነ ይጠቁማል።

የሰትራቴጂ ሰነድ ስለነበር በግልጽ መለጠፉ ጠላትን ማንቃት መሰሎ ሰለታየኝ በውስጥ ለተወሰኑ ግለሰቦች እና ቡድኖች አካፈልኩኝ። ኤርትራ ውስጥ ወዳለው የኦነግ አመራር ልኬ መልሰ ሳይመጣልኝ ሲቀር የቀረበው ሐሳብ ተቀባይነት እንዳጣ ከተወሰኑ አመራሮች ሰማሁ። ሰነዱን ለተወሰኑ የOSA አንጋፋ ምሁራንም ላኩት። ፕሮፌሰር ሙሐመድ ሐሰን17 እና ቀበኔ (Bonnie K. Holcomb) ቀድመው ካዩት በኋላ ግብረ መልሰ (feedback) ላኩልኝ። 18

የመጨረሻውን ሰነድ ከተመረጡ ጥቂት ምሁራን ጋር ተወያይተንበት "ጥሩ ነው' ሰላሉ ተልኮላቸው እ.አ.አ ጁላይ 2013 ዋሸንግተን ውስጥ ተወያየንበት። አንዳንድ ምሁራን የእኔን ትንታኔ ቢወዱትም የሰላማዊ ትግል ኢትዮጵያ ውስጥ ሊሳካ መቻሉን ግን ተጠራጠሩ።

ሌሎቹ ደግሞ ሰለማዊ ትግል በጭራሽ አያስፈልግም በማለት የቀረበውን ስልት አጣጣሉት፤ ጥቂት ሰዎች የሰነዱን ዓለማ በመጠራጠር ለውይይት መቅረቡን እራሱ ተቃወሙት። ከውይይቱ የተገኙ ሐሳቦችን ወሰጄ የሚስተካከለውን ማሰተካከል ከሀገር ውስጥ ግንኙነት ለነበረን አካላት በምሥጢር በመላክ እንዲወያዩበት ተደረገ። በቅድመ ትግል ዳሰሳው ላይ የተመሠረቱ ዝርዝር እቅዶች እና ስልቶች ተዘጋጅተው ወደ ሥራ ተገባ።

17 ፕሮፌሰር ሙሐመድ ሐሰን ታዋቂ የታሪክ ምሁር ሲሆኑ፣ ለኦሮሞ ትግል ግንባር ቀደም የእውቀት አፍላቂናቸው። ዕውቁን The Oromo of Ethiopia: A History 1570-1890 የተሰኘን እና ተዛብቶ ሲቀርብ የነበረን የኦሮሞ ታሪካ ያቃና መጽሐፍ ደራሲ ናቸው።

15 ቦኒ ሆልኮም (Bonnie Holcomb) ዕድሜ ልኳን የኦሮሞን ሕዝብ ትግል ሰትደግፍ የኖረች አሜሪካዊ ምሁርሰትሆን፣ ከሲሳይ ኢብሳ ጋር በመሆን The Invention of Ethiopia: The Making of Dependent Colonial State in North East Africa የተሰኘውን መጽሐፍ ደርሰዋል። ከኦሮሞ ሕዝብና ምሁራን ጋር ካላት ወዳጅንት የተነሳ ቀበኔ (Qabbannee) የሚል የኦሮሞ ሰም ተሰጥቷት አብናኞው ሰው ይህን አንጂ የፈረንጅ ስሟን አያስታውስም።

## 6.2. ስትራቴጂ እቅድ ዝግጅት

ደጋግሜ እንደገለጽኩት ከልጅነቴ ጀምሮ አያየሁ እና አየሰማሁ ያደኩትን ጭቆና ከሕዝቤ ትከሻ ላይ ለማላቀቅ በኦሮሞ ትግል ውስጥ መሳተፍ ቀዳሚ ምኞቴ ነበር። ያኔ ሕልሜ የኦነግን የትጥቅ ትግል መቀላቀል ነበር። በልጅነቴ ያየኋቸው የኦነግ ወታደሮች በአእምሮዬ ውስጥ የቀረጹት ምናብ እና ምስል ሳድግ እንደ እነርሱ የመሆን ብርቱ ፍላጎት ፈጠረብኝ። ምናልባትም የአባባቢያችን ተወላጆች የሆኑት እንደ ጉተማ ሀዋሰ፣ በባሳ ገዳ፣ ረጋቱ ሮባ፣ አሰሊ ኦሮሞ፣ ሀምቢሳ ሰሌ እና ሌሎች የኦነግ አመራሮችን ታሪክ አየሰማሁ ማደጌ፣ የእሱን ፈለግ በመከተል የቤተሰቤ ኩራት አንድሆን አድርጎም ይሆናል።

የአንደኛ ደረጃ ትምህርት ቤት መምህራኖቻችን ስለ ኦሮሞ የጭቆና ታሪክ እና የታጋዮች ገድል በጨቅላ የልጅነት አእምሯችን በማሥረጽ ታጋይ ለመሆን ያለኝ ሕልም እንዲጎለብት አድርገዋል። በጊዜው የነበሩት አስተማሪዎች ለመጀመሪያ ጊዜ በአፋን ኦሮሞ ለማስተማር የሰለጠኑ ስለሆኑ ጠንካራ ብሔርተኞች ነበሩ። ከመደበኛው ትምህርት ጎን ለጎን የተማሪዎቹን ንቃተ-ኅሊና ለማሳደግ ብዙ ጥረት ያደርጋሉ። እኔ ደግሞ ፓለቲካዊ ወሬዎችን ለመስማት ከፍተኛ ፍላጎት ስለነበረኝ ከትምህርት ሰዓት ውጪ መምህራን፣ የግብርና ልማት ሠራተኞች እና የጤና ባለሞያዎች ጋር በመሄድ ማዳመጥ ልማዴ ነው።

ዕድሜዬ ከፍ እያለ ሲሄድ ሁኔታዎች ተለውጠው ኦነግ ከአካባቢያችን እየራቀና ወደእነሱ ለመቀላቀል የነበረኝ ምኞትም አየሟሸሸ ቢመጣም፡ ከልጅነቴ ጀምሮ ትግል ውስጥ ለመሳተፍ የነበረኝ ጽኑ ስሜት ግን ከውሰጤ አልጠፋም። አዳማ ከገባሁ በኋላ የኦነግ ካድሬዎች ተብለው ከተላኩብን ሰዎች የተመለከትኩት ነገር ድርጅቱ ላይ ያለኝን አመለካከት ጥርጣሬ ውስጥ መክተት ጀመረ። በልጅነቴ የማውቃቸው የኦሮሞ ነጻነት ግንባር ወታደሮች ላይ ያየሁትን ሥነ ምግባር፡ የሕዝብ ፍቅር እና ቆራጥነት የኦነግ ካድሬዎች ተብለው የተላኩት ላይ ማጣቴ ልቤን ሰበረው።

ይባስ ብሎ ኦነግ በተለያዩ አንጃዎች መከፋፈሉና ስማቸውን አየሰማን ያደግን ጉምቱ አመራሮች እንደ VOA ባሉ ሚዲያዎች ላይ ቀርበው በአደባባይ ሲወጋገዙ መሰማቴ ተሰፋዬ ላይ ጥቁር ጥላ አጠላበት። ወደ ሲንጋፖር ስሄድ አንጃዎቹ በድረ-ገፆች የሚያደርጉትን እርስ በእርስ የመወጋገዝ ዘመቻ ሰመለከት በኦነግ የሚመራው የሕዝብ ትግል ከፍተኛ ችግር ውስጥ አንዳለ ተረዳሁ። የኦሮሞ ትግል የሚመራበት አደረጃጀት፡ የአመራሩ ብቃት እና ትግሉ የሚከተለው ሰትራቴጂ ውጤታማነት ላይ ጥርጣሬዬ እየጠነከረ ባለበት ሁኔታ፡ ወደ አሜሪካ ሄጄ ዩኒቨርሲቲው ውስጥ ከሰላማዊ ትግል ታሪክ እና ስልት ጋር ተዋዋቅኩ። ይህም ከትጥቅ ትግል ውጪ ጨቋኝ ሥርዓትን ለማሰወገድ የሚያስችል ሌላ አማራጭ አንዳለ እንድገነዘብ ረዳኝ። በዚህ ሁኔታ ላይ ሳለሁ የወቅቱ የኢትዮጵያ አምባንነን መሪ መለስ ዜናዊ ከዚህ ዓለም በሞት

ተለየ የሚል ዜና ተሰማ። የመለሰ ሞት ለአቅዴ ተግዳሮችት እና ዕድል በአንድ ላይ የጋበዘ መስሎ ታየኝ። ተግዳሮቱ ሳዘጋጅ የነበረው ሰትራቴጂ በአንድ ሰው የበላይነት የሚመራ አምባንነናዊ ሥርዓት (Personalistic Dictatorship/Autocracy) ማሰወገድ የሚቻልበት ሁኔታ ላይ ያተኮረ መሆኑ ነው። አንዲህ ባለው አምባገነናዊ ሥርዓት ሥልጣን በአንድ ግለሰብ እጅ የተጠራቀመ ስለሆነ የሚደረገው የሰላማዊ ትግል ዘመቻም በዚያ መሪ ላይ ያነጣጠረ ይሆናል። በሕዝብ ላይ የሚፈጸሙ በደሎችን ከመሪው ጋር ብቻ አያይዞ በማቅረብ ያለውን ቅቡልነት እንዲያጣ በማድረግ ከሥርዓቱ መነጠል ላይ ያተኩራል። የሚሰራው ፕሮፖጋንዳ ያን ውሰብሰብ የሆነን መንግሥታዊ ሥርዓት በአንድ ግለሰብ አምሳያ (personification) በሕዝቡ አእምሮ ውስጥ መሳል ላይ ያነጣጥራል። ይህ ስልት ሕዝቡ የመንግሥትን ትልቅ እና ውስብሰብ መዋቅር ቀለል አድርጎ እንዲመለከት ያስችላል። እንዲህ ዓይነቱ ዘመቻ ሲጠናከር አምባገነኑ ራሱን ለማዳን ለሕዝቡ ጥያቄ ምላሽ ይሰጣል ወይም የሥርዓቱ ባለሥልጣናት ሰውዬውን እንደ ጠንቅ (liability) በማየት ከሥልጣን ወደማሰወገድ ይሄዳሉ። ይህ ካልሆነ ደግሞ የማዕከላዊው እና የታችኛው መዋቅር በአገዛዙ ዕድሜ ላይ ጥርጣሬ በማሳደር ወደ ሕዝባዊ ትግሉ እንዲቀለቀሉ ያደርጋል። ይሀም የሥርዓቱን አቅም በማሽመድመድ ውድቀቱን ያፋጥናል።

ሁለተኛው የአምባገነን ሥርዓት ሥልጣን በፓርቲ ወይም በጦር ቡድን (junta) በተደራጁ ጥቂት ሰዎች (oligarchy) እጅ ሲኖር ነው። በ2001 የሕወሓት አመራር ከመከፋፈሉ በፊት፣ ኢትዮጵያ በእንዲህ ዓይነት የቡድን አመራር ባለው አምባገነናዊ ሥርዓት ትመራ ነበር። ከክፍፍሉ በኋላ መለስ ባለንጣዎቹን አሰወግዶ ሥልጣኑን ሰለጠቀለለ እስከ ዕለተ ሞቱ ድረስ ኢትዮጵያ ትመራ የነበረው በግለሰባዊ አምባገነን አገዛዝ ነው። ሳብላላው የቆየሁት እና በማቀድ ብዙ የለፋሁበት የትግል ስልት የመለሰ ዜናዊ ግለሰባዊ አምባገነን ሥርዓት ላይ ያነጣጠረ ስለነበር፣ የመለሰ ሞት እቅደ ላይ ቀዝቃዛ ውሀ ቸለሰበት።

የመለሰን ሞት ተከትሎ የሕወሓት/ኢሕአዴግ ሥርዓት ከአንድ ሰው ወደ ቡድናዊ አገዛዝ ተቀየረ። ኃይለማርያም ደሳለኝ ለይሰሙላ በመለስ ቦታ ቢተካም ፍጹም ሥልጣን (Absolute Power) ሊኖረው አልቻለም። ይህ ብቻ ሳይሆን በመለስ ጊዜ ሕወሓት በግልጽ የሚታይ የበላይነት ስለነበረው አገዛዙን በብሔር መድሎ ለመክሰሰ ቀላል ነው። ከመለሰ ሞት በኋላ የሕወሓት የበላይነት የቀጠለ ቢሆንም ኃይለማርያም ከኦሮሞ በባሰ ከተጨቆነ ብሔር የወጣ ስለነበር ሥርዓቱን በብሔር መድሎ መክሰሰ አዳጋች አደረገው። በተጨማሪም ኃይለማርያም አምባገነናዊ ሰብዕና ሰለማይታይበት አምባገነናዊ ሥርዓቱን በእሱ መሳል አሰቸጋሪ ሆነ። በእነዚህ ምክንያቶች የትግል ስልቱን ከግለሰባዊ አምባገነንነት ወደ ቡድናዊ አምባገነንነት (oligarchy) መቀየር ግዴታ ሆነ።

የመለሰ ሞት ከተግዳሮቱ ባሻገር ዕድልም ይዞልን መጣ። መለስ ከሀያ እንድ ዓመታት በላይ የፖለቲካ ሥልጣን ብቻ ሳይሆን የኢትዮጵያን የፖለቲካ ተዋስዖ (Political Discourse) በበላይነት ተቆጣጥሮ ነበር። የአምባገነንነት ሥልጣኑን ከአውቀት/ችሎታ

ጋር አዳብሎ ከእሱ አስተያየት ውጪ የሌላው ተደማጭነት እንዳያገኝ ማድረግ ችሏል19። የእርሱ የበላይነት (domination) ሌሎች ተወዳዳሪ እና ተገዳዳሪ ሐሳቦችን እንዳያፈልቁን በማቀጨጭ በሥረዓቱ ላይ የሚደረገውን ትግል በእጅጉ ጎድቶታል። የመለሰ ሞት ትልቅየፖለቲካ ክፍተት በመፍጠር አዲስ እና የተለየ ሐሳብ አድማጭ እንዲያገኝ ዕድል ከፈተ። ይህን በመረዳት እሱ ከሞተ ዕለት አንሰቶ የኦሮሞ ምሁራንን በዚህ ዕድል ተጠቅመን ለኢትዮጵያ የፖለቲካ አጀንዳ በመቅረጽ መለሰ ትቶት የሄደውን ክፍተት መሙላት አለብን በማለት መወትወት ጀመርኩ።

በዚሁ ወቅት ባለፈው ምዕራፍ ውስጥ የተጠቀሰውን ለረጅም ጊዜ ሳዘጋጅ የቆየሁትን "Transforming the Oromo Movement" የተሰኘውን የቅድመ ትግል ስልታዊ ዳሰሳ ጽሑፍ ለምሁራን እና ታጋዮች አሰራጭቼ እንዲወያዩበት አደረኩ። ጽሑፉ በቀጣይምለሰራኋቸው ሥራዎች መሠረት ስለሆነ አሳጥሬ ለመግለጽ አሞክራለሁ።

ጽሑፉ ከ1583 ዓ.ም ወዲህ የኦሮሞ ሕዝብ ያስተናገዳቸውን ማኅበራዊ እና ፖለቲካዊ ለውጦች በመዳሰሰ የትግል ሰትራቴጂ ለውጥ ማድረግ  እንደሚያሰፈልግ ይጠቁማል። በፖለቲካ ረገድ ከ2393 ዓ.ም በፊት የነበሩት የኢትዮጵያ ገዢ ቡድኖች ቀጥተኛ አገዛዝ (Direct Rule) ይከተሉ ነበር። በሌላ አነጋገር የማዕከላዊ ሥልጣን የተቆጣጠረው ልሂቅ፡ የመንግሥትን መዋቅር ከላይ እስከታች በራሱ ብሔር/ወገኖች በመሙላት ያሥተዳድር ነበር። የአምባገነኑ ቁንጮ የሆኑት ልሂቃን እና በየሰፈሩ ተሰማርተው የመንግሥትን ዓላማ የሚፈጽሙት ባብዛኛው ከአንድ ብሔር መሆናቸው ጭቁኑ ሕዝብ በቀላሉ አንድ አድርጎ እንዲገነዘባቸው ያስችላል። ይህ ገዢ ቡድኖች የብሔር ወገኖቻቸውን በማሰማራት በቀጥታ የሚያሰተዳድሩበት ሁኔታ በብሔሮች አምቢተኝነት መቀጠል ካቃተው በኋላ የመጣው የሕወሕት/ኢሕአዴግ መንግሥት ደግሞ የእጅ-አዙር አገዛዝ (Indirect Rule) መጠቀም መረጠ።

በዚህ ረገድ የአማራ ገዢ መደቦች የራሳቸው የብሔር ወገን የሆኑትን ወታደሮች እና አስተዳዳሪዎች ከላይ አስከታች ይመድቡ የነበረ ሲሆን፣ ሕወሓት ግን ማዕከላዊ ሥልጣንን በበላይነት ቢይዝም በታችኛው የመንግሥት አሥተዳደር እርከን የትግራይ ተወላጆችን መመደብ ሳያሰፈልገው በኦሕዴድ ሥር ባደራጃቸው ኦሮሞዎች (ጥገኛ ድርጅትን በመጠቀም) መቆጣጠርን መረጠ። በቀድሞው ሥርዓት ከላይ አስከታች የሚያስተዳድሩት ሰዎች የብሔር ማንነታቸው ከሚያሰተዳድሩት ሕዝብ የተለየ ስለሆነ፣ የጨቋኝ-ተጨቋኝ ማንነት ግልጽ ነበር። ሕወሓት ግን ከኦሕዴድ ጀርባ ሰለተደበቀና በቀጥታ ከሕዝብ ጋር ተገናኝተው ጭቆናን የሚፈጽሙት ኦሮሞዎች ሰለነበሩ የጨቋኙ ልሂቅ ከሕዝቡ የተደበቀ ነው። ይህንን ልዩነት የበለጠ ለማሰረዳትና በቀጥተኛ አገዛዝ እና በእጅ አዙር አገዛዞች ዘመን የኦሮሞን ሕዝብ ትግል የመሩ ሰዎች ሊገጥማቸው የሚችለውን ተግዳሮት ለማሳየት የሚከተለውን ምሳሌ ሰጠሁ።

19 ከልጅነቴ ጀምሮ የመለሰን ንግግሮች ቁጭ ብዬ ሳዳምጥ ነው ያደኩት። የሁለተኛ ደረጃ ተማሪ ሳለሁ ጀምሮ አብዮታዊ ዴሞክራሲን (Revolutionary Democracy) ጨምሮ ብዙ ጽሑፎቹን እንብቢያለሁ። በመለሰ የበላይነት የሚመራውን ሥርዓት ለማሸነፍ ሰውዬውን ማወቅ አሰፈላጊ ነው ብዬ አምን ነበር እንዲያውም ኮሌጅ እያለሁ መለሰ እና ሕወሓትን በዋነኝነት፣ ኦሕዴድን በሁለተኝነት እከታተል እና አጠና ስለነበር፤ ሚጀሬ ወያኖሎጂ ማይነሬ ደግሞ ኦፒዲዮሎጂ እንደሆነ ይቀልዱብኝ ነበር። ነዓጅ ሆኖ ሕወሓትን ለሥልጣን ያበቅው የትግራይ ብሔርተኝነት ላይ ጥናት በማድረግ "Tigrian Nationalism from Resistance To Weapon of Repression" በሚል ርዕሰ ጽሑፍ አዘጋጅቼ፣ በ2010 በኢንተርኔት አሰራጭቻለሁ። የጽሑፉ አንኳር መልዕክት የሕወሓት/ኢሕአዴግ ሥርዓትን ለመጣል፣ ሕወሓትን በዋናነት ደግሞ መለሰን ከማኅበረሰባዊ መሠረቱ መነጠል ላይ ማተኮር አለብን የሚል ነበር።

ሁለት አመራሮች በተመሳሳይ ከተማ ነገር ግን በተለያየ የአገዛዝ ዘመን ስለጭቆና ለሕዝብ ንግግር አደረጉ እንበል። ጄኔራል ታደሥ ብሩ በ1975፣ አቶ ገላሳ ዲልቦ ደግሞ በ1992 ዓ.ም በአርሲዋ ዴራ ከተማ በሠላሳ ዓመት ልዩነት ሕዝብ ሰብሰበው ተመሳሳይ ንግግር እንዳካሄዱ አናስብ። ጄኔራል ታደሠ የነበረውን ሥርዓት ክፋት ለማስገንዘብ «የአማራ ገዢ መደብ ቋንቋህን አግዶ በስማ በለው እንድትዳኝ አሰገደደህ፣ በገዛ እርሻህ ላይ በእርቦና ሲሶ ምርትህን ዘረፈህ» ብሉ ቢናገር ሕዝቡ በቀለላሉ ሊረዳው ይችለል። ጄኔራል ታደሠ «የአማራ ገዢ መደብ ጨቋኝ መንግሥትን ሲል ሕዝቡ የሚያሰበው በአካባቢው ያለውን ዳኛ፣ ፖሊስ እና ሊቀመንበር ነው። ለተራው ሕዝብ መንግሥት ማለት ቀን በቀን የአሥተዳደር ሥራ የሚፈጽመው ነው።

በተቃራኒው ገላሳ በ1992 ወደ ዴራ ከተማ በመሄድ «አየጨቆናችሁ እና አየዘረፋችሁ ያለው የትግሬ ገዢ መደብ ነው» ብሉ ቢናገር ሕዝቡ በቀላሉ ሊረዳው አይችልም። ምክንያቱም በወቅቱ ዴራ ላይ ሊቀመንበር፣ዳኛ እና ፖሊስ ሆኖ የመንግሥትን ጭቆና ሲያሰፈጽም የሚያዩት ገለሳ የሚከሰው ትግሬ ሳይሆን ከአብራካቸው የወጣ፣ ቋንቋቸውን የሚናገር ብሔሩ ኦሮሞ የሆነ ግለሰብ ነው። ሰለዚሀም የኦሮሞ ትግል በ1570ዎቹ ሕዝቡን ሲያነሳሳበት እና ጭቆናን ሲፋለምበት የነበረው መንገድ በ1990ዎቹ ውጤታማ ሊሆን አይችልም፤ አልቻለምም። ቀጥተኛ ጭቆናዊ አገዛዝን እና የእጅ አዙር አገዛዝን በተመሳሳይ መንገድ እና ስልት መታገል ውጤት እንደማያመጣ በመረዳት ለውጥ አለመደረጉ ለትግሉ መቀጨጭ ጉልሀ ሚና ተጫውቷል። ይህም የቅድመ ትግል ስልታዊ ዳሰሳው በቀጣይ የሚደርገውን ትግል ውጤታማነት ለማረጋገጥ
ሰትራቴጂያችንን የእጅ አዙር አገዛዝን ለመታገል ወደሚያስችል ቀመር መቀየር እንዳለብን ይጠቁማል።

የጨቋኝ ሥርዓቱ መለወጥ ብቻ ሳይሆን፣ የምንታገልለት ሕዝብ ውስጥ የተሰተዋሉ ማኅበራዊ ኢኮኖሚያዊ እና ፖለቲካዊ ለውጦችም በቅድመ-ትግል ዳሰሳው ውስጥ ተካተዋል። በዚሀ ረገድ እየታገልነው ያለው የጨቋኝ ሥርዓት ወደ ሥልጣን ከመጣ አንሰቶ ዳሰሳው አስከተሰራበት ወቅት (ከ1951-2010) የኦሮሞ ሕዝብ ያሰተናገዳቸው እና ለትግሉ ወሳኝ የሆኑ ዋና ዋና ለውጦች በጽሑፉ በሦስት ተከፍለው ቀርበዋል።

1. *ሕጻናት በአፍ መፍቻ ቋንቋቸው መማር መቻላቸው* (mass Literacy in mother tongue)

2. *የኦሮሚያ ክልል መፈጠርን ተከትሎ የመንግሥት አሥተዳደራዊ መዋቅር መገንባቱ* (Bureaucratization)

3. *የከተማ መስፋፋት እና በከተማ የሚኖር ኦሮሞ ቁጥር ከጊዜ ወደ ጊዜ እያደገ መምጣቱ* (Urbanization) *ናቸው።*

ባለፉት ምዕራፎች ወሰጥ እንደተገለጸው፣ እስከ 1983ዓ.ም የነበሩ አገዛዞች፣ የኦሮሞን እና ሌሎች ጭቁን ብሔሮችን ማንነት በመጨፍልቅ፣ አንድ ወጥ ሀገራዊ ማንነት ለመገንበት ባላቸው አቅድ መሠረት፣ አፋን ኦሮሞን የትምህርት እና የሥራ ቋንቋ እንዳይሆን አግደዋል። ኦሮሞን ከሚያሰተሳሰሩት መሰተጋብሮች ውስጥ አንዱ አፋን ኦሮሞ በመሆኑ፣ የኦሮሞን የጋራ ማንነት አጠናክሮ ለጋራ ትግል ለማሰልፍ ሲባል፣ ቋንቋውን ከጭቆና ማላቀቅ እና ማሳደግ የትግሉ ግንባር ቀደም ሥራ ነበር። ለዚሁ ነበር ቀደምት ታጋዮች ገና ከጠዋቱ የላቲን ፊደልን ለአፋን ኦሮሞ ሊያገለግለ በሚችል መልኩ በመጠቀም ቁቤን ቀርጸው በኅቡዕ ማሰተማርን እንደ ቁልፍ

የትግል እርምጃ የወሰዱት። በ1983 ዓ.ም ለውጥ  እንደመጣ አፋን ኦሮሞ የኦሮሚያ ክልል የሥራና የትምህርት ቋንቋ ሲሆን በኅቡዕ ሲካሄድ የነበረው ተግባር ኦፊሴላዊ ፓሊሲ ሆነ።

መጻፍና ማንበብ የአንድን ሕዝብ ብሔርተኝነት በማጠናከር ረገድ ከፍተኛ ሚና አላቸው። እንዲያውም ብሔርተኝነት የፖለቲካ ኃይል መሆን የቻለው በ19ኛው ክፍለ ዘመን የተከሰተው የኢንዱስትሪ አብየት (industrial revolution) ጽሑፍን በማሽን ማዘጋጀት አፅችሎ፣ ሐሳቦች በሥነ ጽሑፍ በተለይም በጋዜጦች መስፋፋት ከመቻላቸው ጋር ተያይዞ እንደሆነ ይታመናል። ከሥነ ጽሑፍ ዕደገት እና መሰፋፋት በፊት በማኅበረሰቦች መካከል ተቆርቋሪነትና አጋርነት (solidarity) የሚኖረው በደም ትሰሰርና በአካባቢ ቅርርብ ነበር። ይህ ማለት አንድ ሰው ሲጠቃ ሌላው ሊያግዘው የሚተባበረው ጥቃቱ የተፈጸመው በአንድ አካባቢ በሰፈሩና የሥጋ ዝምድና ባላቸው ላይ ከሆነ ነው። በሁለት ሰዎች ወይም ቡድኖች መካከል ያለው መልክዓ ምድራዊ አቀማምጥ ወይም የሕዝብ ብዛት አየጨመረ በሄደ ቁጥር፡ የሚኖራቸው ትሰሰር፣ ትብብር እና አጋርነት አየቀነሰ ሄዶ ባዳነትን ያሰከትላል።

የማተሚያ ማሽን መምጣትን የተከተለው የሥነ ጽሑፍ መስፋፋት፣ ለሰዎች ትሰሰር እና ትብብር የአካላዊ ቀረቤታን አሰፈላጊነት ኢምንት አደረገው። ቀደም ሲል በቦታ ርቀት እና፣በመሬት አቀማመጥ ምክንያት ግኑንነታቸው የተቋረጠ ሰዎች በሥነ ጽሑፍ ዕድገት ምክንያት የቀድሞ ትሰሰራቸውን ማሳደግ ቻሉ።

በመጻሕፍት እናጋዜጦች ታትሞ የሚሰራጭ የጋራ ታሪክ አሁናዊ ጥቅም አንዳለው በመረዳት የጋራ ማንነታቸው ጎለበተ። ተራርቀው ያሉ ሰዎች በሥነ ጽሑፍ ምክንያት የጋራ ማንነታቸውን እንዲገነዘቡ መቻለቸው፡ አንዱ ሌላውን በአካል አይቶትም ባያውቅ፣ ካነበበው በመነሳት ብቻ ለመተዛዘን እና ለመተጋገዝ በቁ። ለዚህ ማሰረጃው፡ የማተሚያ ማሽን ከመጣ ወዲህ ብሔርተኝነት በአውሮፓ በሰፋት መቀጣጠሉና ብሔሮች ለመብታቸው መታገል መጀመራቸው አንዲሁም የራሰን ዕድል በራስ የመወሰን ጥያቄ ዓለም አቀፍ አጀንዳ መሆኑ ነው።

በተመሳሳይ መልኩ ከ1983 ዓ.ም በኋላ፣ ትምህርት እና ሥራ በአፋን ኦሮሞ መሆኑ፡ የኦሮሞ ብሔርተንነት አንዲሰፋፋና አንዲጠናከር ከፍተኛ ሚና ተጫውቷል። ኦሮሚያ ውስጥ ያሉ ተማሪዎች ሰኞ ጠዋት ከአጽናፍ እስከ አጽናፍ ተመሳሳይ የኦሮሚያ መዝሙር መዘመራቸው፡ ክፍል በመግባት ከተመሳሳይ መጽሐፍ በጋራ ቋንቋ መማራቸው፡ በአካል ቢራራቁም አእምሯቸው በተመሳሳይ መልኩ አየተቀረጸ አንዲያድጉ አስችሏል። ይህ ደግሞ አዲሱትውልድ የደም ዝምድና እና ጉርብታና ሳያሰፈልገው፡ በመካከሉ የሥነ-ልቦና እና የህልውና ትሰሰር(metaphysical connection) አንዲፈጥር አሰቻለ።

እንደ ኦሮሞ በቁጥር እና በአሰፋፈር ግዙፍ የሆነ ማኅበረሰብ በጉርብትና እና ዝምድና ላይ ከተመሠረተ ትብብር ይልቅ፣ የልቦና ትስስር የበለጠ ይጠቅመዋል። ምክንያቱም የጋራ ታሪኩን፣ ባሕሉን፡ ከፍታ እና ዝቅታውን በማወቅ አእምሮው የተቀረጸ ሕዝብ በቦታ ርቀት ሳይገደብ ለጋራ ጉዳዮች በቀላሉ መሰባሰብና መረባረብ ሰለሚችል ነው። አዲሱ የኦሮሞ ትውልድ በመሬት አቀማመጥና በደም ትሰሰር ሳይሆን በቋንቋው መማሩ አንድ የሆነ ሥነ-ልቦናዊ ትስስር አንዲፈጥር አሰቻለው። በተለይ ኦሮሞ በቋንቋው መማር መጀመሩ ከትምህርት መስፋፋት (mass literacy) ጋር ሰለተገጣጠመ በቁጥሩ ግዙፍ የሆነ ብሔርተኛ "የቁቤ ትውልድ" ተፈጠረ።

ከ1983 ዓ.ም በኋላ በኦሮሞ ማኅበረሰብ ውስጥ የተከሰተው ሌላኛው ለውጥ የኦሮሚያ ክክልላዊ መንግሥት አሥተዳደር መፈጠሩ ነው። የቀደመው ሥርዓት የኦሮሞን የወል ማንነት ለማዳከም ከወሰዳቸው ሰልቶች አንዱ ኦሮሞን የጋራ አሥተዳደራዊ መዋቅር ማሳጣት ነበር። ይህ ተቀይሮ ኦሮሞ በስሙ የሚጠራ እና አብዛኛውን የብሔሩን ተወላጆች ያቀፈ አሥተዳደራዊ መዋቅር መመሥረቱ፣ የጋራ ማንነትን መልሶ ለመገንበት ብሎም ለጋራ ጥቅም ለመደራጀት አመቺ ሁኔታ ፈጠረ። የኦሮሞ ልሂቃን (elites) በአንድ መዋቅር ሥር ተጠቃልለው መሿሿም፡ መሻሻር፣ አብሮ መሥራት መጀመራቸው የጋራ ማንነት እንዲጎለብት እንዲሁም የጋራ ጥቅማቸው እንዲተሳሰር አደረገ።

በተጨማሪም የኦሮሚያ መፈጠር፣ በጎሳ እና በአካባቢ/በዞን ተከፋፍለውና ተራርቀው የነበሩ ኦሮሞዎች ቀን ተቀን በሚፈጥሩት መስተጋብር በሂደት እንዲዋሐዱ በማድረግ ክፍፍሉ እየቀነሰ አንድነቱ እየጠነከረ እንዲሄድ ትልቅ ሚና ተጫውቷል። በአፋን ኦሮሞ የሚገለገል የኦሮሚያ ክልል አሥተዳደራዊ መዋቅር መፈጠሩ፡ በመቶ ሺዎች ለሚቆጠሩ የሥራ ዕድል በመፍጠሩ፣ የኦሮሞ ማኅበረሰብ በደሞዝ የሚተዳደር አዲስ የሲቪል ሰርቫንት መደብ እንዲኖረው አሰችሎታል። ይህን ከጊዜ ወደ ጊዜ ቁጥሩ እየሰፋ የመጣ ደሞዝተኛ መደብ  እንደፔቲ ቡርዧ (Petty Bourgeoisie) ልንውሰድው የምንችል ሲሆን፡ ለኦሮሞ ማኅበረሰብ አዲስ ክሰተት ነው።

ሦሰተኛው የኦሮሞ ሕዝብ ያስተናገደው ለውጥ በከተማ የሚኖሩ የብሔሩ ተወላጆች ብዛት መጨመር ነው። ለረጅም ጊዜ ኦሮሞ ከከተማ ርቆ ይኖር ነበር። የመራቁ ምክንያት እንድም በሥርዓቱ መገፋቱ (push factors) ወይም ደግሞ በከተማ አለመሳቡ ነው። ሁሉምየኦሮሚያ ከተሞች በሚባል ደረጃ መጀመሪያ ላይ የጦር ሰፈር (garrison town) ሆነው የተቆረቆሩ ናቸው።

የኃይለሥለሴ እና የምኒሊክ ጦር ወታደራዊ መቀመጫ የነበሩ ቦታዎች በሂደት ወደ ከተማነት አድገዋል። ሰለዚህ የከተሞቹ ባሕል፣ ቋንቋ እና አኗኗር የወታደሮቹን ብሔር የሚያንጸባርቅ ስለነበር ኦሮሞ ለከተሞቹ አንግዳ ሆነ። ለከተሞቹ መሠረት የነበሩት ወታደራዊ ካምፖች የተቋቋሙበት ዓላማ፣ በዙሪያቸው ያለውን ኦሮሞ ለማስገበር እና እንዳያምጽ ለማፈን ስለነበር፣ በገጠር እና በከተማው መካከል በጥርጣሬ ላይ የተመሠረት ግንኙነት ተፈጠረ። ኦሮሞ ወደ ከተማ የሚሄደው ለግብይት፣፣ግብር ለመክፈል፣ለፍርድ ቤት ሙግት እና ለመታሰር እንጂ ለመኖር የሚሄደው በጣም ጥቂት ነው። ሰለዚህ ከተሞችን አይወድም ነበር። እስከ ቅርብ ጊዜ ድረሰ አንድ ሰው ከተሜ ነው ከተባለ፣ ለኦሮሞ ባሕል ባዳ የሆነ፣ ግብረ-ገብነትን የጣለ ተደርጎ ይታያል። ይሀ ሁኔታ ኦሮሞ ወደ ከተማ እንዳይሳብ ምክንያት ሆኗል። በተጨማሪም አብዛኛው ኦሮሞ በግብርና እናበ እርብቶ አደርነት ሰለሚተዳደር፤ በተቃራኒው ደግሞ ከተማን መሠረት ባደረጉ የንግድና ሌሎች የሥራ ዘርፎች ላይ ያለው ተሳትፎ ውስን በመሆኑ ወደ ከተማ የመሳብ ዕድሉን አጥብቦት ቆይቷል።

ከ1983 ዓ.ም በኋላ በከተማ የሚኖረው ኦሮሞ ቁጥር በፍጥነት ጨምሯል። ለዚሀ  እንደኛው ምክንያት ድሮ ኦሮሞ ወደ ከተማ እንዳይገባ ሲገፉት የነበሩ ምክንያቶች መቀነሳቸው ሲሆን፤ ሌላኛው ደገሞ የሕዝብ ቁጥር መጨመር እና የአርሻ መሬት ጥበት ከገጠር ወደ ከተማ  የሚደረገውን ፍልሰት ማባባሱ ነው። ከላይ  እንደተጠቀሰው የኦሮሚያ ክልላዊ መንግሥት

መቋቋሙና አፋን ኦሮሞ የሥራ ቋንቋ መሆኑ ኦሮሞዎች የመንግሥት ሥራ ዕድል እንዲያገኙ መንገድ ጠረገ። አብዛኛው የመንግሥት ሥራ ከተማ ሰለሚገኝ፣ እነዚህ ሠራተኞች ወደ ከተማ መግባታቸው ግድ ነው። የሥራ ዕድል ያገኙት ወደ ከተማ ሲገቡ፣ በተለይ ተማሪዎች የሆኑት ዘመዶቻቸው ጋር ተጠግተው ለመማር ይሄዳሉ። በተጨማሪም ኦሮሞዎች በመንግሥት መሥሪያ ቤት መብዛታቸው እና በአፋን ኦሮሞ መሥራታቸው፣ ትላንት የነበረው የከተማ እና የገጠሩ ነዋሪ ባሕላዊ እና ሥነ-ልቦናዊ መራራቅ እየጠበበ እንዲሄድ በማድረጉ፣ ከተሞች የገጠሩን ማኅበረሰብ ከመግፋት ይልቅ መሳብ ጀመሩ።

ትምህርት በአፋን ኦሮሞ መስጠት መጀመሩ የኦሮሞ ተማሪዎች ቁጥር በአጥፍ እንዲጨምር አድርጎ። እነዚህ ተማሪዎች የሁለተኛ ደረጃ እና የዩኒቨርሲቲ ትምህርታቸውን ለመማር ወደ ከተማ መፍለስ ሰለሚኖርባቸው፣ ከተመረቁ በኋላ የሥራ ዕድል ለመፈለግ ወይም ሥራ ለመያዝ እዚያው ከተማ ይቀራሉ። የተቀሩት ደግሞ በተለያዩ የኦሮሚያ ገጠሮች ውስጥ በመቀጠር በተማሩት ሙያ ማኅበረሰባቸውን ያገለግላሉ።

በአጠቃላይ ከላይ የተጠቀሱት ለውጦች ፣ የኦሮሞ ሕዝብ ከ1983 ዓ.ም ወዲህ መሠረታዊ በሆነ የማኅበረሰብ ለውጥ (fundamental transformation) ውስጥ እንዲያልፍ አስችለውታል።

የቅደመ-ትግል ሰልታዊ ዳሰሳው እነዚህን ለውጦች በአሃዝ በተደገፈ መረጃ በማሳየት፤ ወደፊት የሚኖረው የትግል ስልት ለውጦቹን ከግምት ያስገባ መሆን እንዳለበት ይመክራል። ለውጦቹ በ1960ዎቹ ትግሉ ሲደመር እና በ2010 የቅድመ ትግል ዳሰሰው ሲደረግ ሰፊ ኢኮኖሚያዊ፣ ማኅበራዊ እና ሥነ-ልቦናዊ ልዩነት እንዲፈጠር አድርገዋል። ሰለዚህ 1970ዎቹን ነባራዊ ሁኔታዎች ተንተርሶ የወጣ የትግል ስልት በ2010ቹ በሚኖር ማኅበረሰብ ውስጥ ቢተገበር ውጤታማ የመሆን ዕድሉ ጠባብ ነው። አዲሰ የተፈጠረውን ነባራዊ ሁኔታ መሠረት ያደረገ ስልት መንደፍ አሰፈላጊ ነው።

ለምሰሌ የድሮው የትግል ስልት የገጠሩ ማኅበረሰብ ላይ የተመሠረተ ነው። ምክንያቱም ከተሜው ኦሮሞ ጥቂት በመሆኑ ብቻ ሳይሆን፣ መንግሥት በገጠሩ ሕዝብ ላይ የነበረው ቁጥጥር የላላ ስለነበር አማጺያን በቀላሉ መደበቅ እና መንቀሳቀሰ ይችላሉ። አሁን ግን  እንደ መንገድ እና ቴሌኮሙኒኬሽን ያሉ መሠረተ ልማቶች በመስፋፋታቸው መንግሥት በገጠር የሚደረጉ እንቅስቃሴዎች ላይ መረጃ ለመሰብሰብ እና ፈጣን አርምጃ ለመውሰድ ያስችሉታል።

በተቃራኒው የከተማው ማኅበረሰብ ብዛትና ንቃት ሰለጨመረ ታጋዮች አራሳቸውን በቀላሉ ደብቀው መንቀሳቀስ ይችላሉ። እንዲሁም አዲስ የተፈጠረው ደሞዝተኛ መደብ፣ በግብርና ከሚተዳደረው የተለየ ባሕርይ አለው። ይኸውም ከድህነት ወለል ትንሽ ከፍ ያለ ምቾት ያለው ሕይወት ሰለቀመሰ፣ አሁን በደረሰበት የሕይወት ደረጃ ላይ መጨመር እንጂ ማሽቆልቆል አይፈልግም። ሰለዚህ አሁን ያለበትን የኑሮ ደረጃ ለአደጋ በሚያጋልጡ እና ከፍተኛ መሥዋዕትነት በሚጠይቁ የትግል ሰልቶች ላይ መሳተፍ አይሻም። የትጥቅ ትግል ደግሞ ለወታደሮቹ ይቅርና በሎጂሰቲክ ለሚደግፉት እንኳ እስከ ሕይወት የሚደርስ መሥዋዕትነት ሊያስከትል ይችላል። ከዚህ በመነሳት ትግሉ ከተማን ማዕከል ወዳደረገ ስልት መሸጋገር አለበት።

የቅድመ ትግል ዳሰሳው አምባገነኑ ሥርዓት የሚጠቀምባቸውን ሰልቶች እና የኦሮሞ ሕዝብ ያለፈባቸውን ለውጦች ከተነተነ በኋላ «ከትጥቅ እና ከሰላማዊ ትግል የትኛው ይሻላል?" የሚለውን ጥያቄ ወደ መመለስ ያመራል። የአምባገነናዊ ሥርዓት ስልት ከቀጥተኛ ወደ

እጅ አዙር አገዛዝ መለወጡ የትጥቅ ትግልን አስቸጋሪ ያደርገዋል። ምክንያቱም መግደል ያለብህ እንደበፊቱ የውጪ ኃይልን ሳይሆን የገዛ ዘመድህን ስለሚሆን በራስህ ሕዝብ ውስጥ መከፋፈልን ያመጣል። አንድ ኅብረተሰብ የውጪ ጠላትን ለመውጋት የሚተባበረውን ያህል፤ የፈለገ ክፉ ቢሆን አንኳ ከአብራኩ የወጣን አካል መግደል ላይ በአንድነት ሊቆም አይችልም። ስለዚህ ያንተኑ ወገን ገዝቶ ከጀርባ የተደበቀን አገዛዝ ለማሸነፍ ከትጥቅ ትግል ይልቅ ሰላማዊ ትግል የተሻለ ውጤት አለው።

ሰላማዊ ትግል ብዙ ሰው ስለሚያሳትፍ መሥዋዕትነትን በማከፋፈል (distributed risk) አደጋን ይቀንሳል። ከ1983 ዓ.ም በኋላ ማንበብ እና መጻፍ የሚችለው ኦሮሞ መብዛቱ፣ ከተሜነት መስፋፋቱ እና በቢሮክራሲው ውስጥ ያለው ቁጥር መጨመሩ ውጫዊ አመጽ እና ውስጣዊ ሸፍጥ (internal sabotage) በማቀናጀት ሰላማዊ ትግልን ለማሳካት ከፍተኛ እገዛ ያደርጋሉ። በጥቅሉ ለኦሮሞ ትግል የተሻለ የሚሆነው ስልት ሰላማዊ ትግል መሆኑን በቅድመ-ትግል ስልታዊ ዳሰሳው ደመደምኩ።

በአጠቃላይ በቅድመ-ትግል ሰልታዊ ዳሰሳው ላይ በመመስረት የቀጣዩ ምዕራፍ ትግል የሰላማዊ (ነፍጥ-አልባ)፣ ከተሞችን ያማከለ፣ መካከለኛ ገቢ ደረጃ ያለውን ማኅበረሰብ ያሳተፈ እና በኢኮኖሚ አጀንዳዎች ላይ የተመሰረተ እንዲሆን አቅጣጫዎችን አሰቀምጧል።

ይህንን የቅድመ-ትግል ትንታኔ ጽሑፍ ውጪ ላሉ ምሁራን አቅርቤ በሐሳብ ካዳበርኩት በኋላ ሀገር ውስጥ ላሉ ወጣቶች ልኬ ሰንወያይበት ቆየን። በጽሑፉ የተነሱትን ሐሳቦች ጠቅለል አድርጌ በተለያዩ ሰብሰባዎች ላይ አቀረብኩ። የተመረጡ ፅንሰ-ሐሳቦችን በማኅበራዊ ሚዲያ በማወያየትም ግንዛቤ ለመፍጠር ሞክሬያለሁ፣ በሂደትም ዝርዝር ሰልቶች እና አቅዶች ተዘጋጅተውለት ሥራ ላይ በመዋሉ ለተገኘው ውጤት ጉልህ ሚና አበርክቷል።

## 6.3.የሀይማኖት ጉዳይ

እ.አ.አ በ2011/12 የሕዝበ ሙስሊሙ ተቃውሞ ሲፈነዳ ስማረው እና ሳጠናው የቆየሁትን የሰላማዊ ትግል ስልት በሀገራችን ውስጥ ሥራ ላይ መዋል መቻል አለመቻሉን በቀጥታ ለመገምገም ጥሩ ዕድል አገኘሁ። የኢትዮጵያ መንግሥት አሕባሽ የሚባል የሀይማኖት አንጃ ከሊባኖስ አሰመጥቶ በሀይማኖት ጉዳይ ጣልቃ በመግባት መጅሊስ እና መስጂዶችን እንዲቆጣጠሩ ሙከራ ማድረጉ ሕዝቡን አስቆጥቶ ተቃውሞ ተጀመረ። የመንግሥት እርምጃ እና ሕዝባዊው ተቃውሞ በሀገሪቱ ፖለቲካ እንዲሁም በኦሮሞ ትግል ላይ ተጽዕኖ ማሳደሩ ስለማይቀር በቅርበት መከታተል አስፈላጊ ሆኖ ሰለታየኝ ከተቃውሞው አስተባባሪዎች ጋር  መገናኘት ጀመርኩ።

መንግሥት ሕዝባዊ ተቃውሞውን ከጽንፈኝነት እና ከአሸባሪነት ጋር በማያያዝ ፕሮፓጋንዳ ሲያሰራጭ ስለነበረ የውጪ መንግሥታት እና ሀገራት ዘንድ የተሳሳተ ግንዛቤ እንዳይፈጠር በማሰብ «Muslim Activism and Ethiopian State: Accommodation  Or Repression»20 በሚል ርዕሰ ጽሑፍ አዘጋጅቼ በኢንተርኔት አሰራጨሁ። ከሀገር ውስጥ እና ከውጪ ሆነው ትግሉን የሚያደራጁ ምሁራን እና ወጣቶችን በማነጋገር ተቃውሞው በሰላማዊ መንገድ ብቻ እንዲካሄድ መምከር ጀመርኩ፡ አጫጭር ሥልጠናም ሰጠኋቸው። በማኅበራዊ እና በመደበኛ ሚዲያዎች ሰለ ተቃውሞው መረጃ እና ትንታኔ በማቅረብ የመንግሥትን ፕሮፓጋንዳ በማክሸፍ ላይ በቀጥታ ተሳተፍኩ።

የብሔር ትግል ጥርሴን የነቀልኩበት ቢሆንም ለሀይማኖት መብት ትግል አዲስ ስለነበርኩ ተቃውሞው ከፈነዳ በኋላ በሂደት ብዙ ነገሮችን መማር ጀመርኩ። ከዚያ በፊት ስለሀይማኖት ጭቆና የነበረኝ ግንዛቤ ትንሽ ነበር። ኢትዮጵያ ውስጥ የሀይማኖት ጭቆና ቢኖርም በልጅነቴ በብሔር ከሚነሳ ቅሬታ እና ከሚደረግ ትግል ውጪ የሀይማኖት ጭቆና ለማየት እና ለመሰማት አልቻልኩም። ለዚህ ደግሞ የተለያዩ ምክንያቶች አሉ።  እንደኛው፡ የተወለድኩት የእስልምና እና የክርሰትና ሀይማኖት ከሚከተሉ ቤተሰቦች ስለሆነ ሁለቱም ወገኖች መቻቻልን ለማጎልበት ሰለሚሰሩ ብዙ ውዝግብ አልነበረም። እኛ ያደግነው ሙስሊም ወላጆቻችን ጋር ኢደል ፊጥር እና ኢደል አድሀ (አረፋ) ፤ ክርሰቲያን ወላጆቻችን ጋር ደግሞ መስቀል እና ጥምቀት እየተጠራን ነው።

የሁለቱን ሀይማኖቶች ልዩነት የማየው ሥጋ ላይ ብቻ ነበር፡ በዘመኑ 'የአስላም ሥጋ' እና 'የክርስቲያን ሥጋ' ተብሎ አንዳቸው የሌላኛቸውን አይበሉም። ቤተሰቦቻችን ይህን ችግር ለመቅረፍ የለቅሶ እና የሰርግ ቀን የሚያደርጉትን እስከ አሁንም አስታውሳለሁ። ለምሳሌ የሰርግ ድግስ ሲደረግ ወይም የቀብር ሥነ-ሥርዓት በሙስሊም ቤተሰብ ከተዘጋጀ፡ ክርስቲያኖች የሚገኙ ቢሆንም አብዛኛው ታዳሚ ሙስሊም ይሆናል፣ የክርስቲያኖቹም ቀን  እንደዛው። ይሁን እንጂ የአርድ ከብት ለሁለቱም የሀይማኖት ተከታዮች በቁጥር እና ብዛት/ ውፍረት እኩል መሆኑ ተረጋግጦ ይቀርባል። አንድ ቀን አያቴ ሁለት በሬ ቀርቦ  እንደኛው አጠር

ያለ በመሆኑ ተመልሶ አኩል የሆነ እንዲመጣ ወጣቶችን ሲያዛቸው አይቻለሁ።

የሙስሊሞች ሰርግ ወይም ለቅሶ ላይ አኩል ከብት ከታረደ የታዳሚዎች ቁጥር ትንሽ ስለሚሆን ክርስቲያኖቹ ችለው አይጨርሱም። እንዲህም ሆኖ ግን ሙስሊሞቹ ለሁለቱም እኩል በሬ በማዘጋጀት «ካልታረደ» ሰለሚሉ፣ ክርስቲያኖቹ «በልተን መጨረስ ስለማንችል ማባከን ተገቢ አይደለም» በማለት አነስ ያለ በሬ እንዲቀርብ ይማጸናሉ። ሙስሊሞቹ በተራቸው «ካልጨረሳችሁ ሥጋውን ለልጆች ይዛችሁ ትሄዳላችሁ» በማለት መታረድ እንዳለበት ይከራከራሉ። ክርስቲያኖቹ «አባካችሁ ሰለ እግዚአብሔር ሥጋውን ይዘን ለመግባት ቦታው ሩቅ ነው። በዚያ ላይ ተራራውን ተሸክመን መውጣት አንችልም፡ እሺ በሉን» በማለት ይለማመጣሉ። ሽማግሌዎቹ ተከራክረው ሲጨርሱ አነስ ያለ በሬ ወይም የፍየል/የበግ ሙክት አምጥተው ለክርስቲያኖቹ ያርዳሉ። የክርስቲያኖቹ ሰርግ ወይም ለቅሶ ሲሆንም ተመሳሳይ ትዕይንት እመለከት ነበር።

ይህ የሚያሳየው አንዱ የሌለውን ሀይማኖት ለማክበር የሚሄዱበትን ርቀት ነው። በልጅነቴ ወደ ሁለቱም አያቶቼ ቤት ሰለምሄድ በሁለቱም ወገን የታረደ ሥጋ እበላ ነበር፡ እናቴ ልትከለክለኝ ሞክራ አልቻለችም። እንዲያውም ከራሴ አልፎ ሌሎች የሚበሉበትን ዘዴ እፈልግ ነበር። የሰርግ ወይም የለቅሶ ቀን የሁለቱም ወገን ሽማግሌዎች የሚታረደው ከብት ላይ ከተሰማሙ በኋላ ለየብቻ ታርዶ ይዘጋጃል።

እንግዶቹ ቢላዋ ከሌላቸው፣ ቤት ያለውን ቢለዋ በአፈር ሰባት ጊዜ አጥበው ይጠቀማሉ። ወንዶቹ አርደው ጉበት ከተበላ በኋላ ለሴቶቹ ወጥ እንዲሰሩ ይሰጣል። ከብቶቹ በተለያየ ቢላ እና የተራራቀ ቦታ ቢታረዱም የማብሰያው ቦታ በአንድ ዳስ ውስጥ ጎን ለጎን ይሆናል። ታዲያ እኔ እና አንዳንድ ልጆች ሴቶቹ ሲያበስሉ አጠገባቸው እየሄደን እንቀላውጣለን። እነሱም «አሰኪ ጨው እንዳለው ቅመሱ› ብለው ይሰጡናል። ሴቶቹ እንደ አጋጣሚ ወጣ በሚሉበት ጊዜ ከአንዱ ድስት ወደ ሌላኛው በፍጥነት ገልብጬ በማንኪያ አቀላቅለዋለሁ። ወይም አንድ ሥጋ ከክርሰቲያኖቹ ድስት አውጥቼ የሙስሊሞቹ ድሰት ውስጥ፣ የሙስሊሞቹን ደግሞ የክርሰቲያኖቹ ድሰት ውስጥ እሰቀምጣለሁ። ሕዝቡ ከበላ በኋላ ያደረኩትን ስናገር ሰፈር ውስጥ እያባረሩ ይገርፉኛል። ሰለዚህ በልጅነቴ ያየሁት ትልቁ የሀይማኖት ልዩነት ሥጋው ነው። የብሔር መድሎ ቅሬታዎችን ስሰማ ያደኩ ሲሆን፣ የሀይማኖት ግን ሰምቼ አላውቅም።

የሀይማኖት ተጽዕኖ መኖሩን ለመጀመሪያ ጊዜ የተረዳሁት አዳማ በምማርበት ወቅት ነበር። አንድ ቀን ትምህርት ቤት በር ላይ ስደርሰ መግቢያው ፊትለፊት ቆመው የሚያለቅሱ ሴቶችን ስላየሁ በድንጋጤ ምን እንደሆኑ ጠየኳቸው። «ሂጃብ ካላወለቃችሁ አትገቡም አሉን» በማለት ነገሩኝ። «እናንተ ብታወልቁ ምን ችግር አለው?» ሰላቸው ሀይማኖታችን ይከለክለናል አሉኝ። በወቅቱ የሂጃብን አሰፈለጊነት ሰለማላውቅ ነበር የጠየኩት። እስከማሰታውሰው ድረስ
ባደኩበት አካባቢ አንዷት ሴት ጸጉሯን የምትሸፍነው ማግባቷን ለማሳየት ነው። ያላገባች ሴት ጸጉሯን አትሸፍንም፡ ሹሩባ ተሰርታ፣ ጸጉሯን አያዘናፈለች፡ የወጣቱን ልብ እያሸበረች ትሄዳለች። ሰታገባ ራሷ ላይ ሻሽ ጣል ማድረግ ትጀምራለች፡ ልጆች ወልዳ ዕድሜዋ ሲገፋ ደግሞ ጉፍታ የሚባል ታስራለች። ያገባች እና ያላገባች ሴት መለየት የሚቻለው ጸጉሯን በመሸፈኗ እና ባለመሸፈኗ ነው።

የተማሪዎቹን ቅሬታ እና ሂጃብ ማውለቅ የማይችሉበትን ሰበብ ከተረዳሁ በኋላ የትምህርት ቤቱ

የዲሲፕሊን ኃላፊ ጋር ሄጄ «ለምን አታስገቧቸውም? የሀይማኖት መብት ለምን ትጋፋላችሁን?› ስለው፡ «ከትምህርት ቢሮ የመጣ መመሪያ አንጂ የትምህርት ቤቱ ውሳኔ አይደለም» አለኝ። ወደ ዳይሬክተሩ ሰሄድም ተመሳሳይ መልስ አገኘሁ።

ወንድ እንደመሆኔ የሂጃብ ክልከላው በቀጥታ ባይጎዳኝም በሴት ተማሪዎች ላይ እየደረሰያለው ጫና በጣም አሳዘነኝ። መታገል አለብኝ ብዬ ወሰንኩ። ከግቢ ውጪ ወዳሉት ሴት ተማሪዎች ተመልሼ «ነገ ሌሎቹንም ጨምራችሁ ሁላችሁም ሻሽ አድርጋችሁ በተመሳሳይ ሰዓት ኑ» አልኳቸው። በዕረፍት ሰዓት ሻሽ የማይለብሱ ወይም አውልቀው የገቡ ሴቶችን ሰብሰቤ አወያየሁ። ክርስቲያን የሆኑትም ከሙስሊም አሀቶቻቸው ጋር ለመተባበር በማግሰቱ ሻሽ አሰረው መምጣት እንደሚችሉ ተወያይተው ወሰኑ። ወንድ ተማሪዎች በፊናችን ሴቶቹ እስከሚገቡ ድረሰ ውጪ ቆመን ባለመግባት ትብብር ለማሳየት ተስማማን።

በማግስቱ እንዳቀድነው ብዙ ሴት ተማሪዎች ጸጉራቸውን ተሸፋፍነው በመምጣት አውልቁ ሲባሉ አሻፈረኝ በማለታቸው መግባት ተከልክለው ውጪ ላይ ቆሙ። ወንዶቹም ከአነሱ ጀርባ ቆመን«አናንተ እለፉና ግቡ ስንባል ሴቶቹ ካልገቡ አንገባም አልን። ለተቃውሞው ተዘጋጅተው የመጡ ብቻ ሳይሆኑ በታው ላይ የሰሙ ተማሪዎችም መግባቱን ትተው ተቀለላቀሉን። እኛን ለማናደድ እና ሰሜት ውስጥ ለማስገባት በሚመስል መልኩ የግቢው ጥበቃ ባለፈው ከተማሪዎቹ የሰበሰበውን ሻሽ ማቃጠል ጀመረ። ተማሪዎቹ ሰሜት ውስጥ አንዳይገቡ አረጋግተን ዓላማውን አከሸፍነው።

በሩ ላይ ግርግር በዝቶ ፖሊሶች ተጠርተው ሲመጡ ሄጄ ያለውን ነገር አሰረዳኋቸው። ምንም ዓይነት ፀብ እንደማንፈልግና ያለንን ቅሬታ በሰላማዊ መንገድ ብቻ እንደምናቀርብ ቃል ገብቼ አሳመንኳቸው። አዚያ የነበረው ፖሊስ አዛዥ ረብሻ ፈጥራችሁ በሰው እና በንብረት ላይ ጉዳት አሰካላደረሳችሁ ድረስ አንነካችሁምን በማለት ፖሊሶች ከእኛ ራቅ ብለው መንገድ ተሻግረው አንዲቆሙ አዘዘ። ጥበቃው እንዲያባርሩን ሄዶ ቢነግራቸውም ፖሊሶቹ እሺ አላሉም።

የት/ቤቱ ዳይሬክተር መጥቶ ጥቂቶቻችንን ለብቻ አናገረን። «መመሪያው የመጣው ከላይ ነው፡ ምን ማድረግ አንችላለን?» ብሎ ተማጸነን። እኛም «ከላይም ይምጣ ከታች ትክክል ያልሆነ እና የተማሪውን መብት የሚጋፋ ነገር ሥራ ላይ መዋል የለበትም» ብለን ሞገትነው። ሊያሳምነን ሞክሮ ሲያቅተው ትቶን ሄደና ትንሽ ቆይቶ እንደተመለሰ «ይህን ጉዳይ ተረጋግተን በውይይት እናሰተካክላለን። ለአሁኑ ሁላችሁም ወደ ክፍል ግቡ፡ ሴቶቹም ሻሻቸውን ሳያወልቁ
ይግቡ» አለን። ሁሉም ተማሪዎች ገብተን መደበኛው ትምህርት ቀጠለ።

ዕረፍት ሰዓት ላይ የትምህርት ቤቱ የሥነ-ሥርዓት ኮሚቴ በጉዳዩ ላይ ለመወያየት በማግስቱ ቀጠሮ መያዙ ተነገረን። በታቀደው ውይይት ላይ ሂጃብ መከልከል እንደሌለበት ኮሚቴውን ማሳመን የምንችልበትን ነጥብ አዘጋጅተን እኔ አንዳቀርበው ተወሰነ። ሰብሰባው ላይ መምህራን፣የተማሪ ተወካዮች፣ ወላጆች እና የትምህርት ቢሮ ተወካዮች ተሳትፈዋል። ከሥነ-ሥርዓት ኮሚቴ ውስጥ አንድ መምህር ከትምህርት ቢሮ የመጣውን መመሪያ አነበበ። መመሪያው ሂጃብ የተከለከለበት ምክንያት የተማሪዎችን የጸጉር ንጽሕና ለማረጋገጥ፣ በሀይማኖት መካከል የሚፈጠር ልዩነት እና ግጭት ለማስቀረት አንዲሁም ጽንፈኝነት አንዳይሰፋፋ ለመከላከል እንደሆነ ይዘረዝራል።

ምላሽ ለመስጠት ዕድሉ ሲሰጠኝ ተነሳሁና «በሀገራችን ሕገ-መንግሥት እና ዓለም አቀፍ

ሕጎች መሠረት አንድ ድርጊት፣ ቃልና ምልክት ትምህርት ቤት ውስጥ መከልከል የሚችለው ሁለት ጉዳቶችን የሚያስከትል ከሆነ ነው'' አልኩ። እነሱም፣

1. የተማሪውን እና የአስተማሪውን መብት እና ደኅንነት አደጋ ላይ የሚጥል ከሆነ እና
2. የመማር ማስተማሩን ሂደት የሚያስተጓጉል ከሆነ።

የመጀመሪያውን ነጥብ ብዙ ማብራራት አላስፈለገኝም። «ጸጉር መሸፈን በትምህርት ቤት ውስጥ የደህንነት ችግር እንደማይፈጥር ግልጽ ነው። ሴቶች ሻሽ ሰላሰሩ የተፈጠረ የሀይማኖት ግጭት አላየንም አልሰማንም። ሻሽ ግጭት ፈጥሯል የሚል ሰው ካለ ይናገር» ብዬ አዳራሹ ውስጥ ስመለከት ሐሳብ የሚሰጥ ጠፋ።

ሁለተኛው ነጥብ ወሳኝ ስለሆነ እና መመሪያውን ለማክሸፍ ስለሚጠቅም ተዘጋጅቼበታለሁ። ከእኔ ጋር የሚማሩ ሁለት ሴት ተማሪዎችን አንዷ በሂጃብ አንድትሸፋፈን፡ ሌላኛዋ እንደ ከተማ ዱርዬ ከጉልበት በታች ተቆርጦ ያጠረ ዩኒፎርም አንድትለብስ አድርጌ ወደ አዳራሹ አስገባሁ።

ሁለቱን ልጃገረዶች ጎን ለጎን አሰቁሜ በጣቴ ሂጃብ ወደለበሰችው ልጅ እየጠቆምኩኝ ከተሳታፊዎች መሀል አንዱን ተማሪ «ይህቺ ልጅ ክፍል ውስጥ አጠገብሀ ከተቀመጠች ወይም ግቢ ውስጥ ፊት ለፊትሀ ከቆመች ትረብሽኻለችን» አልኩት። «ምኗን አይቼ ነው የምትረብሸኝ» ብሎ  እንደመቀለድ አለ። ቀጥሎ አጭር ልብስ የለበሰችዋን አሳይቼው «ይህቺ ልጅ ሂጃብ ከለበሰችው አጠገብ ክፍል ውስጥ ፊትለፊትሀ ብትቆም የትኛዋ ናት የበለጠ የምትረብሽሀ?›
ብዬ ሰጠይቀው ልጁ  እንደማፈር ብሎ አቀረቀረ፡ አዳራሹ ውስጥ የነበሩ ተሳታፊዎች ነገሩ ገብቷቸው ቤቱን በሳቅ አናጉት። ዕድሜው ለገፋ አንድ አስተማሪም ለተማሪው ያቀረብኩለትን ጥያቄ ደገምኩለት «ሂጃብ የለበሰች ልጅ ክፍል ውስጥ ማየትሀ የማስተማር ሥራህን ያውካል?›» ስለው «አሷን ካፈናት ነው አንጂ የሚረብሽ ነገር የለውም» አለ። አጭር ልብስ የለበሰችውን?? አሥነስቺ ሰጠይቀው ደግሞ «እኔ ሽማግሌ ነኝ አይረብሸኝምፉ። ለአንዳንተ ያለ ጎረምሳ ግን አደጋ ነው፡ ጭኗን አንጂ ሰሌዳ አታዩም› ብሎ ሰውን አሳቀው።

« እንደምታዩት ጸጉርን መሸፈን የመማር ማስተማሩን ሂደት እንደማያውክ ተማሪውም አስተማሪውም መስክሯል። መጀመሪያ ሕገ-መንግሥቱን ጠቅሼ  እንደተናገርኩት አንድ ድርጊትም ሆነ አለባበስ ሊታገድ የሚችለው የመማር ማሰተማሩን ሂደት ካወከ ስለሆነ ሂጃብ የሚከለከልበት ምክንያት የለም። ከትምህርት ቢሮ የመጣው መመሪያም ሰሕተት ነው» ብዬ ቁጭ አልኩ። በቀረቡት አስተያየቶች ላይ ውይይት ተደርጎ ሂጃብ አንዳይከለከል ስምምነት ላይ ተደርሶ ለትምህርት ቢሮ አንዲገለጽ ተወሰነ። የሚለበሰው ሂጃብ ግን በንጽሕና አንዲያዝና ተመሳሳይ (uniform) ሆኖ መልኩ ነጭ እንዲሆን ተብሉ ተለያየን።

ይህ የሂጃብ ውዝግብ በሀይማኖት መድሎ ቅሬታን የተረዳሁበት እና ለማስተካከልምየተሳተፍኩበት ነበር። ከዚያ በኋላ ሙስሊሙ ማኅበረሰብ ብቻ ሳይሆን የፕሮቴስታንት ተከታዮች (በጊዜው ጴንጤ ይባሉ ነበር) አድሎ እንደሚደርስባቸው መሰማት ጀመርኩ።

21 ሴት ተማሪዎች አጭር ቀሚስ መልበሳቸው ላይ ተቃውሞ አልነበረኝም። እንዲያውም እንደዚያ የሚለብሱ ሴቶችን ወንድ ተማሪዎች ሲለክፏቸው እቃወም ነበር። ባለአጭር ቀሚሷን ከባለ ሂጃቧ ጋር ጎን ለጎን ያቆምኩት ሂጃብ መልበሰን የመከልከል ውሳኔው ኢ-ፍትሃዊ እና መድሏዊ መሆኑን ለማሳመን ይረዳል ከሚል እሰቤ ነው።

አንድ እሑድ ከጓደኞቼ ጋር አዳማ ከተማ ውስጥ ስንሄድ የሆኑ መንገደኞችን የሰፈሩ ወጣቶች እየተከተሉ ሲሰድቧቸው እና ሲያሰፈራሯቸው አየን። መንገደኞቹ መልስ ከመስጠት ይልቅ ለማምለጥ በፍጥነት ይራመዳሉ። በአጠገባችን ሲያልፉ አፋን ኦሮሞ ሲያወሩ ስለሰማሁ የተሰደቡት በሚናገሩት ቋንቋ ምክንያት መስሎኝ ነበር። ካለፍኳቸው በኋላ ከጓደኞቼ ጋር ተመልሼ ለምን እንደሚሰደቡ ስጠይቃቸው በሀይማኖታቸው ምክንያት እንደሆነ ነገሩን። ምን ዓይነት ሀይማኖት እንደሆነ ስጠይቃቸው የፕሮቴስታንት አማኞች መሆናቸውንና ወደ ቸርች እየሄዱ እንደሆነ አስረዱን። ሁሌ ወደቸርች ሲሄዱ በዚህ መልኩ እንደሚሰደቡ እና ማስፈራሪያ እንደሚደርስባቸው ፤ አልፎ ተርፎም ቸርቻቸው ላይ ድንጋይ እንደሚወረወር ገለጹልን። በደሉ ፕሮቴስታንት ስለሆኑ ብቻ ሳይሆን ቸርቻቸው በአፋን ኦሮሞ ስለሚያገለገልም ጭምር እንደሆነ አክሉበት። እያወራን አብረናቸው ስንሄድ ከዚህ በፊት ቤተ-ክርስቲያን ወይም መስጂድ የሚሄድ ሰው ማስፈራሪያም ሆነ ስድብ ሲደርሰበት ስላላየሁ በጣም ገረመኝ።

በአደኩበት አካባቢ መስጂድ እና ቤተ-ክርስቲያን አካባቢ ጮክ ብሎ መናገር በራሱ እንደ ነውር ይቆጠራል። ወደ መስጂድ እና ቤተ-ክርስቲያን የሚሄዱ ሰዎችን የከተማ ዱርዬ እንኳን መንገድ ለቆ ያሳልፋል ፤ እናማ ያየሁት ግን አስገረመኝ። እኛ ስንቀላቀላቸው እየተከተሉ የሚሳደቡትም ቆሙ። ከዚያ ቀን በኋላ ለብዙ እሑዶች ጠዋት ጠዋት ከእነሱ ጋር እስከ ቸርች አብረናቸው እንሄዳለን። አልፍ አልፎ አንድንገባ ይጋብዙንና ከኋላ ሆነን እንመለከታለን። በአፋን ኦሮሞ ለመጀመሪያ ጊዜ የክርስቲያን መዝሙር ሲዘመር በመስማቴ ልቤን ደስ አለው። ያአጋጣሚ በሀይማኖት በኩል ያለውን ጫና እና በደል የበለጠ እንድረዳ ዓይኔን ገለጠልኝ።

ከሁሉም በላይ በሀይማኖት በኩል ያለውን ጫና ያየሁት ከሀገር ከወጣሁ በኋላ ነው። ወደ ሲንጋፖር በሄድኩበት ጊዜ አልቃይዳ በዩናይትድ እቴት ሰላይ ጥቃት ሰንዝሮ ለ«War on Terror» መነሻ ከሆነ ገና ሁለት ዓመት መሙለቱ ነበር። ዓለም አቀፉ የሽብር ጦርነት (Global war on terror) ተጋግሏል።

በሄድኩበት አካባቢ እንደ ኢንዶኔዥያ ባሉሀገራት ውስጥ የቱሪስት መስህብ በሆነችው ባሊ በተፈጸመ የሽብር ጥቃት በመቶዎች የሚቆጠሩ ሰዎች የተገደሉት በ2002 ነው። በዚህ የተነሳ የሙስሊም ስም ያለው ሰው፣ በተለይ ወጣት ወንድ ከሆነ ብዙ መንግሥታት በጥርጣሬ ዓይን ይመለከቱታል። ምንም እንኳን ጥርጣሬ እና ጫና የሚደርሰው በአየር ማረፊያ ፖሊሶች ቢሆንም፤ በሰፊው ሕዝብ ውስጥ ሳይቀር በመልክህ ወይም ስምህን ሲሰሙ መደንገጥ፣ መጀበር፣ መፍራት እና በጥላቻ ዓይን መመልከት በስፋት ይስተዋላል።

አንዴ ከሲንጋፖር ወደ ማሌዥያ በመኪና እየሄድኩ እያለ ድንበር ላይ ስንደርስ፣ ድንበር ጠባቂ ፖሊስ ፓስፖርቴን ተቀብሎኝ ኮምፒውተሩ ውስጥ ካስገባ በኋላ እንደመደንገጥ ብሎ አንዴ እኔን ሌላ ጊዜ ኮምፒውተሩን መመልከት ጀመረ። ድንገት ከየት መጡ ያላልኳቸው ኮማንዶ ፖሊሶች ከበው በጠረባ ጣሉኝ፤ በተዘረርኩበት እጄን የፊጥኝ አስረው መሬት ላይ እየጎተቱ የሆነ ቢሮ ወሰዱኝ። ቱታ የለበሱ ሰዎች መጥተው ልብሴን፣ ምራቄን እና የእጄን አሻራ ወስደው ሄዱ። ፖሊሶቹ ትንሽ ቆይተው ከተደፋሁበት ቀና አድርገው ወንበር ላይ ካስቀመጡኝ በኋላ የተለያዩ ጥያቄዎችን ይጠይቁኝ ገቡ። ከጥያቄዎቹ መሀል ሊገባኝ ያልቻለው «ፕላስቲክ ሰርጀሪ ያሰራኸው የት ነው? » የሚለው ነበር። ከዚያ ቀን በፊት ስለፕላስቲክ ሰርጀሪ (plastic surgery) ሰምቼ አላውቅም። ከሁለት ሰዓት ቆይታ በኋላ በስሕተት እንደያዙኝ ነገሩኝ።

ተመሳሳይ ስም ያለው ሰው በሽብርተኝነት ወንጀል ተሳትፎ እየተፈለገ እንደሆነና ኮምፒውተሩም በዚሁ ሰበብ እንደያዘኝ ነገሩኝ። ይቅርታ ጠይቀውና ከወንጀል ነጻ መሆኔን የሚያሳይ ወረቀት (Clearance) ሰጥተው ለቀቁኝ። ከዚያ በኋላ በተለያዩ የአውሮፕላን፣ የባቡር እና የአውቶቢስ ጣቢያዎች ሲያስቆሙኝ ያንን ወረቀት እያሳየሁ አልፍ ነበር።

ሌላ ጊዜ ደግሞ በአውሮፕላን ልጓዝ ኤርፖርት ስሄድ ለሦስተኛ ዙር ፍተሻ ወደ ዳር አስወጡኝ። በዚያ ዘመን የአውሮፕላን ተጓዦች አውሮፕላን ከመሳፈራቸው በፊት ጥብቅ ፍተሻ የሚደረግ ሲሆን፣ ፍተሻውም የተለያየ ደረጃ ነበረው። የመጀመሪያው ደረጃ ሁሉም ሰው ማሽን ውስጥ የሚያልፍበት ነው። ሁለተኛው ማሽኑ የሆነ ነገር ካሳየ ወይም እዚያ የሚቆመው ፖሊስ ሌላ ነገር ከጠረጠረ ወደ ዳር ወስዶ (ከተጓዦች ትንሽ ፈንጠር ብሎ) በእጅ የሚደረግ ብርበራ እና እጅን በመጥረግ የሚከናወን የኬሚካል ምርመራ ነው። ሦስተኛው እና ቀጣዩ እርምጃ ደግሞ የመጀመሪያዎቹ ሁለት ፍተሻዎች ተጓዡ ንጹሕ መሆኑን ካላረጋገጡ የኋላ ታሪኩን በደንብ ለማጥናት ወይም ለተጨማሪ ጠንካራ ፍተሻ ተጓዡን ወደ ቢሮ መውሰድ ነው። በወቅቱ አሸባሪዎች ቦምብ በተለያየ መልኩ በማሳለፍ አውሮፕላን ተሳፍረው አደጋ ያደርሳሉ ተብሎ ይፈራል። ለምሳሌ ሰውነታቸውን ቀደው ቦምብ ውስጡ በመቅበር መልሰው ሰፍተው አውሮፕላን ላይ ይወጣሉ ተብሎ ይጠረጠራል።

ለሦስተኛ ዙር ፍተሻ ከተለየሁ በኋላ አንዲት ሴት ፖሊስ የሆነ ባዶ ክፍል አስገንብታኝ በኃይለ ቃል «ልብስህን አውልቅ› ብላኝ ወጣች። እንደተባልኩት ልብሴን፣ ካልሲዬን እና ቡታንታ ሳይቀረኝ አወለኩና መለመላዬን ፊቴን ወደበሩ አዙሬ ጠበኳት። ፖሊሷ በሩን ከፍታ ስትገባ ራቁቴን ሆኜ ፊት ለፊት ሰንገጣጠም በድንጋጤ «Oh my God! What the hell? » ብላ ሮጣ ወጣች። ትንሽ ቆይቶ አንድ ወንድ ፖሊስ በሩን ከፍቶ ገብቶ በንዴት «ራቁትህን የምትቆመው ለምንድ ነው? » ሲለኝ «እሷናት አውልቅ ብላ አዛኝ የሄደችው ልብስህን አውልቅ አለች እንጂ ይሄን አውጣ ይሄን ተው ስላላለችኝ የታዘዝኩትን ነው ያደረኩት። እኔ ከመጣሁበት ሀገር የፖሊስን ትዕዛዝ አለመፈጸም ለጉዳት ይዳርጋል። እሷ በንዴት ስታዘኝ ፈርቼ ያወለኩት ለዚህነው› አልኩት። «እሺ አሁን ልብስን ልበስ› ብሎ ስለማንነቴ እና የጉዞዬን ዓላማ ብዙ ጥያቄዎችን ከጠየቀኝ በኋላ ወደምሳፈረው አውሮፕላን እየወሰደኝ «እሰቲ እውነት እንነጋገርና እንዳልከው ፖሊሷን ፈርተህ ነው? ወይስ ልታሸፍባት ፈልገህ ነው? » ሲለኝ ሁለታችንም ተያይተን ተሳሳቅን። «እኔ መጀመሪያም አውቄብሃለሁ፤ መልካም መንገድ ብሎ ሞልቶ ሲጠብቀኝ ወደነበረው አውሮፕላን አሳፍሮኝ ተመለሰ።

አሜሪካ ከሄድኩ በኋላ በሀይማኖት የሚመጣ ጥርጣሬ እና አድሎ እየተባባሰ መጣ። መጀመሪያ ላይ ለፍተሻ ሲነጥሉኝ እደነግጥ እና እናደድ ነበር። በቆይታ ተላመድኩትና በጥርጣሬ ከሚጠይቁኝ እና ከሚፈትሹን ፖሊሶች ጋር መቀላለድ ጀመርኩ።

አውሮፕላን ለመሳፈር ወደ አውሮፕላን ጣቢያ ሲኬድ ድንገተኛ ፍተሻ የሚባል ነገር አለ። እንደሚባለው ከሆነ ኮምፒውተሩ ከተሳፋሪዎች መካከል በዘፈቀደ (Random selection) ጥቂት ሰዎችን መርጦ ሁለተኛ ዙር ፍተሻ (secondary screening) እንዲካሄድባቸው ይልካል። እንደታዘብኩት ከሆነ ግን ተለይተው ከሚወጡት ውስጥ ሁሌም በስም እና በመልክ ሙስሊም የሚመስሉ ሰዎች ይገኙበታል።

ሙስሊሞች ላይ ብቻ ያላነጣጠረና ሙሉ በሙሉ የኮምፒውተሩ ውሳኔ እንዲመስል ሌሎች አምስት ሰዎችን በመጨመር በዘር፣ በሀይማኖት እና በዕድሜ ይቀላቅላሉ ፤ ወርቃማ ጸጉር ያላት ነጭ ሴት እና የደከመ ነጭ አዛውንት ይደባልቃሉ።

ታዲያ አንዴ ሰታንፍርድ ስማር በአንድ ሳምንት ውስጥ እራት አየር ማረፊያዎች ለተጨማሪ ፍተሻ ለይተው አስወጡኝ። በአምስተኛው ደፈር ብዬ «ከዚህ ሁሉ ሰው ለምን ልመረጥ ቻልኩ?» ስል ፖሊሱን ጠየኩት። «አይ አንተ ላይ ብቻ ያነጣጠረ ሳይሆን በአጋጣሚ ኮምፒውተሩ ነው የመረጠህ› አለኝ። መልሱን አስቀድሜ አያወኩ ነበር

የጠየኩት። «የእናንተ ኮምፒዩተር ይወደኛል መሰል በአንድ ሳምንት ውስጥ አምስት ጊዜ ዕጣ አወጣልኝ። በሌሎች ነገሮችም ፅድለኛ ሊያረገኝ ስለሚችል ይህን ኮምፒዩተር ብትሰጠኝ ምን ይመስልኸል› አልኩት። ፖሊሱ አፍረትበተሞላበትሳቅ። እኔም ያሉኝን ነው የነገርኩህ፣ አይዞህ ይህም ጊዜ ያልፋል» ብሎኝ ተለያየን።

ሙስሊም ሆኖ መንዝ ያመጣብኝ ሌላው አሥቂኝ ገጠመኝ እናቴ የሰጠችኝ ቀርጣሳ (ትብታብ) የፈጠረው ችግር ነበር። የአባቴ ጓደኛ የነበሩ ሼክ አብደላ ኡሰማን የተባሉ ዓሊም፣ ከክፉ ሁሉ አንዲከላከልልኝ ቀርጣሳ ሰርተው ለእናቴ ሰጥተዋት ነበርና በ200 ክረምት ላይ ኢትዮጵያ በመጣሁበት ወቅት እንዳስረው ተመጸነችኝ። በቀርጣሳው ከአደጋ የመከላከል ጉዳይ ባላምንበትም፣ እናቴን እና የአባቴን ጓደኛ ማስቀየም ስላልፈለኩኝ ተቀብዬ ክንዴ ላይ አስሬ ወደ አሜሪካ አቀናሁ። ከአውሮፕላን ወርጄ ፓስፖርቴን ሳይ እንደወትሮው ለተጨማሪ ፍተሻ እና ጥያቄ ከሌሎቹ ተጓዦች ተነጥቆ ተወሰድኩ። በፍተሻው ወቅት ክንዴ ላይ ያሰርኩት ነገር ተገኘ። ምን እንደሆነ ተጠይቄ ለማስረዳት ብሞክርም ማመን ስላልቻሉ እንድፈታው ታዘዝኩ። በቆዳ የተጠቀለለውን ትብታብ ሲፈቱት፣ በአረብኛ የተጻፈ ወረቀት ስለተገኘ ጥርጣሬያቸው በረታ። አንዲት የአረብኛ አስተርጓሚ ፈረንጅ መጥታ ብታነብም ይዘቱን መገንዘብ አልቻለችም። እንዲያውም ምሥጢራዊ መልዕክት የያዘ ኮድ ሊሆን እንደሚችል ጠቆመችና ጥርጣሬውን አጠበቀችብኝ። እናም በጊዜያዊነት አስረውን አረብኛ ቋንቋ እና አስልምናን በተሻለ የሚችል አረብ የዩኒቨርሲቲ ምሁር አምጥተው ሲያስነብቡ፣ ጽሑፉ ለመድኃኒትነት የሚውል የቁርኣን አያቶች (አንቀጾች) የያዘ እንደሆነ ስላስረዳ ልለቀቅ ቻልኩ።

# 6.4 ድምጻችን ይሰማ

በጉዞ ላይ ከነበረኝ ልምድ፣ ያኔ ስለእስልምና እና ሙስሊሞች በሚዲያ ይቀርብ ከነበረ ክርክር፣ እንዲሁም ከምዕራቡ ዓለም ጋር ካለው ፍጥጫ በመነሳት ጉዳዩን ለመረዳት ከፍተኛ ፍላጎት አደረብኝ። በሙስሊም ሕዝብ እና በምዕራቡ ዓለም መካከል ስላለው ግንኙነት የሚሰጡ የታሪክ ኮርሶችን መውሰድ ጀመርኩ። በተጨማሪም በሀይማኖት እና በፖለቲካ መካከል ስላለው መስተጋብር የሚሰጡትን አስከተልኩ። በዚህ ዘርፍ ላይ ሰፊ ጥናት ያደረጉ እና ልምድ ያላቸውን ፕሮፌሰሮች ከክፍል ውጪ ፈልጌ በመቅረብ ግንዛቤይን ለማሳደግ ሞክርኩ። እንዲሁም በዩኒቨርሲቲው ውስጥ የሚካሄዱ የተለያዩ ሰብሰባዎችን እና ትምህርታዊ ኮንፈረንሶችን ተከታትዬ ተሳተፍኩ። አስተማሪዎቼም ፍላጎቴን ስለሚያውቁ በጉዳዩ ላይ ኮንፈረንሶች ሲዘጋጁ ይጋብዙኛል።

አ.አ.አ. በ2006 "Islamic Courts Union" የተባለ ኃይል ሱማሊያን ሲቆጣጠር፤ በኋላም የኢትዮጵያ ጦር ሱማሊያን ሲወር በጉቶዩ ላይ በዩኒቨርሲቲያችን ስብሰባ ተዘጋጅቶ ተሳተፍኩ። የነበረው ክርክር "ኢትዮጵያ ጦሯን ወደ ሱማሊያ ማሰገባቷ ይጠቅማል ወይስ ይጎዳል?" የሚልነው። አንዳንድ ሰዎች ኢትዮጵያ ጠንካራ ጦር ሰላላት ጽንፈኛ ኃይሎችን ለመምታት ተመራጭናት ያሉ ሲሆን፣ በሌላ በኩል ግን ኢትዮጵያ እና ሱማሊያ የጠላትነት ታሪክ ስላለቸው የኢትዮጵያ ጦር መሰማራት የሱማሊያን ብሔርተኝነት በመቀሰቀስ፤ ጽንፈኞች ሕዝባዊ ቅቡልነት እንዲያገኙ ስለሚያደርግ ከጥቅሙ ጉዳቱ ይበልጣል የሚል ነው።

ይህን ክርክር አስቀድሜ ስሰማ እና ሳነብ ስለነበረ ለእኔ አዲስ አልነበረም። አዲስ የሆነው ነገር «ጽንፈኛ የሀይማኖት አማጺያን ኢትዮጵያ ውስጥም እያቆጠቆጡ ነው› የሚለው ነበር። አንድ የውጭ ምሁር እና የኢትዮጵያ መንግሥት ተወካይ «እስላማዊ ጽንፈኝነት ኢትዮጵያ ላይ የደቀነው አደጋ» የሚል ጽሑፍ አቀረቡ። ዕንሰ-ሐሳቡ እስላማዊ ጽንፈኝነት ኢትዮጵያ ውስጥ እየተስፋፋ ስለሆነ መንግሥት ከፍተኛ የሽብርተኝነት ሥጋት ውስጥ ገብቷል የሚል ነው። የአሸባሪ ኃይሎች ሱማሊያ ብቻ ሳይሆን ኢትዮጵያም እየመጡ ነው በማለት ተናገሩ።

እንደመፍትሔም ኢትዮጵያ ሱማሊያ ያሉ ጽንፈኞኛችን መዋጋት ብቻ ሳይሆን በሀገሯም ውስጥ ለዘብተኛ የሙስሊም ቡድኖችን (Moderate Islamic Groups) ማበረታታት አለባት የሚልነው። በጥያቄ እና መልስ ጊዜ ጽንፈኝነት ኢትዮጵያ ውስጥ ስለመኖሩ ምን ማስረጃ እንዳላቸው ሲጠየቁ ግን አጥጋቢ ምላሽ አልነበራቸውም። የጽሑፉ ዓላማ የገባኝ ውሎ አድሮ መንግሥት ከሙስሊም ሕዝብ ጋር ግጭት ውስጥ በገባበት ወቅት ነው።

የኢትዮጵያ ጦር ሶማሊያ መግባቱ የሀገሪቱን የጸጥታ ችግር ይበልጥ አባብሶ፤ ከዓለም አቀፍ አሸባሪዎች ጋር ትብብር እንዳለው በግልጽ ያወጀውን የአልሸባብ አንጃ ወለደ። የኢትዮጵያ ጦር መግባቱ በሁለቱ ሀገራት መካከል የነበረውን የታሪክ ቁርሾ ቆሰቁሶ የሶማሌን ብሔርተኝነች በማጠናከር ለአልሻባብ ድጋፍ አስገኘለት። ጆርጅ ቡሽ ከአሜሪካ ፕሬዝደንትነት ወርዶ ባራክ

ኦባማ ከተመረጠ በኋላ አሜሪካ ሶማሊያ ላይ ያላት ፖሊሲ መቀየር ጀመረ። የኢትዮጵያ ጦር መግባት አሸባሪውን ከማጥፋት ይልቅ የባሰ እንዳጠናከረው ለእነ ኦባማ ግልጽ ነበር። በተጨማሪም መለስ ዜናዊ ከቻይና ጋር ያዳበረው ግንኙነት አሜሪካኖቹን ሳያሰስባቸው አልቀረም። አሜሪካ በሶማሊያ ያሉ አሸባሪዎችን ለመቆጣጠር ለረጅም ጊዜ ኢትዮጵያ ላይጥገኛ ሆና የቆየች ሲሆን፣ ኦባማ የኢትዮጵያን ሚና በመቀነስ እንደ ኬንያ እና ኡጋንዳ ያሉ ሀገራትን ማሳተፍ ጀመረ።ይህ ደግሞ የመለስ መንግሥት ከምዕራቡ ዓለም ሲያገኝ የነበረውን የፖለቲካእናየገንዘብአርዳታአሳሳው።መለስ የአሜሪካን የፖሊሲ ለውጥ ቶሎ ስለተንነዘበ ምዕራባውያኑ ከእሱ መንግሥት ጋር ያላቸውን ወዳጅነት እና ቁርኝት ማስቀጠል የሚችለበትን ስለት ይዞ ከተፍ አለ።

ከላይ እንደተጠቀሰው የመለስ መንግሥት ለረጅም ጊዜ "የሀይማኖት ጽንፈኝነት ኢትዮጵያ ውስጥ እየተባባሰ ነው ፤ የሚለውን ሐሳብ በምዕራባውያኑ አእምሮ ውስጥ ሲያሠርጽ ከቆየ በኋላ በ2020 አሕባሽ የተባለውን አንጃ ከሊባኖስ ጋበዘ። ሐሳቡ የሀገር ውስጡ እስልምና በጽንፈኝነት ስለተወሰደ ከውጪ በሚመጣ አስተምህሮ ማለዘብ ያስፈልጋል የሚል ነው።

ድብቅ ዓላማው ግን ለሀገሪቷ ሙስሊም ማኅበረሰብ ባዕድ የሆነ ሀይማኖታዊ አንጃ ሕዝቡ ላይ በኃይል ለመጫን በመሞከር ሙስሊሙን ማኅበረሰብ በተለይ ወጣቱን አስቆጥቶ ወደ አመጽ እንዲያመራ ማድረግ ነበር።

ይህ ቁጣ ሙስሊም ወጣቶችን ወደ ትጥቅ ትግል የሚመራ ከሆነ በኢትዮጵያ ውስጥ "ጽንፈኛ የእስልምና አማጺያን (Militant Islamic groups) ተፈጠሩ' በማለት ምዕራባውያኑ ለመለስ መንግሥት የሚያደርጉትን የገንዘብ እርዳታ አጠናክረው እንዲቀጥሉ ያስችላል ተብሎ የወጣ ስልት ነው። እንደተጠበቀው የመለስ መንግሥት የአሕባሽን አንጃ አምጥቶ የሀገሪቱን መጅሊስ በኃይል አንዲቆጣጠሩ ማድረጉ ተቃውሞ አሥነሳ።

ያንን ተቃውሞ እንድደግፍ ያደረገኝ መብቱ ከተገፋው የሙስሊም ሕዝብ ጋር በአጋርነት ለመተባበር ብቻ አልነበረም። መንግሥት ሕዝቡን በማስቆጣት እየሄደበት ያለው ሀይማኖትን ወደ ፖለቲካ የማምጣት (politicization of religion) እቅድ እና እርምጃ፣ በሀገሪቷ ፖለቲካ በተለይም በኦሮሞ ላይ የሚያስከትለው አደጋ ስላሳሰበኝ ነው። ፍርሀቴ የሚከተሉትን ነጥቦች ላይ የተመሠረተ ነበር፡-

1. የመለስ አቅድ የሙስሊም ወጣቶችን አስቆጥቶ ወደ ትጥቅ ትግል ሊያስገባ ይችላል። ይህ ደግሞ ሥርዓቱ በአምባገነንነት ሕዝባችን ላይ እያደረሰ ያለውን ጉዳት ዓለም ትኩረት እንዲነፍገው ሊያደርግ ይችላል።

2. ሀይማኖች ፖለቲካን ከቀላቀለ፣ በሕዝቦች መካከል ያለውን ግንኙነት ከማባባስ አልፎ ወደ ማኅበረሰባዊ ግጭት (22ወመሬአ33 ሃፈ6156ሪ5) ሊያደርስ ይችላል። ይህም ብዙ ሀይማኖቶች ላሉበት ሀገር ትልቅ አደጋ ነው። በተጨማሪም በኦሮሞ የትግል ጎራ ውስጥ ክፍፍል እና ግራ መጋባት ሊፈጥር ይችላል።

3. ሙስሊም ወጣቶች በንዴት ተነሳስተው የትጥቅ ትግል ከጀመሩ ፤ በዓለም አቀፍ ደረጃ የሚንቀሳቀሱ ሽብርተኛ ቡድኖችን በመሳብ ሀገራችንን የዓለም አቀፉ ሽኩቻ አካል በማድረግ ከባድ የብጥብጥ አውድማ ልትሆን ትችላለች።

4. የህዝበ ሙስሊሙ ተቃውሞ የሀገራችንን እና የዓለምን ፖለቲካ በተረዱ ሰዎች ካልተመራ እና በቁጣ ስሜት እንዲመራ ከተተው፤ በተለያዩ ኃይሎች ተጠልፎ ሙስሊሙን ማኅበረሰብ እና መላውን ሀገር ወደ ሚጎዳ አቅጣጫ ሊሸጋገር ይችላል።

እነዚህን ሥጋቶች ከምሁራን ጋር ተወያይቼ ሐሳቡን ካብላለሁት በኋላ ሕዝበ ሙስሊሙ የጀመረው ትግል ውስጥ እንደ ደጋፊ ለመሳተፍ ወሰንኩ። ይህንንም በሦስት መንገድ ለማድረግ መረጥኩ። አንደኛ፤ ትግሉን ለሚመሩት እና ለሚሳተፉት በሰላማዊ የትግል ስልት እና ፖለቲካዊ ሁኔታ ላይ ምክር እና ሥልጠና መስጠት። ሁለተኛ፣ የውጭ መንግሥታት እና ተቋማት እየተፈጠረ ስላለው ሁኔታ ትክክለኛ ግንዛቤ እንዲኖራቸው ጥረት ማድረግ። ሦስተኛ፣ መንግሥት የሚያደርገውን የሐሰት ፕሮፓጋንዳ በማኅበራዊ ሚድያ እና በተለያዩ ሚዲያዎች ማክሸፍ ናቸው። በተለይ የመንግሥት ፕሮፓጋንዳ የሙብት እንቅስቃሴውን እንደ ጽንፈኝነት እና ሽብርተኝነት ያቀርብ ስለነበር ፤ በተለያዩ የሀይማኖት ማኅበረሰቦች መካከል የአግድም ግጭት (Horizontal conflict) እንዳይፈጠር የተቀናጀ የሚዲያ ዘመቻ በማድረግ ለመርዳት ፈለኩኝ።

ከላይ በተገለጸው መልኩ መጫወት ያለብኝን ሚና ከወሰንኩ በኃላ ሀገር ውስጥ እና ውጪ ላሉ ሰዎች በሰላማዊ ትግል ስልቶች ላይ ሥልጠና መስጠት ጀመርኩ። ውጪ ካለ የምሁራን ቡድን ጋር በተደረገ ምክክር ትግሉ ሊከተለው የሚገባው ትርክት ላይ ያሉንን አስተያየቶች በማስማማት ሀገር ውስጥ ለሚታገሉት እንዲላክ ተደረገ።

ከእነዚህ ነጥቦች መካከል፤

1. ትግሉ ሙሉ በሙሉ ሰላማዊ እንዲሆን፣ አመራሩም ይህንን በግልጽ ለሕዝቡ እና ለሁሉም አካላት አንዲያስረዳ። ወጣቶች በስሜት ተነሳስተው ወደ ብጥብጥ እንዳይገቡ ማረጋጋት እንደሚያስፈለግ፣ ሕዝባዊ ተቃውሞውን ወደ ብጥብጥ እና የኃይል እርምጃ ለመጎተት የሚሞክሩ አካላትን መቆጣጠር እንደሚገባ።

2. የሙስሊሙ ማኅበረሰብ ተቃውሞ በኢትዮጵያ የተወሰነ የሰብዓዊ መብት እና የዴሞክራሲ ትግል እንጂ፣ የዓለም አቀፍ ሽኩቻ አካል አለመሆኑን ለኢትዮጵያ ሕዝብ እና ዲፕሎማቶች በደንብ ማስረዳት። የሕዝባዊ ተቃውሞው ዓላማ በሕገ-መንግሥቱ የተደነገገውን የመንግሥት እና የሀይማኖት መለያየት ለማስከበር መሆኑን በቃልም በተግባርም ማሳየት ያስፈልጋል። ይህንን ለማጠናከር መፈክሮችም ሆኑ የሚተላለፉ መልዕክቶች በሀገር ውስጥ ቋንቋዎች እንጂ በውጪ ቋንቋዎች እንዳይሆን መደረግ አለበት።

ነጥቦቹ መተግበር ከጀመሩ በኋላ እኛም የሥራ ድርሻ ተከፋፍለን መሳተፍ ጀመርን። "ድምጻችን ይሰማ በሚል በጁምዓ ሶላት ላይ ሲሰማ የነበረው መፈክር የንቅናቄው መጠሪያ ሆኖ እንዲለመድና እኛም ይህንኑ እንድንጠቀም ተስማማን። በየሳምንቱ ዓርብ የሚደረገውን ተቃውሞ እንዲሁም በመንግሥት የሚወሰዱ እርምጃዎችን ትንታኔ ጨምራበት በፌስቡክ አጋራለሁ። ለሚዲያዎችም አስፈላጊውን ማብራሪያ እሰጣለሁ፣ በማይመቸኝ ቀን ለሎች ሰዎችን በመመደብ ትኩረት የሚሹ ነጥቦችን አስይዛለሁ። ከሚዲያው ዘመቻ በተጨማሪ የዲያስፖራውን ማኅበረሰብ በማስተባበር ለታሰሩ የትግሉ መሪዎች ቤተሰቦች የገንዘብ ድጋፍ እናደርጋለን።

በውጪም ሆነ በሀገር ውስጥ ሙስሊሙን በማንቃት፣ በማደራጀት እና በማስተማር ውስጥ አንድ እንቅፋት ነበር። እሱም ለብሔር ትግል ለረጅም ጊዜ ከተጋለጡት የኦሮሞ እና የሶማሌ ማኅበረሰብ በስተቀር ሌሎች ሙስሊሞች፣ በተለይም በከተማ ያሉት ፖለቲካዊ ንቃታቸው እና ተሳትፏቸውም እምብዛም ነው። እንዲያውም ብዙዎቹ ፖለቲካን ይጠየፋሉ፣ አንዳንዶቹ መንግሥትን ይደግፋሉ። ስለዚህ የምናቀርባቸው ሥልጠናዎች፣ ንግግሮች እና ጽሑፎች ይህንን የግንዛቤ እና የተሳትፎ ደረጃ መበላለጥ ባማከለ መልኩ መሆን ነበረበት።

ከሥራዎቹ አንዱ የክርስቲያኑ ማኅበረሰብ ግንዛቤ እና ትብብር እንደሚያስፈልግ ለትግሉ አስተባባሪዎች እና ሼኾች ማስረዳት ነበር። የመንግሥትን ሴራ እና ፕሮፓጋንዳ ለማሸነፍ የክርስቲያኑን ማህበረሰብ ከሙስሊሙ ጎን ማሰለፍ ወሳኝ መሆኑን ተናገርኩ። ስለሆነም ውጪ ያሉ ሼኮች እና የሙስሊም ምሁራን የክርስቲያኑን ማኅበረሰብ መሪዎች በማነጋገር እየተካሄደ ሰላለው ነገር በማስገንዘብ ያላቸውን ጥያቄ በመመለስ እና ምናልባትም ጥርጣሬ ካላቸው በማስተካከል ላይ እንዲሰማሩ ተደረገ። ሰልፍ እና ሰብሰባ ባለጊዜ ክርስቲያን የሆኑ አንቂዎች እና ምሁራንን መጋበዝ ተጀመረ።

አንዴ ከአሜሪካ መንግሥት ባለሥልጣናት ጋር ለመነጋገር ቀጠሮ ተይዞ የሙስሊም ሼኾች እና ሽማግሌዎች እንደሚሄዱ ጠብቀው ነበር። እኛ ግን መስቀል የያዙ እና ጥቁር የለበሱ ቄሶች እና ፓስተሮችን ከቄሶቹ ጋር ቀላቅለን ወሰድናቸው።

እኛን ለማናገር የሚጠብቀው ሰው ቄሶች እና ፓስተሮች በጥቁር ልብስ ላይ መስቀል አንጠልጥለው፣ ሼኾቹ ሙደወር ለብሰው እና ኢማማ ራሳቸው ላይ ጣል አድርገው ሲመለከት ተገረመ። ወደ ጆሮዩ ጠጋ ብሎ ይሄንን ቀጠሮ ያሰያዝከው ሙስሊሞችን እንድናናግር አልነበረም እንዴ? » አለኝ። እኔም «አንተ እንዳልከው የመጣንበት ጉዳይ የኢትዮጵያ ሙስሊሞችን የመብት ጭቆና ለመናገር ነው። ነገር ግን ይህ የሙስሊሙ ጭቆና ክርስቲያኖቹንም ስለሚመለከት በጋራ ያለባቸውን ችግር ለመናገር ነው የመጡት› አልኩት። በውይይቱ ጊዜም ቄሶቹ እና ፓስተሮቹ የኢትያጵያ መንግሥት እያደረሰ ያለውን ጉዳት ዘርዝረው ተናገሩ። ቄሶቹ እና ፓስተሮቹ ሲናገሩ የሌላን ወገን ችግር እንደሚናገር ሰው ሳይሆን የራሱን ሕመም እንደሚናገር ሰው ነበር።

የሙስሊሙ ተጋድሎ በዚሁ መልኩ ከውጪም ከውስጥም እየተቀጣጠለ ሲሄድ መንግሥት የተለያየ ቦታ ሰዎችን መግደል፣ የንትናቄውን አስተባባሪዎች ማሰር እና ማስፈራራት ተጀመረ። አንድ ቀን በዚህ ጉዳይ ላይ ከተወሰኑ መሪዎች ጋር ስንወያይ ዛቻ እና አስራ ሁለት ዓላማ አንዳለው ነገርኳቸው። አንደኛው የተወሰኑ መሪዎችን አሸማቅቆ ከትግሉ ለማስወጣት ሲሆን ፤ ሁለተኛው ደግሞ ከሀገር እንዲሰደዱ በማድረግ ተቃውሞውን መሪ ማሳጣት እንደሆነ አብራራሁ። ከትግሉ ያላፈገፈጉትን ወይም ከሀገር ለመሸሽ ፈቃደኛ ያልሆኑትን እንደሚያስሩ ጨምሬ አስረዳሁ።

ያላቸው አማራጭ ሦስት መሆኑን አከልኩበት። ከትግል መራቅ ከሀገር መሰደድ ወይም ለእስር ራስን ማዘጋጀት። «ለራሴ ውጪ ተቀምጬ ራሳችሁን ለአደጋ አጋለጡ ማለት ቢከብደኝም፣ ከሦስቱ አማራጮች ለትግሉ የሚጠቅመው መታሰር ሲሆን፣ ትግሉን የሚጎናው ደግሞ ከሀገር መሰደድ ነው። ከሀገር ከመውጣት ትግሉን መተው ይሻላል› አልኳቸው። ከሀገር መሸሽ ከሁሉም በላይ ጎጂነው ያልኩበት ምክንያት ነበረኝ። የአመራሩ ከሀገር መሰደድ የሕዝቡን ሞራል በጣም ያዳክማል። መንግሥትም የተቃውሞ መሪዎች ከሀገር እንዲወጡ የሚፈልገው

የሕዝቡን ሞራል በመስበር ትግሉን ለማዳከም ስለሚረዳው ነው። በሌላ በኩል ንቅናቄውን በኃላፊነት እና በስትራቴጂ የሚመራ አመራር መሰደዱ፤ የሕዝቡን ቁጣ መንገድ በማሳት ለተለያዩ እኩይ ተግባራት ለሚያውሉ ኃይሎች ዕድል ሊፈጥር ይችላል።

አመራሩ በራሱ ላይ ወስኖ መታሰሩ የሕዝቡ ስሜት ተሟሙቆ እንዲቀጥል እና ትግሉ በሌሎች ኃይሎች እንዳይጠለፍ ወሳኝ መሆኑን አበክሬ ነገርኳቸው። መንግሥት የሚቃወሙትን መሪዎች አሸማቆ እና አሰቃይቶ ከሀገር ማባረር ከዚህ በፊት ተጠቅሞ የተሳካለት ስልት እንደሆነ ኦነግ እና ቅንጅትን በመሳሰሉ የፖለቲካ ድርጅቶች ላይ የተፈጸመውን ዋቢ አድርጌ ዘረዘርኩ። ሳውያያቸው የነበሩ የሙስሊም መሪዎች በሀገር ውስጥ ቆይተው አስፈላጊውን መሥዋዕትነት ለመክፈል ቀድሞውኑ እንደተዘጋጁ ነገሩኝ። በቀጣዮቹ ቀናት የስልክ እና የአካል ማስፈራሪያው መባባስ ብቻ ሳይሆን የተለያዩ ሀገራት ቪዛ እንደሚመታላቸው ቃል በመግባት ከሀገር እንዲወጡ በቅርብ ሰዎች ለማሳመን ተሞከረ። የንቅናቄው መሪዎች ግን በጽናት መታገል ቀጠሉ። እንደማይሸሹ ሲያውቁ የመፍትሔ አፈላላጊ ኮሚቴ መሪዎችን እና ታላላቅ ዓሊሞችን (ሊቃውንትን) ሰብስበው አሰሩ። ሕዝባዊ ተቃውሞው ግን አልቆመም።

ከሀገር ውጪ ያለነው በምንችለው ሁሉ ትብብራችንን አጠናክረን ቀጠልን። በሚዲያ ከሚደረግ ዘመቻ በተጨማሪ የእስረኛ ቤተሰቦችን ለመርዳት በውጭ ሀገር ከሚገኘው ሕዝብ እርዳታ አሰባሰብን። በተለያዩ የሰሜን አሜሪካ ከተሞች ማኅበረሰቡ ሰብሰባዎችን በማዘጋጀት ይጋብዙኛል። በእነዚህ መድረኮች ባደረኳቸው ንግግሮች የሙስሊሞች ትግል የሰብዓዊ መብት እና የዴሞክራሲ ትግል አካል መሆኑን እናገር ነበር። በተለይ ለሀይማኖት እና ለብሔር መብት የሚደረግ ትግል የሚደጋገፍ እንጂ የሚቃረን መሆን እንደሌለበት አጽንኦት ሰጥቼ እመክር ነበር።

የድምጻችን ይሰማ ንቅናቄ በኢትዮጵያ ውስጥ የሰላማዊ ትግል መርሆችና ስልቶችን በሚገባ የተጠቀመ የመጀመሪያው የመብት ትግል ነው ቢባል ማጋነን አይሆንም። ከዚያ በፊት የነበሩ ህዝባዊ ንቅናቄዎች የሰላማዊ ትግል ስልቶችን የተጠቀሙ ቢሆንም፣ ጊዜ ሲራዘም ወይም የመንግስት የአፈና እርምጃ ሲጠናከር፣ ወደ ትጥቅ ትግል የመቀየር ወይም የመክሰም ታሪክ አላቸው። የድምጻችን ይሰማ ንቅናቄ ግን ፈተናዎችን በመቋቋምከሰላማዊ ትግል ፈር ሳይለቅ የመንግስት አላማ የነበሩት የአልሀባሽን አስተምሮ መጫንም ሆነ ወጣቱን ወደ ትጥቅ ትግል ማስገባትን ማክሸፍ ቻለ።

በቀጣይ የፈነዳው የቄሮ ትግልም ከድምጻችን ይሰማ ንትናቄ ብዙ ተሞክሮዎችን አግኝቷል። የድምጻችን ይሰማ ስኬት "ሰላማዊ ትግል በኢትዮጵያ ውስጥ ውጤታማ አይሆንም" የሚለው አስተሳሰብም የተሳሳተ መሆኑን በተጨባጭ ስላሳየ፣ ለቄሮ ሞራል ሰጠ። ብዙ የቄሮ አስተባባሪዎች በድምጻችን ይሰማ ንቅናቄም ተሳታፊ ስለነበሩ ያካበቱትን ልምድ ወደዚህ አሸጋገሩ። የወረሳቸው ዝርዝር ስልቶች ብዙ ሲሆኑ፣ የቄሮ ትግል ምልክት የሆነው እጅን ማጣመር እራሱ የተወረሰው ከድምጻችን ይሰማ የተቃውሞ ሰልፎች ነው።

## 6.5. የሀይማኖት እና የብሔር መብት ትግል፡ ተመጋጋቢ ወይስ ተገዳዳሪ?

የሀይማኖት እና የብሔር ትግል ተደጋጋፊነት ላይ አተኩሬ ማውራት የጀመርኩበት ምክንያት ነበረኝ። ይህም በሁለቱም ወገን ያሉ ታጋዮች ማለትም ሀይማኖት እና ብሔር አንዱ አንዱን ሊውጠው ወይም ሊያደበዝዘው ይችላል የሚል ጥርጣሬ ውስጥ ስለነበሩ ነው። የሀይማኖት መብት ታጋዮች የብሔር ትግል የሀይማኖትን ጎራ ይከፋፍላል ብለው ይፈራሉ፤ የብሔርም እንዲሁ የሀይማኖት ልዩነት ከፋፍሎ ያዳክመናል በማለት ይጠራጠራሉ። በተለይ በኦሮሞ ትግል ውስጥ ይህ ጥርጣሬ ከድሮም ጀምሮ የነበረ ሲሆን፣ በሕዝበ ሙስሊሙ ትግል ወቅት በአዲስ መልክ ብቅ ማለት ጀምሯል። በብሔር ትግል ተሳትፎዬ እታወቅ ስለነበር፣ በሀይማኖት ትግል ላይም መሳተፍ መጀመሬ ለእነዚህ ጥያቄዎች እና ጥርጣሬዎች ምክንያት መሆኑን ተንነዘብኩ።

በዚህ ጉዳይ ላይ ዝርዝር መግለጫ ለመስጠት ዕድሉን አግኝቼ እ.አ.አ. በ2012 ወደ ሚኒሶታ ሄድኩ። የሚኒሶታ ሙስሊም ማኅበረሰብ ባዘጋጀው ስብሰባ ላይ ከተለያየ ብሔር የተውጣጡ ሙስሊሞች ተሳትፈዋል። በንግግሬም የኦሮሞ ትግል በኢትዮጵያ ውስጥ ያለውን ዘርፈ ብዙ ጭቆና በመቀነሱ ረገድ ትልቅ ሚና እንዳለው ገለጽኩ። ለዚህ ምክንያቱ፣ ‹ አንደኛ፣ የኦሮሞ ጥያቄ የእኩልነት እና የዴሞክራሲ ስለሆነ የኦሮሞ ጥያቄ ሲመለስ ሌሎች ጭቁን ሕዝቦችም ተጠቃሚ ይሆናሉ። በሁለተኛ ደረጃ፣ ኦሮሞ በቁጥር ግዙፍ ሕዝብ በመሆኑ፣ እንዲሁም የፖለቲካ መቀመጫ የሆነችውን ከተማ ከብቦ የሚገኝ ሰፊ መልከአ-ምድር ስላለው የፖለቲካ እንቅስቃሴው እና ተቃውሞው አገዛዙን የመናጥ እና የፖሊሲ ለውጥ የማምጣት ኃይል አለው። የኢትዮጵያ ሕዝቦች ባለፉት ሃምሳ ዓመታት በሂደት ለተጎናጸፏቸው መብቶች የኦሮሞ ትግል ድርሻ ቀላል አይደለም። በ1966ቱ አብዮት የተገኘው የመሬት ባለቤትነት መብት ፣ በፌደራላዊ ሥርዓት መዘርጋት የተቀዳጁት የማንነት እና ራስን በራስ የማሥተዳደር መብት ሊጠቀስ ይችላል። ተከታታይ መንግሥታት የኦሮሞን ሕዝብ ሰፋት እና መልክዓ ምድራዊ አቀማመጥ ስለሚፈሩ፣ ሕዝቡ ሲያምጽ ጥያቄዎቹን እየሸራረፉ በመመለስ አባብለው ሊያረጋጉት ይሞክራሉ። ለኦሮሞ አንድ ጥያቄ ሲመለስ፣ ኦሮሞ ብቻ ሳይሆን ሁሉም የተጨቆኑ ብሔሮች ይጠቀማሉ።

«የኦሮሞ ሕዝብ የተለያዩ ሀይማኖቶች የሚከተል ስለሆነ፣ ይህን ሕዝብ በአንድነት አስተባብሮ ለማታገል የኦሮሞ መሪዎች እና ድርጅቶች የሀይማኖት እኩልነት እንዲሁም የሀይማኖት እና የመንግሥትን መለያየት (secularism) ለመደገፍ ይገደዳሉ። በተጨማሪም ከኢትዮጵያ ሙስሊሞች ውስጥ አብዛኛው ኦሮሞ በመሆኑ፣ ኦሮሞ እንድ መብት ሲጎናጸፍ ሙስሊሙም ይጠቀማል። ወደፊትም ቢሆን የኦሮሞ ትግል በሚያገኘው ድል ሙስሊሙም ሆነ ሌላው ጭቁን ሕዝብ መብቱ ይበልጥ እንዲከበር መንገድ ይከፍታል። ሙስሊም ኦሮሞዎች ሀይማኖትን

ጨምሮ ሌሎች መብቶችን ለማስከበር የሚታገሉት በብሔር ድርድቶች ማዕቀፍ ውስጥ ነው። የብሔር መብት ሰንጎናጸፍ፣ የሀይማኖት መብትም እናገኛለን ብለው ያምናሉ።

«ሙስሊም ኦሮሞዎች ከሀይማኖቱ የበለጠ የሚሰማቸው የብሔር ጭቆና ነው። ምክንያቱም ኦሮሚያ ውስጥ ሙስሊሞች በቁጥር ትንሽ ሰላልሆኑ መንግሥት በቀላሉ የሀይማኖት መብቶችን ለመደፍጠጥ አይቻለውም። ሕዝቡም ከብዛት በሚመጣ ድፍረት (safety in numbers) የተነሳ በመተጋገዝ በደልን ይመክታል። በተጻራሪው በሰሜን አካባቢ ያሉ ሙስሊሞች ህዳጣን (minority ስለሆኑ በቀላሉ ለጭቆና ይጋለጣሉ። መንግሥት እንደፈለገ መብታቸውን ለመጣስ ይቀለዋል። በአንዳንድ የሰሜን ኢትዮጵያ አካባቢዎች እንደሚስተዋለው መስጂድ መሥሪያ እና የቀብር ቦታ ላይ የሚደረግ ክልክላ ኦሮሚያ ውስጥ ታስቦም አያውቅም። ለምሳሌ እኔ በተወለድኩበት አካባቢ ሙስሊሙ ብዙሃን ስለሆነ ሀይማኖቱ ሲነካ ማንም ዝም አይልም፤ ማንም ሰው ሀይማኖቱን ቢነካ በሜንጫ አንገቱን ይሉታል» ብዩ ሰፊ ማብራሪያ ሰጠሁ።

ንግግሬ የአማራ አንቂዎች እና የኢትዮጵያ መንግሥት እንዲያጠቁኝ ዕድል ሰጣቸው። ያደረኩትን ንግግር ቆራርጠው መልዕክቱን በመለወጥ ሕዝቡን ለማሳሳት ዘመቻ ጀመሩ። ጀዋር የክርስቲያኖችን አንገት በሜንጫ ቁረጡ ብሏል» በማለት ቪድዮዎችን ቆርጠው በመቀጠል እሰራጩ።

የሀይማኖት አክራሪ እንደሆንኩ ተደርጎ የተለያዩ ግለሰቦች እና ድርጅቶች እንደ ፌስቡክ እና ፓልቶክ ባሉ የማህበራዊ ትስስር ገፆች ቀሰቀሱ። እንዲሁም በተቃዋሚዎች እና በመንግሥት ሚዲያዎች ላይ እየተቀባበሉ በማስተላለፍ ሰፊ ፕሮፓጋንዳ አካሄዱብኝ። በጣም የገረመኝ ነገር ቪድዮውን ቆራርጠው የለቀቁት ሰዎች ለእኔ ቅርብ የሆኑ እና ስለ ሀይማኖት ያለኝን አመለካከት ጠንቅቀው የሚያውቁ፣ የጽንፈኝነትም ሆነ ሀይማኖታዊ መድሎን የሚያንጸባርቅ ሐሳብ እንደሌለኝ ምስክር ሊሆኑ የሚችሉ መሆናቸው ነው።

መጀመሪያ ላይ ዘመቻው ተጧጡፎ ሲካሄድ ብዙም አላሳሰበኝም። ሌሎች ሰዎች ግን «ውሸት ከተደጋገመ እውነት መስሎ ሕዝቡን የበለጠ ያሳስታልና ማብራሪያ ስጥበት› ብለው መከሩኝ። ምክራቸውን ተቀብዩ በፃፍኩት ግልጽ ደብዳቤ ውስጥ ተቆራርጦ እየተሰራጨ ያለው ቪድዮ የስም ማጥፋት ዘመቻ እንጂ እኔየተናገርኩትን ሙሉ በሙሉ የሚያንጸባርቅ እንዳልሆነ ጠቀስኩ። ንግግሩ የተለያዩ እምነት ተከታዮች በተገኙበት ስለተደረገ በአንድ ሀይማኖት ላይ ጥላቻ ለመፍጠር እንደሆነ ተደርጎ የሚነዛው ውሸት መሆኑንን ጻፍኩኝ።

እናቴ እና ባለቤቴ ከክርስቲያን ቤተሰብ ተወልደው ሳለ፣ በግራ እና በቀኝ በክርስቲያን ዘመዶች ተከብቤ እንዴት ክርሰቲያኖችን ጨርሱ ብዬ አውጃለሁ በማለት እየተካሄደ ያለው ዘመቻ የፖለቲካ አመለካከቴን ቀርቶ ማንነቴን የማያንፀባርቅ እንደሆነ ገለጽኩ። ይህ ማብራሪያ ሰፊውን ሕዝብ ያረጋጋ ቢሆንም በውሸት ስሜን ለማጠልሸት ያሰቡትን ግን አላስቆመም። በዚያ ፕሮፓጋንዳ በእኔ ላይ የተሳሳተ አመለካከት እንዲኖራቸው የተደረጉ ብዙ ሰዎች ቀርበው ሲረዱኝ ይፀፀታሉ፣ ይቅርታም ይጠይቁኛል። አንዳንድ የፖለቲካ አካላት ግን አሁንም እነዚህን ሀይማኖታዊ ፕሮፓጋንዳዎች በመድገም ስሜን ለማጥፋት መሞከራቸውን አላቆሙም። ለምሳሌ ወደ ኢትዮጵያ ከተመለስኩ በኋላ ስታሰር ከቀረቡብን የሐሰት ክሶች መካከል «ሕዝቡን በሀይማኖት አጋጭተኸል› እና «የኦርቶዶክስ ጳጳሳትን ለመግደል አቅደኸል» የሚሉት ይገኙበታል።

ምናልባት በሀገራችን ውስጥ በሀይማኖቶች መካከል ስላለው መስተጋብር፡ የሀይማኖት እና የፖለቲካን ግንኙነት በልምድ እና በትምህርት ከሚረዱ የፖለቲካ መሪዎች መካከል አንዱ ነን ብዬ አስባለሁ። ታሪኬ እንደሚያሳየው ውልደት እና አሥተዳደጌ የተለያዩ ሀይማኖቶችን ያቀፈ ነው።

ከአሥራ ሰባት ዓመቴ ጀምሮ ዓለምን ተዟዙሬ ብዙ ልምድ በማግኘት ሀይማኖቶችን ለማቻቻል ሥልጠና ስሰጥ ቆይቻለሁ። ኮሎምቢያ ዩኒቨርሲቲ እያለሁ ጀምሬው የነበረው የዶክትሬት ዲግሪ ምርምሬ በሀይማኖት እና በመንግሥት መካከል ባለው ግንኙነት ላይ ያተኮረ ነው። ካለኝ ግንዛቤ፣ የሕይወት ልምድ እና ትምህርት በመነሳት በኦሮሞ ውስጥ አልፎ ተርፎም በኢትዮጵያ ሕዝቦች መካከል የሀይማኖት ግጭት እንዳይፈጠር በተለያዩ መንገዶች ጥረት አድርጌያለሁ። ወደ ኢትዮጵያ ሰመለስም የሀይማኖት አባቶችን በመያዝ የሀይማኖት ችግር ወደተፈጠረባቸው ብዙ ቦታዎች በመሄድ እርቅ እና መረጋጋት እንዲፈጠር ጥረት አድርጌያለሁ። ነገር ግን ለዚህ መከራ ዋጋ መስጠቱ ቀርቶ የሀይማኖት አክራሪ እንደሆንኩ በሚዲያ ተዘመተብኝ፤ታስሬም የውሸት ክስ ተከፈተብኝ።

ከሀይማኖት ጋር ተያይዞ የሚከፈትብኝ የሰም ማጥፋት ዘመቻ ምክንያቱ ምን እንደሆነ ብዙ ጊዜ ራሴን ስጠይቅ ቆይቻለሁ። መልሱን አንድ በማኅበራዊ ሚድያ ላይ ፕሮፓጋንዳ የሚነዛብኝ ሰው ከፃፈው ሐሳብ መረዳት የሚቻል ይመስለኛል። ይህ ሰው በአንድ የፌሰቡክ ልጥፉ፡ ፡ጀዋር ሙሐመድ ማለት ግራኝ አሕመድ እና ሌንጮ ለታ ሲደመሩ የሚገኝ ውጤት ነው ብሎ ጽፉል። ሰውዬው ለማለት የፈለገው የኢትዮጵያን ታሪክ ለሚያውቁ ግልጽ ነው።

ከማንነቴ፡ ከልምዴ እና ከፓለቲካ ተሳትፎዬ የሚመነጩት የሀይማኖት ጉዳዮች በእኔ ላይ መደጋገማቸው ስለነገሩ እንዳስብ እና እንድማር አድርጎኛል። ኮሎምቢያ ዩኒቨርሲቲ በነበርኩበት ጊዜ የመንግሥት፣ የብሔር እና የሀይማኖት ግንኙነትን ማወቅ ስለፈለኩኝ ስለ ጉዳዩ የሚያጠናውን ታዋቂ ምሁር ፕሮፌሰር አልፍሬድ ሰቴፋን (Alfred Stepan) አማካሪ አድርጌ ያዝኩ። ፕሮፌሰር ሰቲፋን «የሁለትዮሽ መቻቻል (Twin Toleration) » የሚባል ፅንሰ-ሐሳብ በማመንጨት የሚታወቅ ሲሆን፣ ሐሳቡም መንግሥት እና ሀይማኖቶች ተቻችለው ለመኖር የሚያስፈልጋቸውን የሥነ-ምግባር ስልቶች ያቀርባል። እኔም ይህንኑ ሐሳብ ከኢትዮጵያ ነባራዊ ሁኔታ ጋር አያይዤ ሳጠና ነበር።

የመንግሥት እና የሀይማኖት (state and religion) ግንኙነት ከጥንት ጀምሮ አከራካሪ ጉዳይ ነው። ከ20ኛው ክፍለ ዘመን በፊት ሀይማኖት እና መንግሥት በአብዛኛው የተጣመሩ ነበሩ። አንዳንድ ሀገሮች ውስጥ የመንግሥት እና የሀይማኖት አሥተዳደር ተደባልቀው በአንድ ሰው/ቡድን ይመራሉ።

በሌላ ሀገር ደግሞ የመንግሥት ሕግጋት ከሀይማኖት መጽሐፍት የተቀዱ ይሆናሉ። ለምሳሌ ሀገር የሚተዳያደረው ከቁርኣን፣ከመጽሐፍ ቅዱስ እና ከመሳሰሉት በመነጨ ሕገ-መንግሥት ይሆናል። ሌሎች ሀገሮች ውስጥ ደግሞ የመንግሥት እና የሀይማኖት አሥተዳደር ተለይቶ ቢገኝም፤ንጉሱ ቅቡልነት ለማግኘት የሀይማኖት መሪዎች እና ተቋማትን ቡራኪ ይፈልጋል። ይህም የሀይማኖት ተቋም/መሪ የተቃወመው መሪ ከሥልጣን ሊወርድ (abdicate) ይችላል። በሌላ በኩል ደግሞ የአንድ ሀይማኖት መሪ በመንግሥት ይሾማል ወይም የመንግሥትን ይሁንታ ይፈልጋል። አሠራሩ ግን ቀሰ በቀሰ ችግር መፍጠር ጀመረ። በዚሀም ምክንያት መንግሥት በሀይማኖት

ውስጥ ጣልቃ እየገባ ነጻነታቸውን ከማሳጣቱም ባሻገር በሀይማኖቶች መካከልም መድሎ ፈጥሯል። ይህ ደግሞ ለሀይማኖት ግጭት ዋነኛ መንሰዔ ሆነ። በተለይ የሀይማኖት ቡድኖች እና አስተምሀሮዎች እየበዙ ሲሄዱ ወደ መንግሥት የተጠጋው የሀይማኖት ቡድን ሌሎቹን ሲጨቁን የተገፋው ደግሞ በማመጽ፡ በተለይም በአውሮፓ ከፍተኛ ግጭትን አስከትሏል።

የሀይማኖት እና የመንግሥት መቀለቀል ያሰከተለውን ጉዳት በሂደት በመረዳት ሁለቱን የመለያየት እንቅስቃሴ ተጀመረ። የመንግሥት እና የሀይማኖትን መለያየት የሚያቀነቅኑ ምሁራን ብዙ አሳማኝ መከራከሪያዎችን ያቀርባሉ። ለምሳሌ ንጉሥ ወደ ሥልጣን ለመምጣትም ሆነ ሥልጣን ለይ ለመቆየት የሀይማኖት አባቶች ቡራኬ ካስፈለገው፣ በገለልተኛነት ውሳኔ መስጠት አይችልም። በተመሳሳይ መልኩ በመንግሥት የሚሾም የሀይማኖት መሪ ሀይማኖታዊ አስተምህሮዎቹን ንጉሡን በሚደግፍ መልኩ አጣሞ በማቅረብ አማኙን ሊያሳስት ይቻላል። ይህም ቁሳዊ እና ሞራላዊ ንቅዘት ተደጋግፈው እንዲስፋፉ በር ይከፍታል። በተጨማሪም ሕገ-መንግሥት ከሀይማኖት ከመነጨ ለማሻሻል ይከብዳል። ሕገ-መንግሥት የተዘጋጀው ለምድራዊ ሕይወት ስለሆነ ነባራዊው ሁኔታ ሲቀያየር አብሮ ማሻሻል አለበት። በተቃራኒው የፈጣሪ ሕግ ፍጹም ስለሆነ ለማሻሻል ከባድ ይሆናል። ከሁለት እና ከዚያ በላይ ሀይማኖቶች ባሉበት ቦታ መንግሥት እና ሀይማኖት ከተቀላቀለ አድሎ፣ ጭቆና እና በሀይማኖቶች መካካል ውድድር ተፈጥሮ ግጭት እንዲነሳ ያደርጋል የሚሉ መከራከሪያዎች ናቸው።

በአብርሆት (enlightenment) ዘመን የተስፋፋው ይህ ሀይማኖትን ከመንግሥት የመነጠል (secularism) አሰተሳሰብ ተቀባይነቱ እየሰፋ ሲሄድ ሕገ-መንግሥትም ሆነ ሌሎች ሕጎች በፖለቲካ አካላት ሰምምነት አንጂ ከሀይማኖች መጽሐፍት እናተቋማት የሚቀዳ መሆን የለበትም የሚለው ሐሳብ ገዥ አየሆነ መጣ። በተጨማሪም የሀይማኖት እና የመንግሥት መሪዎች መሿሿም እና መሻሻር እንዲቀር ተደረገ።

በሀያኛው ክፍለ ዘመን የኮሚኒሰት ንቅናቄ የሴኩላሪዝምን ሐሳብ የበለጠ በመለጠጥ፤ ሀይማኖት የማኅበረሰብ ዕድገት ፀር ነው ወደሚል ጽንፈኛ አስተሳሰብ ተሸጋገረ። በዚህ ፀረ- ሀይማኖታዊ አስተሳሰብ (radical secularism) በአንዳንድ ሀገራት ኢ-አማንነት (Atheism) የመንግሥት ፖሊሲ ሆኖ ሀይማኖትን እስከ ማገድ ተደረሰ። ኮሚኒሰት ያልሆኑትም በብሔርተኝነት እሳቤ ተመርተው ለመዘመን ባላቸው ፍላጎት፤ ሀይማኖትን ከመንግሥት ማራቅ ብቻ ሳይሆን በማኅበራዊ ሕይወት ሳይቀር ለማፈን ሞከሩ። ዘመናዊ ቱርክን የገነባው ሙሰጠፋ ከማል አታቱርክ በእነዚህ አሳቤዎች በዋነኛነት ይታወሳል። ይህ የሀይማኖት እገዳ እና ጭቆና የአማኞችን ተቃውሞ እና አመጽ አስከትሎ ለጽንፈኝነት (religious fundamentalism) መወለድ ምክንያት ሆኗል። ከዚህ በመነሳት መፍትሔው “እንደ ጥንቱ ሀይማኖት እና መንግሥትን መቀለቀል ወይም ሀይማኖትን ማገድ ሳይሆን ማቻቻል ይሻላል" የሚለው ሐሳብ ሚዛን ደፋ። የአኔ ፕሮፌሰር አልፍሬድ ስቴፋን እና ባልደረቦቹ ያቀረቡት "Twin Toleration” የሚለው ሐሳብም የዚሁ መንግሥትን እና ሀይማኖትን የማቻቻል እሳቤ አካል ነው።

የሁለትዮሽ መቻቻል (Twin Toleration) ሐሳብ ሀይማኖት እና መንግሥቾ ያላቸው ግንኙነት በመገፋፋት ላይ የተመሠረተ መሆኑ ቀርቶ የትብብር ከሆነ ለሀገር ሰላም እና መረጋጋት ይጠቅማል የሚል ነው። የመንግሥት እና የሀይማኖቾ ግንኙነት መተባበር ላይ

የተመሠረተ እንዲሆን ሊተገበሩ የሚገባቸው መርሆዎች አሉ። እነሱም፤

1. ሁለቱም ወገኖች (ሀይማኖት እና መንግሥት) ለሌላው ነጻነት እውቅና መስጠት አለባቸው። ይህ ማለት መንግሥት በእምነት ተቋማት አሰተምህሮ፣ አካሄድ እና አሥተዳደር ላይ ለመወሰን ሥልጣን አይኖረውም። እንዲሁም የእምነት ተቋማትም በመንግሥት ሹመት፣ሕጎች እና መዋቅሮች ላይ የመወሰን ሥልጣን የላቸውም።
2. ከአንድ በላይ ሀይማኖት ባለበት ሀገር ወሰጥ መንግሥት ሁሉንም ሀይማኖቶች እኩል ማስተናገድ አለበት። እንዲሁም ከሁሉም ሀይማኖቶች በእኩል ርቀቱን መጠበቅ ይኖርበታል። በሌላ አነጋገር የመንግሥት ባለሥልጣናት እና ተቋማት አንዱን ሀይማኖት ወደራሳቸው አሰጠግተው ከመጥቀም፣ ሌለውን በመግፋት ከመጉዳት መታቀብ አለባቸው"22

እዚያው ኮሎምቢያ እያለሁ በ2013 በተካሄደው የኦሮሞ ጥናት ማኅበር (OSA) ስብሰባ ላይ "Twin Toleration" በሚለው ፅንሰ-ሐሳብ ላይ በመመሥረት የኦሮሞ ትግል የሀይማኖትን ጉዳይ እንዴት መያዝ እንዳለበት የጥናት ጽሑፍ አቅርቤ ነበር። በዚያ ጽሑፍ ላይ «የኦሮሞ ትግል ወደ ፀረ-ሀይማኖት (radical secularism) የተጠጋ ፓሊሲ ሲከተል ነበር» በማለት ሞግቼ, ፓሊሲውን ለመከተሉ ምክንያት ያልኳቸውን ነጥቦች እንደሚከተለው ዘረዘርኩ።

1. የኦሮሞ ትግል የጀመረው ኮሚኒዝም በዓለም ፖለቲካ፣ በተለይም በተጨቆኑ ሕዝቦች ትግል ውስጥ የርዕየተ-ዓለም የበላይነት ባገኘበት ዘመን ስለነበር፤ ብዙዎቹ ታጋዮች ሀይማኖት ሕዝብን ያደነዝዛል የሚለውን አስተሳሰብ ያቀነቅኑ ነበር። የሀይማኖት መሪዎች እና ተቋማት ሕዝቡን በማታለል፣ አእምሮውን በመስረቅ፣ ለትግል እንዳይነቃቃ በማድረግ ለጨቋኝ እና በዝባዥ ሥርዓት እንዲንበረከክ ያደርጋሉ። ስለሆነም ሀይማኖትን ከትግል ማራቅ እንደ ወሳኝ ስልት ታየ።
2. ትግሉ በጀመረበት የኃይለሥላሴ ዘመን፣ ንጉሣዊው ሥርዓት አንዱን ሀይማኖት ወደራሱ አሰጠግቶ ሌሎቹን የሚጨቁን በመሆኑ፡ አብዛኛው የኦሮሞ ሕዝብ በእነዚህ መድሏዊ ፖሊሲዎች ተጎጂ ነበር። ስለዚህም መንግሥትን እና ሀይማኖትን ለያይቶ እኩልነትን ማምጣት ከኦሮሞ ትግል ዓላማዎች አንዱ ሆነ።
3. እንደ ኦሮሞ የተለያየ ሀይማኖት ለሚከተል ሕዝብ፤ ሀይማኖት የመከፋፈል ምንጭ ተደርጎ ይወሰዳል። ስለሆነም የሀይማኖትን ጉዳይ ከትግሉ ማራቅ የመከፋፈልን አደጋ ለመከላከል ይጠቅማል ተብሎ ታሰበ።
4. ብሔርተኝነት ከማንነት መገለጫዎች ውስጥ የባሕል የበላይነትን የሚያቀነቅን ሲሆን፣ ሀይማኖት ነባር ባሕልን ያቀረቁዛል ተብሎ ይጠረጠራል። በ1980ዎቹ ኦነግ ለሁለት ሲከፈል፣ ክፍፍሉ ሀይማኖታዊ መልክ በመያዙ ሀይማኖታዊ ጉዳይን ከትግል ማራቅ በጣም አስፈላጊ እንደሆነ ታይቷል። በእነዚህ ምክንያቶች በኦሮሞ ትግል ውስጥ ሀይማኖትን ከማራቅ እና ከማግለለ ታልፎ እስከ

22 Stepan, Alfred C."Religion, Democracy, and the 'Twin Toleration'." Journal of Democracy, vol. 11, no. 4, Oct 2000, pp. 37-57.

ማጥላላት ተደረሰ።አካሄዱ የሕዝቡን አንድነት እና ትግሉን ለመጠበቅ የተወሰደ እርምጃ ቢሆንም ጉዳት ማድረሱ አልቀረም።ሀይማኖትለአደጋ ጊዜ ብቻ ሳይሆን ለትግሉ ያለውን ጥቅም መረዳት ያሰፈልጋል።ዜጎች ሙሉ በሙሉ በሚባል ደረጃ በፈጣሪ በሚያምኑበት ማኅበረሰብ ውስጥ ሀይማኖትን ጠልቶ፣ የሀይማኖች መሪዎች እና ተቋማትን አግልሎ ሕዝቡን በቂ በሆነ መልኩ በትግል ማሳተፍ አይቻልም።

የኦሮሞ ትግል በሀይማኖት በኩል በተፈጠረው ትሰሰር አንዳንድ ጥቅሞችን አግኝቷል። ለምሳሌ የፕሮቴስታንት ሀይማኖትን ከወሰድን ሀይማኖቱን በአፋን ኦሮሞ ለማስፋፋት በሚያደርጉት ሙከራ መንግሥት ቋንቋውን ለማቅጨጭ ያደርግ የነበረውን ጫና በመቋቋምረገድ ትልቅ ሚና ተጫውቷል።በተጨማሪም በፕሮቴስታንት ሚሽኖች በኩል በተፈጠረ የትምህርት ዕድል በኋላ ላይ ትግሉን የመሩ ሰዎችን በማፍራት ረገድ ትልቅ አሰተዋጽዖ ነበረው። የፕሮቴስታንት ፓስተሮች እምነታቸውን በቋንቋቸው የመስበክ መብትን ለማስከበር ሲታገሉ፤ በተተኪው ትውልድ ውስጥ ብሔርተኝነት እንዲ ጎለብት ሁኔታዎችን አመቻችተዋል።ከዚህ ባሻገር የፕሮቴስታንት ቤተ-ክርሰቲያን ከምዕራቡ ዓለም ጋር ያላት ግንኙነት የኦሮሞ ትግል ለሚፈልገው የዲፕሎማሲ ድጋፍ መንገድ መጥረጉ የሚታወቅ ነው።

በእስልምና በኩልም ሰናይ መንግሥት የሕዝቡን ማንነት ለመሸርሸር ሲከተል የነበረውን የብረዛ (assimilation)ፖሊሲ እንዳይሳካ እንቅፋት በመሆን፣ኦሮሞነትን ለማቆየት ረድቷል። ቋንቋን በማሳደግ ረገድ አኒይ እና ዳኒይ የሚባሉ የራያ ኦሮሞ ሼኾች አፋን ኦሮሞን በአረብኛ ፊደል በመፃፍ የኦሮሞን ትውፊት በማሰፋፋት ረገድ ፋና ወጊ መሆናቸውን ከታሪክ እንረዳለን።

በሐረርጌ በኩል እንደ ሼኽ በክሪ ሰጳሎያሉ ምሁራን መንግሥት አፋን ኦሮሞን ለማጥፋት ያደረገውን ሙከራ ለማክሸፍ አዲስ ፊደል እስከ መቅረጽ ደርሰዋል።ከዚህም ባለፈ ደረሶች (የእስልምና ተማሪዎች)እና ተከታዮቻቸውን ሰለ ኦሮሞ ታሪክ እና እየደረሰበት ስለነበረው በደል በማሰተማር ሐረርጌ የጨቋኙ ሥርዓት የእምቢተኝነት እና የብሔርተኝነት አስኳል እንድትሆን መሠረት ጥለዋል።

ከሺኽ በክሪ ሰጳሎ ተማሪዎች (ደረሳዎች) መካከል አንዱ ዶ/ርሼኽ ሙሐመድ ረጃድ አብዱሌ ፈለጋቸውን በመከተል የላቲን ፊደልን ለአፋን ኦሮሞ መጻፊያ እንዲያገለግል አድርገው ሠርተዋል።ዛሬ የምንጠቀምበት ቁቤ ሼኽ ሙሐመድ ረሻድ እና ኃይሌ ፊዳ ለየብቻ ያዘጋጁትን የሰዋሰው ስብስብ በማጣጣም የተዘጋጀ ነው። በተጨማሪም እስልምና በመካከለኛው ምሥራቅ ካሉት ሀገሮች ጋር ካለው ትሰስር የተነሳ የኦሮሞ ትግል ከአረብ ሀገሮች ያገኝ ለነበረው የመሣሪያ እና የዲፕሎማሲድጋፍ የራሱ ድርሻ አለው። የኦነግ የትጥቅ ትግል ሲጀመር በጃራ አባገዳና ኤሌሞቂልጡ ሲመራ የነበረው የመጀመሪያው ታጣቂ ቡድን ቁሮ ገነማ፤ ሰልጥኖ የታጠቀው በአረብ ሀገራት ውስጥ መሆኑ ይታወሳል።

በአጠቃላይ ሀይማኖት ትላንትም ለኦሮሞ ትግል ትልቅ ጥቅም ነበረው፤ ዛሬም ሆነ ነገ ሀይማኖት በህኅብረተሰብ እና በፓለቲካ ውስጥ ያለውን ሚና በትክክል ከተረዳን ፡ትግሉን ሊጠቅ ምበሚችልመልኩ ልንይዘው እንችለለን ።ሕዝባችን የሚከተላቸውን ሀይማኖቶች ለትግሉ በሚመች መልኩ ካልተጠቀምንባቸው ጠላት እኛን የሚጎዳበት መሣሪያ ሊሆን ይችላል። በእነዚህ ምክንያቶች የኦሮሞ ትግል በሀይማኖታዊ ጉዳይ ሰኬታማ ለመሆን “Twin Moderation Secularism” ስልትን ከእኛ ነባራዊ ሁኔታ ጋር ባጣጣመ ልኩ መጠቀም አለበት የሚል ሐሳብ በዚያ የPOSA ዓመታዊ ሰብሰባ ላይ አቀረብኩ ።በኦሮሞ ውስጥ የሀይማኖት እና የፖለቲካ

ግንኙነታች ጠቃሚ ሊሆን የሚችለው የሚከተሉት ነጥቦች ሲተገበሩ ነው ብዬም ምክረ ሐሳብ ጨመርኩበት፡

-የፖለቲካ ድርጅቶች ከሁሉም ሀይማኖቶች በእኩል ርቀት ላይ ሲገኙ፡

-የፖለቲካ ተቋማት እና የሀይማኖት ተቋማት እውቅና መሰጣጠት ሲችሉ፣

-የፖለቲካ አመራር/ድርጅት ለሁሉም ሀይማኖቶች መብት እና እኩለነት በግለጽ መታገል ሲችሉ፣

-የሀይማኖት አመራር/ተቋም ለብሔር መብት እና ጥቅም በግልጽ ሲታገል፡

- እንዲሁም ኦሮሞ የሚከተለውን ሀይማኖት የባዕድ አድርጎ ከመፈረጅ እና ከማየት ይልቅ ከነባር ባሕል ጋር ተመጋጋቢ እንዲሆን ሲደረግ(ይህም ማለት በሀይማኖታዊ ትምህርቶች፡ምልክቶች፡ መዝሙሮች እና በዓላት ላይ የኦሮሞ ቋንቋ፣ ባሕል እና ታሪክ እንዲንጸባረቅ ሲደረግ) ።

አንዳንድ ጊዜ "ብሔርህ ወይስ ሀይማኖትህ ነው የሚቀድመውን ።የሚል ጥያቄ ይነሳል። ይሀ ችክክለኛ ጥያቄ አይደለም።አንድ ሰው ብዙ ማንነቶች ሊኖሩት ይችለሉ። ብሔር፤ ሀይማኖት፣ ፆታ ።ሙያ እና የመሳሰሉት ይጠቀሳሉ። ለምሳሌ አያንቱ የተባለችን ሰው ብንወስድ ሴትነት ከማንነቷ ውስጥ አንዱ ስለሆነ፣ለጾታ እኩልነት በሚደረግ ትግል ላይ ልትሳተፍ ትችላለች። ሀይማኖቷ ክርሰትና ከሆነ ፡ይህም አንዱ ማንነቷ ነው፡ኦሮሞነት የብሔር ማንነቷ ነው። ከሦሰቱ ማንነቶች አበላልጠሸ አንዱን ምረጪ መባል የለባትም ።አንዱን ማንነት ከፍ አድርጎ ሌለውን ገሸሽ የሚያደርግ ፖለቲካ፣አሷን ወደተቃራኒ አቅጣጫ አንድትሄሂድ ሊያደርጋት ይችላል።

በአጠቃላይ ሀይማኖትና ፖለቲካ አንዱ ሌላውን ሊውጥም ሆነ ሙሉ ለሙሉ ሊዋሃዱ ወይም ፍጹም ሊነጣጠሉም የማይችሉ ጉዳዮች ሰለሆኑ ፡መፍትሔ ውበ ብልሃት አቻችሎ ማስኬድ ነው። የብሔር ጭቆና ባለበት የሀይማኖት ነጻነት፣ የእምነት መድሎ ባለበት የብሔር እኩልነት ሊኖር ሰለማይችል፣ከሁለቱ በተጨማሪ ሌሎች ማንነቶች እና የግለሰብ መብት የሚከበርበት ፖለቲካዊ ሥርዓት ለመገንባት መትጋት ያስፈልጋል።

## 6.6 የ'oromo first'ዘመቻ

ስለ ኢትዮጵያ፣አፍሪካ ቀንድ እና መካከለኛው ምሥራቅ በየጊዜው በምጽፋቸው ጽሑፎች እና በምሰጣቸው ትንታኔዎች ምክንያት በርካታ ዓለም አቀፍ ሚዲያዎች ቃለ-መጠይቅ ያደርጉልኛል። በተለይም ከ2002 የኢትዮጵያ ሀገራዊ ምርጫ ጀምሮ የአልጀዚራ ቴሌቭዥን ጣቢያ ላይ ቀርቤ በተለያ ዩርዕሰ-ጉዳዮች ዙሪያ ትንታኔዎችን አቀርብነበር። ሜይ 23 ቀን 2013 የኮሎምቢያ ዩኒቨርሲቲ ቤተ-መጻሕፍት ውስጥ እያለሁ፣«በኦሮሞ እና በኢትዮጵያ ጉዳይ ላይ በአልጀዚራው «Aj-stream»ፕሮግራም ላይ ተሳታፊ እንድትሆን ጋብዘንኸል›» የሚል የኢሜል መልዕክት ደረሰኝ።

ጣቢያው ወደ ሚገኝበት ከተማ የሚወስደኝ የባቡር ትኬት ልከውልኝ ጉዞዬን ጀመርኩ። በመንገዴ ላይ ከጥቂት ቀናት በፊት ከሀገር ቤት የተላከልኝን "waa'ee keenya"የሚለውን የሀጫሉ አልበም እየሰማሁ ነበር። "Maasan Gamaa" የሚለው ዘፈኑ ላይ ስደርስ በጣም ሰለሰበኝ ደጋግሜ ማዳመጥ ጀመርኩ ።ዘፈኑ ሕዝባችን ላይ ሲደርስ የነበረውን ግፍ፣በደል እና ዘረፋ በዓይነ-ኅሊናዬ እየመላለሰ ስሜቴን ቀሰቀሰው።የኦሮሚያን ውብ ተራሮች እና ሸለቆዎች በምናብ ሰወጣና ስወርድ ጉዞው ሳታወቀኝ ዋሽንግተን ዲሲ ደርሼ ወደ አልጀዚራ ስቱዲየ ዘለኩ።

ስቱዲዮ ስደርሰ ተዘጋጅተው ሲጠብቁን የነበሩ ሁለት ሴት ጋዜጠኞች ተቀበሉኝ። ዝግጅቱ በቃለ- መጠይቅ ሳይሆን በክርክር መልክ ስለሆነ ማሰታወሻ መያዝ አትችልም ብለው የያዝኩትን ደብተር ውጭ አውጥተው እኔን ከጎናቸው አሰቀመጡኝ።ከፊቱ ያለውን "ስክሪን"ስመለከት ሙሐመድ አደሞ እና ዶ/ር ታደሠ ኤባ ተዘጋጅተዋል። ሙሐመድ አደሞ እንደ ጋዜጠኛ፣ ዶ/ር ታደሠ ኦነግን ወክሉ።እኔ ደግሞ እንደ ተንታኝ ቀረብን።የኢትዮጵያ መንግሥት ተወካይ ተጋብዞ እንደቀረም ሰማን።

ጋዜጠኖቹ ሰለ ዝግጅቱ በትዊተር(አሁን "ኤክስ/X።" በሚል ተቀይሯል) ላይ አስቀድመው በማስተዋውቅ ፡ተመልካቾች ጥያቄዎችን እንዲልኩላቸው ጋብዘውና ጥያቄዎቹን ሰብሰበው ለእኛ ያቀርቡ ጀመር። የኢትዮጵያ መንግሥት በኦሮሞ ሕዝብ ላይ ከድሮ እስከ ዘንድሮ እያደረሰ ያለውን በደል ስናገር የሰማቸው ጋዜጠኛ ድንገት፣ «Jawar,are you oromo first. Or Ethiopia first>>በማለት ያልጠበኩትን ጥያቄ ጠየቀችንኝ። «የምታሰቀድመው ኦሮሞነትን ነው ወይስ ኢትየዮጵያዊነትን» እንደ ማለት ነው።ጋዜጠኛዋ የጠየቀችኝ ጥያቄ ያልጠበኩት ስለነበር ትንሽ እንደማሰብ ብይ <<I am oromo frist,Ethiopia was Imposed on me(እኔ መጀመሪያ ኦሮሞ ነኝ፤ኢትዮጵያዊነት ተጭኖብኝ ነው) >› አልኳት። ይሀንን መልስ የሰጠሁበት በሁለት ምክንያቶች ነበር።

አንደኛው ፣ከድሮም ጀምሮ እኔም ሆንኩ ሌሎች የኦሮሞ ብሔርተኞች የምንገልጸው ቀዳሚ ማንነታችን ኦሮሞ እንደሆነ ለማሳወቅ ነው።በኢትዮጵያ ሀገረ-መንግሥት ምሥረታ ውስጥ መንግሥት ኦሮሞነትን ለማፈን ይሞክር ስለነበር፡ትግሉ ሲጀመር ኦሮሞነትን በኩራት

ማቀንቀን የጋራ ማንነትን መልሶ ለመገንበት አስፈላጊ ነው። እንዲያውም ኦሮሞነትን ማቀንቀን እና ኢትዮጵያዊነትን ማጥላላት በተለይ በዲያስፖራው ዘንድ የብሔርተኝነት መለኪያ ነበር። የእኔ ትውልድ ለአቅመ-ፖለቲካ ስንደርስ ከኢትዮጵያዊነት ይልቅ ኦሮሞነትን ማስቀደም ልማድ (norm) ሆኗል።

ወጣቶችን በምናደራጅበት ወቅት የነበረው አንዱ ክርክር ማንነታችን ኦሮሞ መሆኑ ላይ ስምምነት ሲኖር፣ «ሀገራችንን ኢትዮጵያ ወይስ ኦሮሚያ አንበል?›» የሚለው ነው። አብዛኞቹ ወጣቶች በተለይ ዲያስፖራ ያደጉት «ብሔረ ኦሮሞ፣ ሀገሬ ኦሮሚያ ነው, ይላሉ። አንዳንዶች ደገሞ ብሔራቸው ኦሮሞ መሆኑን ገልጸው ሀገራቸውን ኢትዮጵያ ብለው ይጠራሉ።

ከአርፋሴ ጋር ደጋግመን የምናደርገው ሙግት ትዝ ይለኛል። ፈረንጆች ከየት ሀገር እንደሆንን ሲጠይቁን እሷ ሁሌም ከ«ከኦሮሚያ›› ብላ ሰትመልስሰ፣ ኦሮሚያ የት ነውን የተመሠረተችው መቼ ነው? የሚሉ ጥያቄዎች ሰለሚያነሱ፡ ጊዜ ወሰዳ ታሪክ እና ጂኦግራፊ እያጣቀሰች ታሰረዳለች። ለዚህ ትዕግሥት ሰለሌለኝ «ኢትዮጵያን ስል ትናደድ ነበር፡ ስለዚህ እሷ ባለችበት ሀገሪ የት እንደሆነ ስጠየቅ «ቻይና, ማለትን መረጥኩ። ውሸቴን መሆኑን አውቀው ሲደናገሩ «ዓይኔን አታዩም እንዴ›› እላቸው ነበር።

ሁለተኛው ምክንያት በማንነት ግንባታ እና ቅደም-ተክተል ላይ በርካታ ኮርሶችን ሰለወሰድኩ፡ መጽሐፎችን ምሰ ላነበብኩ፤እንዲሁም የጋዜጠኛዋ ጥያቄ ከምን እንደመነጨ ሰለተረዳሁ ነበር። ዘመናዊ ሥርዓት-መንግሥት (modern nation state) ከተፈጠረ አንሰቶ፣ በብሔር እና በሀገራዊ ማንነት መካከል መኖር ሰላለበት ግንኙነት በምሁራን እና በፓለቲካ ቡድኖች መካከል የሐሳብ ልዩነት እና ክርክር አለ። አንዱ ሐሳብ፣ ሀገራዊ አንድነትን ለማረጋገጥ በአንድ ሀገር ውስጥ ያሉ የብሔር ማንነቶች ተጨፍልቀው (assimilation) አንድ ወጥ ብሔራዊ ማንነት መፈጠር አለበት የሚል ነው። ሁለተኛው ሐሳብ፣ የብሔር እና ሀገርዊ ማንነት በአንድ ሀገር ውስጥ ጎን ለጎን መኖር ስለሚችሉ መደፍጠጥ አያስፈግም የሚል ነው። እንዲያውም ለመደፍጠጥ መሞከር አንድነትን ከማጠናከር ይልቅ ብሔርተኝነትን ቀሰቅሶ የሀገር መፍረሰ አደጋን ይጋብዛል ይላሉ። የብሔር ማንነት ተደፍጥጦ ወጥ በሆነ ሀገራዊ ማንነት መተካት አለበት የሚለው ሐሳብ እንደ ፈረንሳይ ባሉ ጥቂት ሀገሮች የተሳካ ቢሆንም፣ በርካታ ሀገሮች ላይ ግን የአመጽ እና ያለመረጋጋት መንሰዔ በመሆን ሀገራትን እስከማፍረስ ደርሷል።

አብዛኛው የሀገር ግንባታ (state formation) ሂደት የሚጀመረው በብሔሮች መካከል በሚደረግ ጦርነት ነው። ከተፋላሚ ብሔሮች አንዱ ሌላውን በጉልበት አሰገብሮ በእርሱ የበላይነት የሚተዳደር አንድ ሥርዓት-መንግሥት ይፈጥራል። ይህም አሸናፊው ቡድን ኢኮኖሚያዊ፣ ማኅበራዊ እናፖለቲካዊ የበላይነትን እንዲጎናጸፍ በማድረግ መበላለጥ (inequality) ያስከትላል። በአንድ ሀገር ውስጥ የተለያዩ የብሔር ማንነቶች መኖራቸው ሀገራዊ አንድነትን ያዳክማል በሚል ሰበብ ሌሎቹን ጨፍልቆ የሚገነባ አንድ ወጥ ብሔራዊ ማንነት፡ የአሸናፊውን ቡድን ማንነት አንጂ ብዝኀነትን አያንፀባርቅም። በተጨማሪም የአንድን ቡድን ማንነት በዘላቂነት ብሔራዊ ማንነት ለማድረግ የኃይል እና የኢኮኖሚ የበላይነት ማስፈን ግደታ ስለሆነ የኢኮኖሚ ጭቆና እና አድሎ ይኖራል። ይህ ጭቆና በተገፋው ሕዝብ ዘንድ ቅሬታ ይፈጥርና ሲጠራቀም አመጽን ይወልዳል።

ሀገረ-መንግሥቱ ተጨቆንኩ የሚለው ማኅበረሰብ የሚያሰማውን ሰሞታ በመረዳት ለውጥ

የማያመጣ ከሆነ፤ በብሔራዊ እና በሀገራዊ ማንነት መካከል ያለው ተቃርኖ እያደገ ይሄድና የጭቁኑ ብሔር ተወላጆች የብሔር ማንነታቸውን የበለጠ እያቀነቀኑ ሀገራዊ ማንነትን ገሸሽ ወደማድረግ ያመራሉ።

ይህ የብሔር እና የሀገራዊ ማንነት ተቃርኖ ሦስት ውጤቶችን ሊያስከትል ይችላል። የመጀመሪያው በሥልጣን ላይ ያለው ቡድን የብሔሮችን ማንነት በኃይል በመጨፍለቅ ሀገራዊ ማንነት ይገነባል። ሁለተኛው፣ ማንነታቸውን ለመዋጥ በተደረገ ጥቃት ላይ ያመጹ ሕዝቦች፤ መንግሥት የሚያደርገውን መከራ በማክሸፍ በሚያደርጉት ትግል ነጻ ሀገር የሚያቋቁሙበት ሁኔታ ሊፈጠር ይችላል። ብዙ ኢምፓየሮች ፈርሰው የተለያዩ ሀገራት የተመሠረቱት በዚህ አካሄድ ነው። ሦስተኛው፣ ሕብረ-ብሔራዊ ማንነቶችን የመጨፍለቅ ሙከራ ሲቀር ወይም ሲከሽፍና የብሔር ማንነቶች ሲከበሩ፡ በሂደት በሚደርግ ፖለቲካዊ፣ ኢኮኖሚያዊ እና ማኅበራዊ ትሰሰር ሀገራዊ የጋራ ማንነት ሊወለድ ይችላል። ይህ ሲሆን ብሔረሰባዊ እና ሀገራዊ ማንነቶች ከተቃራኒነት ወደ ተመጋጋቢነት (complimentary and compatible) ይቀየራሉ።

ወደ ኢትዮጵያ ፖለቲካ ስንመለስ በምኒሊክ እና በኃይለሥላሴ ዘመነ-መንግሥቶች ሀገሪቷ ውስጥ ያሉ ብዙ ብሔሮችን ጨፍልቆ አንድ ሀገራዊ ማንነት የመገንባት ፖሊሲ ነበር። በጦርነቱ የበላይነት የነበረው የአማራ ወገን ማንነት ሀገራዊ እንዲሆን እየተሠራ፡ የሌሎች ብሔሮች ማንነት እንዲጨፈለቅ ሙከራ ተደርጓል። ይህ ደግሞ በሂደት የኦሮሞን ጨምሮ የሌሎች ብሔሮችን ተቃውሞ እና አመጽ ቀሰቅሷል። ግጭቱን ብሔሮች የራሳቸውን ማንነት እያወደሱ፥ በአንድ ማንነት አምሳያ የተቀረጸውን ኢትዮጵያዊነት ማጥላላት የትግላቸው አካል አደረጉት።

አንተ መጀመሪያ ኦሮሞ ነህ ወይስ ኢትዮጵያዊ?» የሚለው ጥያቄ እና መልስ መነሻው ይኸው ነው። የአልጀዚራዋ ጋዜጠኛ የጠየቀችኝ ጥያቄ አዲስ አይደለም፣ በኢትዮጵያዊነት እና በኦሮሞነት መካከል ያለው ቅራኔ ከኢትዮጵያ መመሥረት እና ክኦሮሞ ትግል ውልደት አንሰቶ የነበረ ነው።

ምኒሊክ ኢትዮጵያን ከመሠረታት ጀምሮ፣ የአማራ ማንነት የኢትዮጵያ ብሔራዊ ማንነት እንዲሆን በጉልበትም በብልኃትም ተሞክሯል። አማርኛ የትምህርት እና የመንግሥት ሥራ ቋንቋ ሲደረግ አፋን ኦሮሞ ተከልክሏል። የአማራ ባሕል እንደ ሥልጣኔ ሲታይ፡ የኦሮሞ ባሕል እንደ ኋለቀርነት ተቆጥሮ ተንኳሷል። አንድ ሰው ትክክለኛ ኢትዮጵያዊነትን ለመጎናጸፍ ኦሮሞነቱን ማውለቅ ነበረበት። የትምህርት ዕድል ያገኙ ዜጎች ትምህርት ቤት በገቡ ማግሰት ቤተሰቦቻቸው ያወጡላቸውን የኦሮሞ ስም በመተው ወደ አማራ ስም የሚቀይሩት በዚህ ምክንያት ነበር። ይህ የኦሮሞን ማንነት በመግፋት ከአማራ ማንነት ብቻ የተሠራውን ኢትዮጵያዊነት የመጫን ግፊት የኦሮሞ ሕዝብን ተቃውሞ ወልዷል። መጀመሪያ ላይ ኢትዮጵያዊነትን ከብሔር ማንነታቸው አስበለጠው የነበሩ እንደ ጄኔራል ታደሠ ብሩ ያሉ የመንግሥት ባለሥልጣናት ሳይቀር በሂደች በተፈጠረ የመገፋት ሰሜት ወደ ብሔር ማንነታቸው ተመልሰው ለማመጽ ተገደዱ። ከእነሱ በኋለ የመጣው ትውልድ በአንድ በኩል በኦሮሞ የትግል ጎራ ኦሮሞነት ይበልጥ እንዲቀነቀን በሚከወን የፖለቲካ ሥራ፡ በሌላ በኩል መንግሥታት በኢትዮጵያዊነት ስም የሚፈጽሙትን በደል እየተመለከተ ስላደገ ብሔርተኝነቱ ጠንካራ መሆን ቻለ።

በአጠቃላይ «Oromo First» ብዬ ልመልs የቻልኩች ከልጅነቴ ጀምሮ ይዤ ባደኩት

አመለካከት እና ከትምህርት ቤት ባገኘሁት ግንዛቤ ላይ ተመስርቼ ነው። በኦሮሞ ፖለቲካ ውስጥ የብሔራችንን ማንነት ማስቀደም የተለመደ ስለነበር «Oromo First» ብዬ መመለሴ ብዙም አነጋጋሪ (controvesial) ይሆናል ብዬ አላሰብኩም ነበር። ውይይቱን ጨርሼ ከአልጀዚራ ስቱዲዮ ስወጣ ስልኬ በጥሪዎች እና መልዕክቶች ተሞልቷል። ፌስቡክ እና ትዊተር ስከፍት አሳቱ ነዷል፣ ኦሮሞዎቹ ሲያሞግሱኝ ሌሎቹ ያወግዙኛል። በቀጣዮቹ ቀናት በማኅበራዊ ሚዲያ፡በሬዲዮ እና በቴሌቪዥን ከፍተኛ እና የተቀናጀ ዘመቻ ተከፈተብኝ።

አንድ ቀን ወዳጄ እና ከ2005 ጀምሮ አብረን ሰንሰራ የነበረው ኤሊያስ ኢብሳ ደውሎልኝ ሰናወራ የተከፈተብኝን ዘመቻ ወደ ዕድ ልመቀየር አንዳለብን ተሰማማን። ከዚሂያበፊት በኦሮሞ ላይ የሚነዛውን ፐርፓጋንዳ ለመመከት እና ትግሉንም ለማጠናከር ሚዲያ ማቋቋም  እንደሚያሰፈልግ ስንወያይ ስለነበር፡የሚካሄድብኝን ዘመቻ ለመመከት የሚያሰችል ዘመቻ  ለማድረግ ወሰንን። የንትርኩ መነሻ የሆነው «Oromo First»ም የዘመቻችን ስም እንዲሆን ተሰማማን።

ዘመቻችን ሁለት ዓላማዎች ነበሩት፡- 1ኛ) ከእኔ አልፎ በኦሮሞነት ላይ የተከፈተውን ዘመቻ ኮመመከት ባለፈ፡ ሕዝባችንን መልሶ ለማንቃት ስንሰራ የነበረውን ሥራ ለማጠናከር፡ 2ኛ) የዲያስፖራውን ሕዝብ መነቃቃት ተጠቅመን ገንዘብ በማሰባሰብ ለኦሮሞ ሕዝብ ትግል ድምፅ የሚሆን አንድ ሚዲያ ማቋቋም ናቸው።

በዚሁ መሠረት የመጀመሪያውን ዝግጅት በሚኒሶታ የኦሮሞ ማኅበረሰብ አዘጋጅቶ ጠራን። ማኅበረሰቡ ዝግጅቱን ያሰናዳው እንደ ግለሰብ በተከፈተብኝ ዘመቻ ሞራሌ አንዳይነካና  በአንድ ኦሮሞ ላይ የሚከፈትን የጥላቻ ዘመቻሁሉም ኦሮሞ በጋራ እንደሚመክከት ለማሳየት ነበር። በወቅቱ አዳራሽ ውስጥ የታደመውን በመቶዎች የሚቆጠር ሕዝብ ሰመለከት የተለየ ስሜት ተሰማኝ። የኦሮሞ ሕዝብ የቁርጥ ቀን ሲመጣአንዴት አብሮ እንደሚቆም አየሁ። በመድረኩ ላይ በአጋጣሚ ከሀገር ቤት መጥቶ ሚኒሶታ የነበረው ዶ/ር ገመቹ መገርሳ ሕዝባችን ኦሮሞነቱን ለምን እንደሚወድ እና ሌሎች ለምን እንደሚያጠቁት ንግግር አደረገ።  በተጨማሪም “Oromo First” የሚለው ንግግር የኦሮሞን ሕዝብ አነቃቅቶ ባላንጣዎቹን  ለምን እንዳስከፋ ለታዳሚው በዝርዝር አስረዳ።

ከሚኒሶታ ቀጥሎ በአሜሪካ፣ በካናዳ እና በአውሮፓ ወደሚገኙ ብዙ ከተሞች በመንቀሳቀስ ለወራት የዘለቀ ዘመቻ አካሄደን። ዘመቻውን በሂደት ወደ ሕዝባዊ የምክክር መድረክ አሳደግነው። በአነዚህ ሕዝባዊ መድረኮች እኔ እና ሌሎች ምሁራን የኦሮሞን እና የዓለም ጭቁን ሕዝቦችን የትግል ውጣ ውረድ ታሪክ እናሰተምራለን። መድረኮቹ የአዳራሽ ውስጥ ውይይት (Townhall Meeting) መልክ ነበራቸው። ይህ ማለት ምሁራን የመነሻ ሐሳብ ካቀረቡ በኋላ ተሳታፊዎቹ በነጻነት ጥያቄ እና ሐሳባቸውን ያቀርባሉ።

ይሀን መሰል ክፍት ውይይት ያደረግንበት ምክንያት የኦሮሞ ትግለ በመዳከሙ በውጭ የሚኖረው ማኅበረሰ ብሞራሉ ተሰብሮ አርሰ በአርስ ኮመወያየት ይልቅ በቡድን ተከፋፍሎ  መተማማት እና መወነዳጀል በመለመዱ ነበር። ዲያስፖራው በቡድን ተከፋፍሉ ሲያደርግ የነበረው ዘመቻ ሀገር ውስጥ ያለውን ሕዝብ ሞራልም ጎድቷል። የፖለቲካ ድርጅቶች ኮጊዜ ወደ ጊዜ አየተከፋፈ መሄዳቸው እና ትግሉ ወደፊት መራመድ አለመቻሉ የኦሮሞ ማኅበረሰብ ውስጥ የጋራ ሞራላዊ ስብራት (collapse of collective self –

esteem) አስከትሏል። ለዚህ አንዱ ማሳያ ኦሮሞ በደረሰበት ሁሉ የሚያወራው ድክመቱን ብቻ ነው። ለቅሶ ቤት፣ሰርግ ቤት እናመዝናኛ በታዎች ላይ ሲገናኝ «ኦሮሞ ዋጋ የለውም፤ አይሰማማም፣ አንድነት የለውም› በማለት *ያማርራል*። በአንጻሩ ኦሮሞ ያልሆኑትን ኃይሎች ከአቅማቸው በለይ አግዝፎ ያወድሳል። «ሃምሳ ሚሊዮን ኦሮሞ በአምስት ሚሊዮን ሰዎች ይገዛል፤ እነርሱ ጠንካራ አንድነት አላቸው። አመራራቸው ብልህ እና ጀግና ነው› የሚሉ አመለካከቶች መስፋፋታቸው የሕዝቡን ሥነ-ልቦና ክፉኛ ጎድቶታል።

በራስ ወገን ድክመት አየቆዘሙ እና የባለንጣን ጥንካሬ እያገዘፉ ማቅረብ የጋራ ሞራላዊ ስብራት ምልክት ስለሆነ ይህን ሥነ-ልቦና ሳንቀይር ትግሉን ወደ ፊት አንድ አርምጃ ማራመድ እንደማንችል ተገነዘብን። "አይቻልም" የሚለውን አመለካከት ወደ "ይቻላል፣ “አንድነት የለንም” የሚለውን “አንድ ነን ወደ ሚለው ለመለወጥ ሰራን።

የጋራ ሞራላዊ ሰብራትን ለማከም ሁለት ስልቶችን ተጠቀምን። የመጀመሪያው የትላንቱን የጋራ ስኬት ታሪኮች ማሰታወስ ነበር። ይህን ለማሳካት በኦሮሞ ትግል ውስጥ የተከናወኑ አዎንታዊ ኹነቶችን የሚዘክር ታሪካዊ የመታሰቢያ ዝግጅቶችን እሰናዳን።

ከ2012 እስከ 2013 የተዘጋጁት የአፍረን ቀሎ 50ኛ ዓመት መታሰቢያ፣ የባሌ ሕዝብ እንቅስቃሴ መታሰቢያ፣ የሜጫ እና ቱለማ ምሥረታ እና አሊ ቢራ ሙዚቃ የጀመረበት 50ኛ  ዓመት አየዮቤልዩ ትልቅ ፋይዳ ነበራቸው። ከዚያ በፊት በሚጠሩ የኦሮሞ ሕዝባዊ ስብሰባዎች ላይ የሚታደሙ ሰዎች በጣት የሚቆጠሩ ነበሩ። በየመድረኩ የቡድኖች መወጋገዝ እንጂ ተጨባጭ እና መሬት የሚወርድ ሐሳብ ወይም ሥራ አልነበረም።

የትለንትን በጎ ገድል በሚያወሱ ዝግጅቶች ላይ አንጋፋ ታጋዮችን ጨምር በቡድንተኝነት ሰበብ ተራርቆ የነበረ ሕዝብ በሰፋት መገናኘት ቻለ። በክፉ ዘመናት ውስጥ አብረው ያሳለፉትን መከራ እና ደሰታ በማስታወስ ጊዜያዊ አለመሰማማትን ለማለፍ አጋዥ ሆነ። አሊ ቢራ ዘፈን የጀመረበትን ሃምሳኛ ዓመት መታሰቢያ ያዘጋጀን ዕለት የኦሮሞን ስብሰባ ለረጅም ዓመት እርም ብለው የነበሩ በመቶዎች የሚቆጠሩ ሰዎች ታደሙ። በሐረርጌ የጦርሜዳ በረሃ፣ በሶማሊያ፣ በጅቡቲ እና በሳኡዲ የሰደት መከራን አብረው ሲቀምሱ ቆይተው፡ በአንጃዎች የተለያዩ ታጋዮች ዝግጅቱ ላይ ተገናኝተ ናፍቆታቸውን ተወጡ።

እ.አ.አ. በ2013 ጃራ አባ ገዳ ሲሞት ገላሳ ዲልቦና ሌንጮ ለታን ጨምሮ ከእርሱ ጋር በትግል መስመር ተለያይተው እና ተዋግተው የነበሩ ሰዎች ሚናውን ዘከሩ። ሕዝቡ እነዚህ አንጋፋ መሪዎች እንደቀድሞው በቡድንተኝነት ሳይሆን በወንድማማችነት እና በኦሮሞነት ስሜት ጃራ የሚገባውን ክብር ሲሰጡ በመሰማቱ ቁስሉ መሻር እና ሞራሉም መታደስ ጀመረ። በዚህ ሁኔታ የትለንትን ታሪክ የሚያዕታውሱ ዝግጅቶችን ማዘጋደት ትልቅ ጥቅም አስገኘ። በወቅታዊ ጉዳይ ላይ ሕዝቡን ማሰተባበር ካልተቻለ የቀደመውን የድል ትውስታ እና የጋራ ደስታ እንደ መሰባሰቢ ያመጠቀም ትልቅ መፍትሔ እና ጥቅም እንዳለው አየን።

ሁለተኛው ስልት ኦሮሞ ዛሬም እንደ ትላንቱ ውጤታማ ሊሆን እንደሚችል ለማሳየት፤ ጥቃቅን ነገር ግን ጉልሀ ተምሳሌታዊ ፋይዳ (symbolic value) ያላቸውን ሥራዎች አከታትሎ ማከናወን ነበር። ለዚሀ OMN የማቋቋም ፕሮጀክትን ተጠቀምን። የብሔርተንነት ስሜትን  ለማነቃቃት የምናደርገውን የOromo First ዘመቻ ከገቢ ማሰባሰቢያ ዝግጅት ጋር አጣመርነው። የትለንቱ ኦሮሞ እንደ ዛሬው ብዙ መነቃቃት ባልነበረበት ዘመን ብዙ ታሪክ ከሰራ፡

ዛሬም የበለጠ ሊሰራ እንደሚንገባ እና እንደሚችል በሕዝባዊ ስብሰባዎች ላይ አስተጋባን።
ይህን ስናደርግ ሕዝቡ በጥርጣሬ እንደሚሰማን እናውቃለን። የተለያዩ የፖለቲካ ድርጅቶች ብዙ ጊዜ ለሕዝብ የገቡትን ቃል ከዳር ማድረስ ሰላልቻሉ፡ እኛንም ሕዝቡ እንደነገሩ ያዳምጠን አንጂ በልበ ሙሉነት ተሰፋ አልጣለብንም። የሕዝቡን ጥርጣሬ መቀየር የምንችለው ቃል የገባነውን ነገር በመፈጸም ብቻ ነበር። በተጨባጭ ሰርተን ለማሳየት ቃል የገባነው ጠንካራ የሚዲያ ተቋም ማቋቋም ሲሆን፣ ወደ ተግባራዊ ሥራ ከመሻንራችን በፊት የዲያሰፖራውን ማኀበረሰብ ሚናበ ግልጽ ማሰቀመጥ ነበረብን። በትግል ውስጥ የዲያሰፖራ ሚና መምራት ሳይሆን መደገፍ መሆኑን አሰረግጠን በመናገር፡ ድጋፉን ኮታች በተጠቀሱት አምስት መንገዶች ሊያበረክት እንደሚችል ጠቆምን። እነዚህም፣

1. *ዲፕሎማሲ፡- የውጭ ሀገራት መንግሥታት እና ድርጅቶች በኦሮሞ ሕዝብ ላይ የሚደርሰውን ጭቆና እንዲረዱ ብሉምትግሉን እንዲደግፉ ለማሳመን መሥራት፣*

2. *ጥብቅና* (Advocacy)፡- *ዲያሰፖራው የሚኖርባቸው ሀገራት ዜጎችእና እንደራሴዎች ሰለ ኦሮሞ ሕዝብ ያላቸውን ግንዛቤ ማሳደግ፤ አውቀት ማምራትና ማሰራጨት* (Knowledge Production & Dissemination) ፤ *- በዲያሰፖራ የሚኖረው ምሁር የኦሮሞ ሕዝብ ታሪክ፡ ባሕል እና የትግል ዓላማ ላይ ምርምር በማካሄድ፣ በመጻፍ እና በማሳተም ለተለያዩ አካላት እንዲደርs ማድረግ፣*

3. *የገንዘብ/ የቁሳቁሰ አርዳታ፡- ዲያሰፓራው ሰርቶ ሀብት ለማፍራት የተሻለ ዕድል ሰለለው ለትግሉ የሚሆን ቁሳቁስ ማቅረብ፣ እና*

4. *ሚዲያ፡- በኦሮሞ ሕዝብ ላይ የሚደርሰውን በደል ለማጋለጥ፣ የትግል ዓላማውን ለማሰተዋወቅ ሚዲያን መገንባት እና በአግባቡ መጠቀም ናቸው።*

ለሕዝባዊ ውይይት በምንንቀሳቀስባቸው ከተሞች ሁሉ እነዚህን አምስቱን የዲያስፓራ ሚናዎች ደጋግመን በመግለጽ፣ ግለሰቦች እና ቡድኖች ከአምሰቱ የተመቻቸውን መርጠው ተጨባጭ ደጋፍ ማድረጋቸው ትገሉን እንደሚያግዝ መከርን። ከሀገርውጭየሚኖርሰው ትግሉን መርዳት እንጂ መምራት እንደማይችል ለማሰገንዘብ፣ «ዲያሰፓራው ለትግሉ ማገር እንጂ ምሰሶ መሆን አይችልም› እያልኩ በየመድረኩ ደጋግሜ ተናገርኩ። ይሀንን ነጥብ በደንብ እንዲረዱ የቦክስ ውድድርን እንደ ምሳሌ ስጠቅስ ነበር። ይሀም ቦክሰ መወዳደር የሚፈልግ ሰው ቢያንስ ወደ መወዳደሪያ ሜዳ (ring) ውስጥ መግባት አለበት። መግባት ብቻ ሳይሆን ሊገጥመው የሚፈልገውን ሰው መምታት እናለ ራሱም መመታት በሚያሰችለ ውርቀት ላይ መቆም ይኖርበታል። መምታት እና መመታት ካልቻለ የውድድሩ አካል አይደለም። የቦክስ ሜዳ ውስጥ ለመግባት ወኔው፡ ሁኔታው፣ መሰፈርቱ የማይፈቅድለት ወይም ርቀት የሚገድበው ሰው ሊሆን የሚችለው ተወዳሪ ሰይሆን ቲፎዞ ነው።ተሰትፎው ሜዳው ውስጥ ገብቶ መወዳደር የሚችለውን ሰው መደገፍ ሲሆን፣ ድጋፉ ደግሞ በቁሳቆስ ወይም በሞራል ሊገለጽ ይችላል። አውነታው ይህ ሆኖ ሳለ፣በቦክስ ሜዳ ውስጥ ገብቶ ለመምታት እና ለመመታት የሚያስችል ርቀት ላይ መሆን ያልቻለ/ያልፈለገ ሰው ውድ ድሩ ውስጥ አንዳለ ማሰመሰል ለአውነተኛ ተወዳዳሪዎች ሊውል የሚገባውን ገንዘብ እና ሞራል ከማባ ከንውጪ ጥቅም አይኖረውም።

የኦሮሞ ትግል ለረጅም ጊዜ ይሀንን አውነታ በመቃረን ወደፊት መራመድ ሳይችል ቀርቷል። በነበሩ አሰገዳጅ ምክንያቶች የኦሮሞ ትግል ድርጅት እና መሪዎቹ ከትግል ሜዳ ርቀው የሰው ሀገር ገብተዋል። ከትግል ሜዳ እንደወጡ ከመሪነት ወደ ደጋፊነት መሸጋገር ሲኖርባቸው አንርሱ ግን ከሀገር ውጪም ሆነው ራሳቸውን እንደ መሪ ማየት ቀጠሉ፡ ከዲያሰፖራውም መልምለው
ሹመት አከፋፈሉ። ይህ ሁኔታ ድርጅቱ እና አመራሩ ከትግሉ ሜዳ በመራቁ የተነሳ ተጨባጭ ሥራ መሥራት እንዳይችል ብቻ ሳይሆን፣ መሬት ላይ ተጨባጭ ሥራ መሥራት የሚችል ሌላ ድርጅት እና አመራር እንዳይበቅል እንቅፋት ሆኗል።

ስለሆነም ውጪ ያለን ሰዎች የሀገር ውስጡን ትግል እንመራለን ብለን ራሳችንን ዋሽተን በተጨባጭ የማይቻለው ላይ ከመድከም እና ሕዝቡንም በማይጨበጥ ተስፋ ከማዘናጋት፣ ሚናችን ከላይ በተገለጹት አምስት መንገዶች መርዳት እንደሆነ አውቀን ወደዚያው አተኮርን። ከአምስቱ መንገዶች ውስጥ የ"Oromo First' ቡድን ሚዲያ ማቋቋም ስለመረጠ በምትችችሉት አግዙን በማለት ሕዝቡን ጠየቅን። ሕዝቡም የእኛን መልዕክት በመቀበል በሚያስደንቅ ሁኔታ ረድቶን OMNን ማቋቋዎ ቻልን።

ብዙዎች የ"Oromo First" ዘመቻን ጽንፈኝነትን ወይም የመገንጠል ፖለቲካን የሚያበረታታ መስሏቸው ሲተቹን ነበር፡ ነገሩ ግን እንደዚያ አልነበረም። ከጅምሩም ኦሮሚያ ከኢትዮጵያ ተገንጥላ ነጻ ሀገር ትሁን የሚለውን ሐሳብ እንደማልደግፍ በኦሮሞ የፖለቲካ ጎራ በደንብ የሚታወቅ እና ስተችበት የነበረ አቋሜ ነው። የኦሮሞን ሕዝብ መብት እና ጥቅም በኢትዮጵያ ማዕቀፍ ውስጥ ማስከበር ይሻላል፤ ይቻላልም ብዬ እንደማምን ጽሑፎቼን እና ንግግሮቼን የተከታተለ ሁሉ ሊረዳው ይችላል። ለምሳሌ በ2010 Gadaa.com ለተሰኘ ድረ-ገጽ በሰጠሁት ረዘም ያለ ቃለመጠይቅ ላይ ለኦሮሞ ሕዝብ ዘላቂ ጥቅም ያለው፣ ኦሮሚያን ነጥሎ አዲስ ሀገር ከመመሥረት ይልቅ ያለችውን ኢትዮጵያ ወደ ዴሞክራሲ በማሸጋገር፣ የሁሉንም ሕዝቦች መብት እና ጥቅም የሚያስጠብቅ ሥርዓት መገንባት  እንደሆነ በግልጽ ተከራክሬያለሁ።23

ብዙ ሰው ያልተገነዘበው፣ "Oromo First" ከዚያ በፊት የኦሮሞ ትግል መሪ መፈክር የነበረውን "Oromia shall be free" የሚለውን መተካቱን ነው። “Oromia shall Be Free” ነጻ ሀገር መመሥረትን የሚያቀነቅን ቁርጥ ያለ አቋም ሲሆን፣ “Oromo First" ግን አንድ እርምጃ ወደ መሀል የተራመደ ነው። “"Oromo First" በቅድሚያ ኦሮሞ ነኝ ማለት ስለሆነ፣ ለተጨማሪ ማንነቶች በሩን ክፍት ያደረገ ነው። በሌላ አባባል ከ”oromia Shall be free" ወደ "Oromia First" የተደርገው ሽግግር፣ ኦሮሚያን ከመገንጠል ኦሮሞን ለሥልጣን ወደ ማብቃት (empowering oromo) የተደርገ ነበር። በoromo First ዘመቻ እናኋለም በቁሮ ትግል ወቅት ብሔርተኝነትን ያጋጋልን ስለነበር የኦሮሞን ፖሊቲካ ወደ ጽንፍ እንደወሰድነው ይተቹን ነበር። እውነታው ግን ወደ መሀል ነው ያመጣነው።

በወቅቱ ከ"Oromia Shall Free" ወደ "Oromo First” ሰለተደረገው ሽግግር በግልጽ ያልተነገረው አላስፈላጊ ተቃውሞ (backlash) እንዳይቀሰቀስ በመሥጋት ነበር። እንዲያዉም የትርክ ሽግግሩ እንዳይነቃብን የጋለ የብሄረተኝነት ንግግሮችን እና ምልክቶችን እንደሸፋን እንጠቀም ነበር።

እንዲሁም፣ ለረዥም ጊዜ የኦሮሞን ትግል ውስጥ የቆየውን “ነጻ ኦሮሚያን መመስረት ወይም ኢትዮጲያን ወደ ዴሞክራሲ ማሻጋገር" የሚለው ክርክር አንጀዳ እንዳይሆን በማድረግ ነበር። ሆኖም የ"Oromo First ዘመቻን ውይይት በጥንቃቄ የተከታተለ ሰው ስለሽግግሩ

23 Mohameed Jawar. “ I am quite optimistic about the Future of Ethiopia.” Gadaa. Com. 13 Mar. 2010

መገንዘብ ይችላል። በተለይ የማስተር ፕላኑ ተቃውሞ የተቀረጸበት ሁኔታ ይበልጥ ሽግግሩን ማሳያ ነው። በመጨረሻም ሥልጣን ለኦሮሞ እንዲሰጥ በይፋ ሰንጠይቅ የመገንጠል ትርክቱ ተዋጠ፡ ይህንንም ሀጫሉ «አራት ኪሎ ይገባሃል› በሚለው ሽለላ ደመደመው።

ይህ የኦሮሞን ፖለቲካ ትርክት24 ወደ መሀል የማምጣት ሥራ በእኛ ትውልድ የተጀመረ አይደለም። ኦሮሞ መብቱን የሚጎናጸፈው «ነጻ ኦሮሚያን በመመሥረት ወይስ ኢትዮጵያን በመጠገን ነው?› የሚለው ክርክር ገና ከትግሉ ውልደት አንስቶ የነበረ ነው። በ1960 በየመን ሀገር ኤደን ከተማ የተሰባሰቡት የትግሉ መስራቾች፣ በዚሁ ሐሳብ ተለያይተው በሐጂ ሁሴን ሱራ የሚመራው ቡድን በኢትዮጵያ ማዕቀፍ ውስጥ መታገል ይሻላል የሚለውን ሐሳብ ተከትለው "የኢትዮጵያ ብሔራዊ ነጻነት ግንባር" የተሰኘ ድርጅች ሲመሰርቱ፣ በኤሌሞ ቂልጡ እና ጃራ አባገዳ የተመራው ቡድን ደግሞ ነጻ ኦሮሚያን መመሥረት ይገባል በሚል የኦሮሞ ነጻነት ጦርን መሥርቶ የትጥቅ ትግል ጀመረ። ኦነግ በ1973 ሲመሰረት "የራሰን ዕድልበራሰ መወሰን/ self - determination" የሚለውን መርህ ሁለቱን ተጻራሪ ሐሳቦች እንደ ማሰታረቂያ ተጠቀመበት። ሆኖም የደርግ አፈና እየተባባሰ ሄዶ የኢትዮጵያ ፓለቲካበመካረሩ፣ ኦነግ በ1980ዎቹ ነጻ ኦሮሚያ መመሥረትን ሲያቀነቅን ነበር።

በ1990ዎቹ የኦነገ ምክትል ሊቀመንበር እና የድርጅቱ የሀሳብ መሪ (ideologue) ሌንጮ ለታ የኦሮሞ ትግል ዓላማ ኢትዮጵያን ወደ ዴሞክራሲ ማሸጋገር መሆን እንዳለበት በግልጽ በመጻፍ፡ የራስን ዕድል በራስ የመወሰን መንታ መንገድ እንዲያበቃለት ተማጸነ" ነገር ግን በድርጅቱ አመራር ውስጥ በነበረው ክፍፍል የተነሳ፣ በሐሳቡ ጠለቅ ያለ ውይይት ከማድረግ ይልቅ፣ የሌንጮንና የደጋፊዎቹን ብሔርተኝነት እና የትግል ተዓማኒነት ለማንቋሸሽ ሥራ ላይ ዋለ።

ቀጥሎ ሊንጮ ከድርጅቱ ሰለተባረረ፣ ኢትዮጵያን ዲሞክራታይዝ የማድረግ እሳቤ እንደ ነውር (taboo) ተቀጥሮ ሐሳቡን ማንሳት አራሱ የፓለቲካ ዋጋ የሚስሰከፍል ሆነ። ""ኢትዮጵያኒስት/ Ethiopianist ለሚል ፍረጃ መጋለጥ አንድን ሰው ከፓለቲካ ምህዳሩ ብቻ የሚገፋ ሳይሆን ለማኅበራዊ መገለል ወደሚዳርግ ደረጃ አደገ።

እኔም ይሄን ጉዳይ ከሲንጋፖር ሰከታተለው ቆይቼ፣ አሜሪካ ከሄድኩ በኋላ ኢትዮጵያን ወደ ዴሞክራሲ በማሸጋገር የኦሮሞን ሕዝብ መብት ማስከበር የሚለውን ሐሳብ ከነውርነት ለማላቀቅ መሞከርን ተያያዝኩት። እንደ ፕሮፌር መረራ ጉዲና እና ዶ/ር ነጋሶ ጊዳዳ ያሉ የዚህ ሀሳብ አራማጅ የነበሩ ሰዎች ላይ የሚደርገውን የማጥላላት ዘመቻ እቃወም ነበር። እንደ ፓልቶክ ባሉ የኢንተርነት ሚዲያዎች በመቅረብ፣ በሕገመንግሥቱ የተደነገገውን የራሰን ዕድል በራሰ የመወሰን መብት ተጠቅሞ የመጨረሻ ውሰኔ የሚሰጠው ሕዝቡ ቢሆንም፣ ከመገንጠል ይልቅ ኢትዮጵያን ወደ ዴሞክራሲ ማሸጋገር ይሻላል የሚል መከራከሪያ አቀረብ ነበር። በሂደት ግን ነጻ ኦሮሚያን መመሥረት ከጥቅሙ ጉዳቱ እንደሚበዛ በማስረዳት፣ የኦሮሞን መብትበኢትዮጵያ ማዕቀፍ ውስጥ ማስከበር የተሻለ፣ አንዲያውም ብቸኛው አማራጭ እንደሆነ

24 በዚህ መጽሃፍ ውስጥ ትርክት የሚለውን ቃል የምጠቀመው በአማርኛው ቀጥተኛ ትርጉም ሳይሆን የእንግሊዝኛውን narrative በማህበራዊ ሳይንሰ ውስጥ ያለውን ትርጓሜ ነው።

25 The Ethiopia State at the crossroads: Decolonization and Democratization or Disintegration red sea press, 1999

በጽሑፎቹ እና በንግግሮቹ ውስጥ መከራከር ጀመርኩ። በ“Oromo First" እና "Oromo protest" ወቅት ተሰሚነቴ በከፍተኛ ሁኔታ በማደጉ፣ እንዲሁም እኔ እና ባልደረቦቼ ሚዲያን በመጠቀም የኦሮሞን ፖለቲካ

ዲስኮርሰ በበላይነት መያዝ በመቻላችን፣ የመገንጠል ፖለቲካን ወደዳር በመግፋት፣ ኢትዮጵያን ወደ ዴሞክራሲ ማሸጋገር የትግሉ መሪ ትርክት ማድረግ ቻልን26።

ለረጅም ጊዜ በትግሉ ውስጥ የበላይነት የነበረውን የመገንጠል ትርክት በመጻረር፡ የኦሮሞን ጥያቄ በኢትዮጵያ ማዕቀፍ ውስጥ መፍታትን ስሰብክ፣ ዋና ዋና የኦሮሞ ብሔርተኀነት ትርክቶችን እና ምልክቶችን ስለምጠቀም፡ በብሔርተኝነቴ ላይ ሲነሱ የነበሩ ትችቶችን  መቋቋም አስቻለኝ።

ለምሳሌ የኦነግን ባንዲራ መጠቀሜ፣፡ መገንጠሏን ባልደግፍም ኦሮሚያን ማቀንቀኔ፣ አንዲሁም የመገንጠል ዓላማን ያነገቡ እንኳን ቢሆኑ ለቀድሞ አመራሮች እውቅና መስጠቴ፣ ከግለሰቦች አና ከአንጃዎች የሚሰነዘሩብኝ ነቀፌታዎች አየገነባሁት የነበረውን ቅቡልንት እንዳይጎዳ ረድቶኛል።

26 የብሔር ትግልን ዓላማ ከመገንጠል የመቀየር ፈተናን የተጋፈጠው የኦሮሞ ትግል ብቻ አልነበረም። መገንጠልን ግብ አድርጎ የተነሳው የሕወሓት ትርክት የትግራይን ጥያቄ በፌደራላዊ ኢትዮጵያ ውስጥ መመሊሰ ወደሚለው ለማሸጋገር ብዙ ጥረትን የጠየቀ ነበር። በ1980ቹ መጨረሻ በመለሰ ዜናዊ አመራርነት ሐሳቡ በግልጽ ሲወጣ ድርጅቱ ውስጥ ክፍፍልን አስከትሏል። ከዚያ ወዲህም በአመራሩ መካከል የአንጃ ክፍፍል በመጣ ቁጥር የመካሰሻ አጀንዳ ሆኖ ቀጥሏል። አኔም ይህን የትርክት ሽግግር ለማሳካት መለሰ ሲጠቀምባቸው የነበሩ ስልቶችን ማጥናቴ የኦሮሞን ፖለቲካ ትርክት ለማቃናት ረደቶኛል።

# 6.7.OMN

የኦሮሞ ታጋዮች የሚዲያን አስፈላጊነት የተረዱት ገና በማለዳው ነው። አንድን ሕዝብ ነፍጥ ከማስታጠቅ ይልቅ ንቃተ-ኅሊናውን ማሳደግ አስፈለጊ መሆኑን በመረዳት የትጥቅ ትግል ኮመጀመራቸው በፊት ሚዲያን ለማግኘት ሲተጉ ነበር። ዶ/ር ሙሐመድ ረሻድ አብዱሌ በ1950ዎቹ ግብጽ በሚገኘው አል-አዝኻር (Al-Azhar)ዩኒቨርሲቲ ሲማሩ የአፋን ኦሮሞ ሬዲዮ ለመክፈት የሀገሪቷን መንግሥት ፈቃድ ጠይቀው ከተፈቀደላቸው በኋላ በኢትዮጵያ መንግሥት ተቃውሞ ምክንያት ሳይሳካ ቀረ።

ሼኽ ሙሐመድ ረሻድም ተስፋ ሳይቆርጡ አፋን ኦሮሞን በሬዲዮ የማሰራጨት ውጥን በልባቸው ይዘው ገና ነጻ ወደወጣችው ሱማሊያ በማቅናት ከአዩብ አቡበከር ጋር በመሆን የአፋን ኦሮሞ ሬዲዮ ስርጭት ጀመሩ። ስርጭቱም መጀመሪያ ላይ በቀን ለአምስት ደቂቃ ብቻ ነበር። የሱማሊያ መንግሥት ዝግጅቱን የፈቀደው ከኢትዮጵያ መንግሥት ጋር ባለው ግጭት ለራሱ ጥቅም አስቦ እንጂ ለኦሮሞ ሕዝብ አዝኖ አልነበረም። የሱማሊያ መንግሥት ፕሮፓጋንዳውን ለኦሮሞ ማኅበረሰብ ለማድረስ ፍላጎት ቢኖረውም የኦሮሞ ብሔርተኝነት መጠናከር ለምኞቱ እንቅፋት እንደሚሆን ስለጠረጠረ፡ እነ ሼኽ ሙሐመድ ረሻድ እንደፈለጉት "የኦሮሞ ቋንቋ ከማለት ይልቅ የጋላ ቋንቋ" አንዲባል ወሰነ። እነ ሙሐመድ ረሻድ ቃሉ ውስጣቸውን ቢያሳምማቸውም የሬዲዮ ፕሮግራም መጀመሩ ከስሜታቸው የሚበልጥ ስለሆነ፣ መግቢያው ላይ የጋላ ቋንቋ እያሉ፣በዜና ውስጥ ግን አፋን ኦሮሞ የሚለውን በመጠቀም በ1962 ስርጭታቸውን ጀመሩ።

ይህ የሬዲዮ ፕሮግራም ተጀምሮ በጥቂት ጊዜያት ውስጥ ስርጭቱ በሚደርስባቸው እንደ ሐረርጌ፣ባሌ እና ቦረና ያሉ አካባቢዎች ብዙ አድማጭ ለማፍራት ቻለ። ሬዲዮ የሌላቸው ነዋሪዎች ሰፈር ውስጥ ሬዲዮ ያለው ሰው ጋር ተሰብስበው ያዳምጣሉ፤ በቦታው ተገኝተው በቀጥታ የሰሙት ላልተገኙት ጠቅለል አድርገው በመንገር ላልሰሙት ያዳርሱ ነበር።

ሚዲያ ሕዝብን ምን ያህል ለትግል እንደሚያዘጋጅ የምንመለከተው የሞቃዲሾ ሬዲዮ ተጀምሮ በጥቂት ጊዜ ውስጥ ስርጭቱ በሚደርስባቸው የኦሮሚያ አካባቢዎች ውስጥ አመጽ ፈንድቷል። በሐረርጌ የአፍረን ቀሎ የባሕል እና የቋንቋ ንቅናቄ፡ በባሌ ደግሞ የገበሬዎች የትጥቅ ትግል ተጀመረ።

የኃይለሥላሴ መንግሥት ካይሮ እንዳደረገው ሱማሊያን አስፈራርቶ የአፋን ኦሮሞ የሬዲዮ ስርጭት ማስቆም ሲያቅተው፡፣ይጠየፈው በነበረው ቋንቋ ሐረር ላይ የአፋን ኦሮሞ መሰናዶ አስጀመረ። ይህ ሁኔታ የሞቃዲሾን ስርጭት ሊያስቆመውም ሆነ ሊያቀዘቅዘው ስላልቻለ ጋዜጠኞቹን ወደ ማጥፋት ተሸጋገረ። በቀዳሚነት አዩብ አቡበከርን ገደለ። የግድያ እርምጃው እና በሱማሊያ የተከሰተው ፓለቲካዊ ለውጥ የሞቃዲሾን ሬዲዮ ቢያዳክመውም የሚዲያው ትግል የለኮሰው ችቦ በስፋት ተዳረሰ። ለዚህ ማሳያው የሞቃዲሾ ሬዲዮን ጫና ለመቋቋም የተከፈተው የሐረር ሬድዮ የኦሮሞ ብሔርተኝነትን በማነቃቃት መንግሥት ካሰበው ዓላማ

በተቃራኒ መሥራት ጀመረ። እንደ አዩብ አቡበከር እና የሸዋልዑል መንግሥቱ ያሉ ጋዜጠኞች በቀጥታ ስለፓለቲካ ባያወሩም፣ የኦሮሞን ባሕል እናሥነ-ጥበብ በማስተዋወቅ ብሔርተኝነቱን አቀጣጠሉት። አዩብ አቡበከር እና የሸዋልዑል መንግሥቱ በተለያየ ጊዜ ሕይወታቸው ተቀጠፈ።

የኃይለሥለሴ መንግሥት ወድቆ ደርግ ሲተካ የለውጡን ዕድል በመጠቀም እንደ ማህዲ ሃሚድ ሙዴ ያሉ ጋዜጠኞች የበሪሳ ጋዜጣ እና ሌሎችን በማቋቋም የሚዲያውን ትግል አስፍተው አስቀጠሉት። በወትቱ ምርጫቸው የሆነውን የላቲን ፊደል መጠቀም ቢከለክሉም፤ የአማርኛ ፊደል በመጠቀም ስለ ኦሮሞ ሕዝቡ ባሕል፣ ታሪክ እና መሻት በመጻፍ ንቃተ-ኅሊናውን የበለጠ አሳድገዋል።

በመቀጠል በ1980ዎቹ የኦነግ ልሳን በመሆን የተመሠረተው የኦሮሞ ነጻነት ድምፅ የታጋዮችን ገድል ለሕዝቡ በማብሰር እና የደርግንጥፋቶች በማጋለጥ ሕዝብ የማነቃቃቱን ሥራቀጠለበት። የኦሮሞ ነጻነት ድምፁን ለመቋቋም በማሰብ የደርግ መንግሥት ሐረር ከነበረው የሬዲዮ ስርጭት በተጨማሪ ፊንፊኔ ላይም ፕሮግራም ከፈተ። በዚህ ጣቢያ ውስጥ የነበሩ ጋዜጠኞች የደርግን ፕሮፓጋንዳ ቢያሰራጭም፤ ስለኦሮሞ ባሕል እና ቋንቋ በሚያቀርቧቸው ፕሮግራሞች ለብሔርተኝነቱ መነቃቃት ከፍተኛ አስተዋጽዖ አድርገዋል።

በ1983 ዓ.ም ኦሮሚያ እንደ ክልል በግልጽ ስትመሠረት እና አፋን ኦሮሞ የሥራ ቋንቋ ከሆነ በኋለ የአፋን ኦሮሞ የሬዲዮ ስርጭት ሰዓት ከመጨመሩ በተጨማሪ በቴሌቪዥንም መተላለፍ ጀመረ። በመንግሥት ሚዲያ የሚተላለፈው የአፋን ኦሮሞ ሰርጭት ሥልጣን ላይ ሆኖ ሕዝባችንን የሚዘርፈውን የፖለቲካ ቡድን አጀንዳ በማራመድ ከኦሮሞ ትግል በተቃራኒ ቢሰራም፣ በቋንቋው የሚተላለፈው ዝግጅት መስፋቱ እና የስርጭት ሰአት መጨመሩ በባሕል እና በቋንቋ ረገድ የሚደረገውን ትግል አጠናክሮታል። ከእልህ አስጨሪሽ ትግል በኋላ የአሜሪካ ድምፅ ሬዲዮ (Voice of America) በአፋን ኦሮሞ ስርጭት መጀመሩ ቋንቋው ዓለም አቀፋዊ ይዘት እንዲኖረው አስቻለ። በተጨማሪም የኦነግ አባላት የነበሩ ጋዜጠኞች
በኤርትራ ሬዲዮ እና ቴሌቪዥን የአፋን ኦሮሞ ዝግጅቶችን በማቅረብ፣ እንዲሁም በዲያሰፖራ እንደ ሚኒሶታ እና ሜልቦርን ካሉ ከተሞች የሚተለለፉ የማኅበረሰብ ሬዲዮ ፕሮግራሞች በሀገር ውስጥ ሚዲያዎች እንዳይዘግቡ የተከለከሉ የተለያዩ ጉዳዮችን በማቅረብ ትልቅ ሚና ተጫዉተዋል።

የኦሮሞን ትግል በሚዲያ በኩል ለማጠናከር በጎረቤት ሀገራት እና በሀገር ውስጥ ሲደረግ የነበረው ጉዞ ውሎ አድሮ በምዕራባውያን ሀገራት ለተቋቋሙ የኦሮሞ ሚዲያዎች ውልደት መሠረት ጣለ። በውጪ ያለው የኦሮሞ ሚዲያ ይበልጥ መስፋፋት የጀመረው ከኢንተርኔት መምጣት ጋር ተያይዞ ነው። በተለይ ፓልቶክ (paltalk) የተባለው የድረ-ገጽ መድረክ (plat form) ውጪ ያለው የኦሮሞ ማኅበረሰብ መረጃ እንዲለዋወጥ እና ለኦሮሞ ትግል ድጋፉን እንዲያጠናክር ጉልህ ሚና ተጫውቷል። ይሁን እንጂ ፓልቶክ ጥቅሞች እንዳሉት ሁሉ የኦነግ አንጃዎችን ሽኩቻ በማባባስ ረገድ ጉዳትም ነበረው። ከፓልቶክ ቀጥሎ ፌስቡክ መጣና ኦሮሞ ለራሱም ሆነ ለሌሎች መረጃ የማድረስ ዕድሉን የበለጠ እንዲያሰፋ አስቻለው።

OMNን ያቋቋምን ሰዎች ቀደም ብለን እንደ ፓልቶክ እና ፌሰቡክ ባሉ የማህበራዊ ሚዲያዎች ገና ከጅምሩ ስንሳተፍ ስለነበረ የኢንተርኔት መስፋፋት ይዞ የመጣውን ፋይዳ በጠዋቱ ለመረዳት ችለናል። ፌሰቡክ በ2004 ተመስርቶ በአንድ ዓመት ውስጥ መቀላቀሌን አስታውሳለሁ።

ከኢንተርኔት በፊት መረጃን ማሰባሱበም ሆነ በጋዜጣ፣ በሬዲዮ እና በቴሌቪዥን ማሰራጨት ብዙ ገንዘብ ብሉም የመንግሥትን ፈቃድ ሰለሚጠይቅ፣ ሚዲያ ሥልጣን እና ሀብት ባካበቱቡድኖች እጅ ነበር። የኢንተርኔት ቴክኖሎጂ መሰፋፋት የመረጃ ልውውጥን ፍጥነት በከፍተኛ ሁኔታ ሲጨምር፣ ክፍያውን አሳንሰና የመረጃ ልውውጥን ምሥጢራዊነት አሻሽሎ ለጭቁን ሕዝቦች አመቺ ሁኔታን ፈጠረ። ይህንን ተረድተን ፓልቶክን በኋላም ፌሰቡክን ለትግላችን አላማ በሚገባ ተጠቀምንበት። ምናልባትም ከአረብ ሀገራት ንቅናቄ ቀጥሎ ፌሰቡክን በሚገባበመጠቀም ለውጥ ያመጣው የቄሮ ትግል ነው ቢባል ማጋነን አይሆንም።

ኢንተርኔት እየተሰፋፋ መሄዱ የኦሮሞ ትግልን የሚዲያ ሽፋን አያሰፋ ቢመጣም በጥንቃቄ እና በጥበብ ካልተመራ ከጥቅሙ ጉዳቱ እንደሚያመዝን ከፓልቶክ ልምዳችን ሰለተረዳን ፌስቡክ ላይ የእርምት አርምጃ ወሰድናል። በፌሰቡክ ላይ መረጃ በማጋራት የሚታወቁ ዋና ዋና ሰዎችን በቡድን በማደራጅት፣ መረጃን በዝግ በመለዋወጥ እና በመወያየት የማኅበራዊ ሚዲያውን አጀንዳ አቅጣጫ ማስያዝ ቻልን። በዚሀ መልኩ በሚዲያ በኩል ከመንግሥት ጋር በነበረው ግብግብ በአጭር ጊዜ የበላይነቱን ተቆጣጠርን። ስናስበው እና ስንዘጋጅበት የነበረው የሰላማዊ ትግል ሰልትም ሚዲያን በብቃት መጠቀምን ሰለሚጠይቅ፡ ከ2005-2012 በማኅበራዊ ሚዲያ ቆይታችን ጥሩ ልምድ እና ብቃት አካብተናል። በማኅበራዊ ሚዲያ ካካበትነው ልምድ በመነሳት፣ የራሳችን የሚዲያ ስርጭት ሲኖረን በብቃት በመምራት ትግሉን መጥቀም እንደምንችል በራሳችን ተማመንን። ማኅበራዊ ሚዲያን በአግባቡ ከመጠቀም በተጨማሪ ለሰፊው ሕዝብ ተደራሽነት ያለው ሁነኛ የሚዲያ ተቋም አሰፈላጊነት ላይ ጥርጥር አልነበረንም። ከዚህ በመነሳት ጠንካራ ሚዲያ ማቋቋም በምንችልበት ሁኔታ ላይ በርካታ ውይይት ስናደርግ ቆይተናል። ሆኖም ግን ሚዲያ ለማቋቋም እና ለመምራት የሚያሰፈልገንን ገንዘብ ማግኝት ባለመቻላችን ባሰብነው ፍጥነት መራመድ አልቻልንም።

የ"oromo First" ክሰተት ይህን የገንዘብ ችግር የምንፈታበትን ዕድል እንድናገኝ በሩን ሲከፍትልን፣ ከዘመቻው ጎን ለጎን ሚዲያ ለመመሥረት ሦስት ኮሚቴዎችን አቋቋምን። የመጀመሪያው ዋና አሰተባባሪ ኮሚቴ የሚባል ሲሆን የ"oromo First" ንቅናቄን እያሰተባበረ ሚዲያ ለማቋቋም የሚያሰፈልገውን ገንዘብ የማሰባሰብ ኃላፊነት ተጥሎበታል። ሁለተኛው የሚዲያ ኮሚቴ ሲሆን ኃላፊነቱ ለሚዲያ ፕሮግራም ዝግጅት እና ሰርጭት የሚያሰፈልገውን ሁለንተናዊ እቅድ እና ይዘት ያዘጋጃል። በሦስተኛነት የቴክኒክ ኮሚቴው ሰቱዲዮ መገንባት፣ ድረ-ገጽ መሥራት፣ ሳተላይት ላይ ማሰተላለፍ እንዴት እንደሚቻል እና የመሳሰሉት ላይ ጥናት በማካሄድ ያቀርባል። በሦስቱ ኮሚቴ ውስጥ የነበሩ አባላት እና የዘርፍ ክፍፍሉ የሚከተለውን ይመሰላል።

**የዋና አስተባባሪ ኮሚቴ አባላት፡-**

1. ዶ/ር ስንታየሁ በዳኔ

2.ኤሊያስ ኢብሳ

3.ግርማ ታደሰ

4.አርፋሴ ገመዳ

5.በድሪ አብዶ

6. ሌይላ አባዋሪ

7. ሙሀመድ አብዶሽ

8.*ጌዲራ ዲንቃ*
9.*ሙራድ ደሚና*
10.*ጃዋር መሀመድ*
***የሚዲያ ኮሚቴ፡-***
1. *ሙሀመድ አደሞ*
2.*ዶ/ር ሰለሞን ኡንጋሼ*
3. *አብዲ ፊጤ*
4.*ትእግስት ገሜ*
***የቴክኒክ ኮሚቴ፡-***
1. *ሚጃ ጭሪ*
2. *ሙሳ ዳውድ*
3. *ቂጤሶ ጭሪ*

እኔ በበኩሌ በዋና አሰተባበሪ ኮሚቴ ውሰጥ ከመሳተፍ አንዲሁም ለ 'oromo First' ዘመቻ በየከተሞቹ ከመዞር በተጨማሪ ሦስቱንም ኮሚቴዎች የማቀናጀት ኃላፊነት ወሰድኩ። እንቅሰቃሴ ስንጀምር ከቦታ ቦታ የመጓጓዣ ገንዘብ እንኳን አልነበረንም። ለዘመቻው የምናገኘውን ለመቆጠብ ሰንል እስከ ሀያ ሰዓት የሚወሰደውን ረጅም እና አድካሚ መንገድ ከአሕመድ ያሲን ጋር በመኪና አንጓዛለን። አሕመድ ያሲን የካሜራ ባለሙያ ሲሆን እንደ ሾፌር በማገልገል ይዞኝ ከቦታ ቦታ ይንቀሳቀሳል። ዝግጅት ያለበት ከተማ ከደረሰን በኋላ እኔ ንግግርሳደርግ እሱ ይቀርፃል፤ ማታ ላይ የተቀረጸውን ኢዲት አድርገን እናሰራጫለን። ከዚያም ያለምንም ዕረፍት በሌሊት ተነሰተን ወደሚቀጥለው ከተማ ጉዟችንን እንቀጥላለን።

እቅዳችን ዘመቻውን ጀምረን በሰድስት ወር ውስጥ፣ ማለትም ጃንዋሪ 1 ቀን 2014 ሚዲያውን ሥራ ማስጀመር ነበር። ገንዘብ በማሰባሰቡ ረገድ ጥሩ ስኬት ቢገኝም፤ በተጨባጭ ሚዲያ ማቋቋም ላይ የተጠበቀውን ያህል በፍጥነት መራመድ አልተቻለም። በሂደትም ቃል በገባነው ቀን ሥራችንን መጀመር እንደማንችል ግልጽ አየሆነ ሲመጣ አንዳንድ ሰዎች ቃል የገባነውን ሚዲያ የማቋቋም ዓላማ ማሳካት ሰለመቻለችን መጠራጠር ጀመሩ።

ሕዝብ ፊት ቆሞ ቃል እንደገባ አና ገንዘብ አንዳሰባሰበ ሰው ባሰቀመጥነው አቅድ መሠረት መራመድ አለመቻላችን ከፍተኛ ጭንቀት ውስጥ ከተተኝ። ለ"oromo First" ዘመቻ ወደ አንግሊዟ ብራይተን ከተማ ስንሄድ የኦነግ አንጋፋ መሪዎች ከሆኑት አቶ ገላሳ ዲልቦ እና ጠሀ አብዲ ጋር ተገናኘን። ምሽት ላይ ስናወራ ሚዲያ ለማቋቋም የገባነው ቃል ለሕዝቡ ከፍተኛ ተስፋ ሰለሰጠው መሳካት ካልቻለ ትልቅ የሞራል ኪሳራ አንደሚያመጣ አሳሰበው ጠንክረን ከዳር እንድናደርሰው ተማጽኗቸውን አቀረቡ። ንግግራቸው አሰቀድሜ ተወጥሬበት የነበረውን ጭንቀት የበለጠ አባባሰው።

ወቅቱ የ2013 ዲሴምበር ወር መጨረሻ ነበር። ከእንግሊዝ ጉዞ አንደተመለስኩ ሶስቱን ኮሚቴዎች የጋራ ሰብሰባ ጠርቼ ውይይት አደረግን። ሥራው መጓተቱ ላይ በሁላችንም መግባባት ላይ ተደረሰ። ቀደም ብለን አንዳቀድነው ጥር አንድ መጀመር አንደማንችል በማመን በሁለት ወር አራዝመን ማርች 1 ቀን 2014 ለመጀመር በቁርጠኝነት ወሰንን። ይህን እቅድ እውን ለማድረግ አንድ ሰው በኃላፊነት ሚኒሶታ ሄዶ ሙሉ ጊዜውን ሰውቶ ሰቱዲዮ መከራየት፣ አስፈላጊ የሚዲያ እቃ መግዛት አና ጋዜጠኞችን ተቀጥሮ ዝግጅት ማድረግ አንደሚያስፈልግ ተስማማን። ማን ይሂድ በሚለው ላይ ግን ኃለፊነት የሚወስድ ሰለጠፋ አሄዳለሁ ብዩ እራሴን አጨሁ። ሌሎች አባላት በተለያዩ ምክንያቶች መሄዴን ተቃወሙ።

አንዳንዶቹ ትምህርት ትቼ መሄዴን አልፈለጉም፡ የተቀሩት ከአኔ ጋር ተያይዞ ባለው ውዝግብ የተነሳ ሚኒሶታ ሄጄ በግልጽ መምራቴ የሚዲያውን ነጻነት ጥያቄ ውስጥ ይከተዋል የሚል ሥጋት

አደረባቸው። «ሌላ የሚሄድ ሰው ከሌለ እኔ የግድ መሄድ አለብኝ። ሕዝቡ ፊት ቆሜ ሚዲያ ለማቋቋም ገንዘብ የሰበሰብኩት እና ቃል የገባሁት እኔ እንደመሆኔ፣ ይህ ሚዲያ ካልተቋቋመ ከሁሉም በላይ የምዋረደውና ተጠያቂ የምሆነው እኔ ነኝ። ስለዚህ ትምህርቴን በጊዜያዊነት አቋርጬ ወደ ሚኒሶታ በመሄድ በሦስት ወር ውስጥ ሚዲያውን አቋቁሜ ለሚቀጠረው አዲስ አመራር ማስረከብ አፈልጋለሁ>> በማለት ሐሳብ አቀረብኩ። ስብሰባውን ሲመራ የነበረው ዶ/ር ስንታየሁ በዳኔ <ጃዋር ሚኒሶታ መሄድ አለበት ወይስ የለበትም?> በሚለው ላይ ድምፅ እንዲሰጥ አድርጎ በአብላጫ ድምፅ እንድሄድ ተወሰነ።

በወቅቱ የዶክትሬት (phD) ትምሀርቴን አየተከታተልኩ ጎን ለጎን ለ"oromo First" ዘመቻ በተለያዩ ከተሞች እንቀሳቀስ ነበር። ትምህርቴን አቋርጬ ሚዲያ ማቋቋም እንደምፈልግ ከአማካሪዎቼ አንዱ ለሆነው ለፕሮፌሰር ማሀሙድ ማምዳኒ ሰነግረው በጣም አዘነ። «ያገኘኸውን ትልቅ ዕድል አታባክነው፣ ትምህርትህን ከጨረሰክ በኋላ ለሚዲያውም ሆነ ለፖለቲካው ትደርሳለህ› ሲል ደጋግሞ መከረ እኔ ግን «ቃል የገባሁትን ዳር ካላደረሰኩ ለሕዝቤ ከባድ የሞራል ውድቀት፣ ለእኔም ውርደት ነው> በማለት ትምህርት ለማቋረጥ መወሰኔን ነገርኩት። ውሳኔዬ ጠንካራ መሆኑን ስለተረዳ ለአንድ ሴሚስተር ብቻ እንደማቆም ቃል ገብቼለት ትምሀርት ቤቱን አሰፈቀደልኝ።

በዚሁ መሠረት እ.አ.አ. ጃንዋሪ 3 ቀን 2014 ሚኒሶታ በመሄድ OMNን የማቋቋም እና ወደ ዕርጭት የማሰገባት ሥራን ማፋጠን ጀመርኩ። በጥቂት ቀናት ውሰጥ ለስቱዲዮ የሚሆን በታ አግኝተን ተከራየን። በነገራችን ላይ ከላይ ከተዘረዘሩት የኮሚቴ አባላት ውሰጥ የቴሌቪዥን ጣቢያ እንዴት እንደሚሰራ ወይም አሰፈላጊውን ግብዓት በዝርዝር የሚያውቅ አልነበረም። የቴሌቪዥን ሰቱዲዮ ምን አንደሚመስል ገብቶ የተመለከተ እንኳን ከቁጥርአይገባም።በበኩሌ ለጥቂት ጊዜያት አልጀዚራ እና ሌሎች ዓለም አቀፍ ጣቢያዎች ለቃለ-መጠይቅ በሄድኩበት ጊዜ ከተመለከትኩት ውጪ የማውቀው ነገር አልነበረም። ከእኛ መካከል ትንሽ የሚሻለው አሕመድ ያሲን ነው። አንድ የሚኒሶታ ቲቪ ሰቱዲዮ ውሰጥ <Oromo Tv>የተሰኘ ሰርጭት ያስተላልፍ ስለነበረ የሚያሰፈልጉ እቃዎችን በመጠኑም ቢሆን ያውቃል።

ከመነሻው ልምድ እና እውቀት ማጣታችን ተሰፋ አላሰቆረጠንም። ካለን መረጃ በተጨማሪ በማጥናት፣ የቀረውን የቴሌቪዥን ስቱዲዮ በመሄድ እየጠየቅን ሥራችንን ቀጠልን፤ የሚያሰፈልጉትን እቃዎች ከሥር ከሥር ገዛን። ከጥቂት ሳምንታት በኋላ አብዲ ፊጤ ከዋሽንግተን ዲሲ ወደ ሚኒሶታ መጥቶ ተቀላቀለን። የ"oromo First" ዘመቻ ለማድረግ ሳውዝ ዳኮታ በሄድኩበት አጋጣሚ ኡስማን ኡኩሜ የሚባል ልጅ ጠንካራ ጥያቄዎችን ዕለጠየቀኝ ፣ ጋዜጠኛ እንደሆነ ስጠይቀው ልምድ እንደሌለው ነገር ግን ሚዲያ ላይ የመሥራት ፍላጎት እንዳለው ስለነገረኝ፤ ጠራሁትና ወደ ሚዲያ ቡድኑ ቀላቀልኩት። በተጨማሪም ለሊሴ እንዳለ እና አለማየሁ ቀና የሚባሉ ጋዜጠኞች ሀገር ቤት ኦሮሚያ ቴሌቪዥን ውስጥ ልምድ ስለነበራቸው እነርሱንም ቀጠርናቸው።

ፊት ለፊታችን ተደቅኖ የነበረው ትልቁ ችግር የቴሌቪዥን መሰናዶ እና ይዘት አንዴት እንደሚዘጋጅ እና አንደሚመራ አለማወቃችን ነበር። ባለሙያ በመፈለግ ላይ ሳለን ሀገር ውሰጥ የኦሮሚያ ቲቪ ከፍተኛ ዳይሬክተር ሆኖ ሲያገለግል የነበረው ዶ/ር ብርሃኑ ዲርባባ አውስትራሊያ እየተማረ አገኘነው። ሊያግዘን ፈቃደኛ ሆኖ በአጭር ጊዜ ውሰጥ የሚዲያ

ፓሊሲ እና የተለያዩ መመሪያዎች አዘጋጀልን፣ በተጨማሪም ያገኘናቸውን ጋዜጠኞች ካለበት ሆኖ በኢንተርኔት ማሰልጠን ጀመረ። OMNን ለማቋቋም የተዋቀረው ኮሚቴ የሚዲያ መዋቅር እና የመተዳደሪያ ደንቦችን በማሰናዳት አዲስ ለሚቋቋም አመራር ለማሰረከብ ዝግጅቱን አጠናከረ። በዚሁ መሠረት ድርጅቱ የአሥተዳደር ቦርድ እና የሥራ አስፈፃሚ ኮሚቴ በተሰኘ ሁለት የአሥተዳደር መዋቅር እንዲተዳደር ተወሰነ። ቦርዱ አሥራ አምስት፣ የሥራ አሰፈፃሚ ኮሚቴው ዘጠኝ አባላት እንዲኖሯቸው ከሰምምነት ተደረሰ።

ቦርዱን ለማዋቀር የመሥራች ኮሚቴ ውስጥ ያለን አባላት እያንዳንዳችን አምስት ሰው እንድንጠቁም ዕድል ተሰጠን። ጥቆማው ከተሰበሰበ በኋላ ሰማቸው በተጠቀሱች ዕዎች ላይ እየተወያየንና ቆይቶም ድምፅ አየሰጠን አሥራ አምስት ሰዎች ላይ ተሰማማን ። 15ቱ የOMN የመጀመሪያ የቦርድ አባላት ከታች የተዘረዘሩት ነበሩ።

| *ስም* | *የትውልድ ቦታ* | *የመኖሪያ ቦታ* | *ሙያ* | *የስራ ድርሻ* |
|---|---|---|---|---|
| ዶ/ር ሀምዛ አብዱራዛቅ | ሀረርጌ | ቦስተን | የፋይናንስ ፕሮፌሰር | ሊቀመንበር |
| ኪታባ መገርሳ | ሸዋ | ቶሮንቶ | አካውንታት | ጸሐፊ |
| ፕሮፌሰር መሀመድ ሀሰን | ሀረርጌ | አትላንታ | የታሪክ ፕሮፌሰር | አባል |
| ዶ/ር አስፋው በየነ | ወለጋ | ሳን ዲዮጎ | የኢንጂነሪንግ ፕሮፌሰር | አባል |
| ዶ/ር አህመድ ገልቼ | ባሌ | ቨን ኩቨር | የአካባቢ ባዮሎጂስት | አባል |
| ዶ/ር ደምሰው ኢጃራ | ሸዋ | ኮኔክቲከት | የአካውንቲንግ ፕሮፌሰር | አባል |
| ወ/ሮ ኤርትሪያ ነመራ | ወለጋ | ሚኒሶታ | የማህበረሰብ አደራጅ | አባል |
| ዶ/ር ተክለአብ ሽብሩ | ቦረና | ቺካጎ | የጂኦማቲክስ ፕሮፌሰር | አባል |
| መይሙና ሁሴን | ቦረና/ገሪ | ሎስ አንጀለስ | የስደተኞች አስተባባሪ | አባል |
| አብዱልሰመድ ኡመር | ሀረርጌ | ዳላስ | ኢንጂነር | አባል |
| በድሪ መሀመድ | ሀረርጌ | ኤድመንተን | መምህር | አባል |
| ሌንጮ አባ ገሮ | ጅማ | ለንደን | የማህበረሰብ ሊቀመንበር | አባል |
| አበራ ተፈራ | ወለጋ | ዋሽንግተን ዲሲ | የማህበረሰብ አስተባባሪ | አባል |
| ኢሳ ኡሎ | አርሲ | ሲያትል | የአየር መንገድ ስራ አስፈጻሚ | አባል |
| አቢ ኢቲቻ | ወለጋ | ሚኒያፖሊስ | አካውንታንት | አባል |

የተመረጡት የቦርድ አባላት ባካሄዱት የመጀመሪያ ስብሰባ የተዘጋጀውን መተዳደሪያ ደንብ ረቂቅ አጽድቀው አመራር መርጠው ሥራቸውን ጀመሩ። የመጀመሪያዎቹ የOMN ሥራ አሰፈፃሚ ኮሚቴ አባላት የሚከተሉት ነበሩ።

| ስም | የትውልድ ቦታ | ሙያ | የስራ ድርሻ |
|---|---|---|---|
| ግርማ ታደሰ | ፊንፊኔ(አዲስ አበባ) | አይቲ ኢንጂነር | ከፍተኛ ዳይሬክተር |
| መሀመድ አብዶሽ | ሀረርጌ | አይቲ ኢንጂነር | ምክትል ዳይሬክተር |
| ሌይላ አባ ኖሪ | ጅማ | የሰው ሀይል ባለሙያ | ጸሀፊ |
| ዶ/ር ብርሀኑ ዲርባባ | ሸዋ | የሚዲያ አስፈጻሚ | ዋና አዘጋጅ |
| ዶ/ር ስንታየሁ በዳኔ | ሀረርጌ | የጤና ባለሙያ | የሀብት ማሰባሰብ |
| ራሚ መሀመድ | ፊንፊኔ(አዲስ አበባ) | ቢዝነስ ማኔጅመንት | ፍይናንስ |
| ሚሻ ጭሪ | አርሲ | አይቲ ኢንጂነር | አይቲ |
| ዶ/ር ሄኖክ ገቢሳ | ወለጋ | ህግ | የህግ ጉዳዮች |
| ሙራድ ደሚና | ሀርጌሳ(ሶማሊያ) | ቢዝነስ | ማርኬቲንግ |

ከእነዚሀ ውስጥ ለዋና አዘጋጅ ከሚከፈል የተወሰነ ደሞዝ ውጪ የተቀሩት ሁሉም በነጻ ሲያገለግሉ ነበር። የተቀሩት የመሥራች ኮሚቴ አባላት በተለያየ ዲፓርትመንት ሥር ተመድበው ሥራቸውን ቀጠሉ።

የተወሰኑት በቃን ብለው ወደ መደበኛ ኑሯቸው ተመለሱ። በቦርዱም ሆነ በሥራ አሰፈፃሚ ኮሚቴ የአካባቢ፣ የሀይማኖት እና የፖለቲካ አመለካከት ብዝሕነት ሚዛናዊ በሆነ መለኩ ማመጣጠን ለሚዲያው ቀጣይነት ወሳኝ መሆኑ በሁላችንም የታመነበት ጉዳይ ነበር። የአካባቢ እና የሀይማኖት መስፈርትን ለማሟላት ብለን እስከዚያች ዕለት ድረስ በሚዲያ ማቋቋም ፕሮጀክት ውሰጥ ያልተሳተፉ ሰዎችን ወደ ቦርድ ለማስገባት ወሰንን። ሲቃወሙን እና እንቅፋት ሲሆኑብን የነበሩ ሰዎችን ማካተታችን በጣም ሲረዱን የነበሩ እና ቦርድ ውሰጥ የመግባት ፍላጎት የነበራቸውን አስቀየመ። በኦሮሞ አና በኦሮሚያ ስም የተቋቋመ ድርጅት አመራሩም የኦሮሞ እና የኦሮሚያን ብዝኀነት ማንጸባረቅ አለበት ብለን ስለምናምን የሚደግፉንን ሰዎች ብናስቀይምም በአቋማችን ጸንተን ቀጠልንበት።

አመራሩ ብቻ ሳይሆን ጋዜጠኛቹም ብዝኀነትን የሚያንጸባርቅ እንዲሆን ሞክረናል። በወቅቱ ያሉት የአፋን ኦሮሞ ጋዜጠኞች ጥቂት ነበሩ፣ ከእነዚሀ ውሰጥ በውጪ ሀገር የሚኖሩት በጣት ይቆጠራሉ። በጋዜጠኞች ምልመላ ወቅት ሌላው ያተኮርንበት ጉዳይ የቋንቋ ዘዬ (dialect) ስብጥር ነበር። ሁሉም ኦሮሞ በአፋን ኦሮሞ የሚግባባ ቢሆንም ቋንቋው የተለያየ የንግግር ዘዮ ሰላሉት ጋዜጠኞች፣ አቅራቢዎች እና እንግዶቻችን በተቻለ መጠን ይሀንን የዘዮ ብዝሐነት ማንፀባረቅ አንዲችሉ ከተለያየ ቦታ የመጡ ባለሙያዎችን ፈልገን ወደ ሥራ አሰማራን። መጀመሪያ ላይ ባይሳካልንም ሚዲያው ተከፍቶ በአጭር ጊዜ ውስጥ ከዲሮ ኤሌሞን ከቦረና፣ በፍቃዱ ሞረዳን ከኢሉ አባቦር፣ ደመቀ ነጋሳን ከሸዋ እንዲቀላቀሉ በማድረግ አድማሳችንን እያዕፋን ሄድን። ጋዜጠኛ ስናጣ ራሳችን እናሰለጥናለን። ዶ/ር ብርሃኑ ብዙ ጊዜ «አፋን ኦሮሞ ማንበብ እና መጻፍ የሚችል ብለህ ማሰታወቂያ አውጣ፣ ዲግሪ አና ልምዱን ተወው>> ይለኛል። OMN (omn) ውሰጥ ሌላው ለማንጸባረቅ የፈለግነው የሀይማኖት ብዝኀነት ነበር። አንድ ቀን አዲሰ ለማሰልጠን ከመለመልናቸው ልጆች ውሰጥ አንዷ ሂጃብ አድርጋ ሰለነበር፣ አንዱ

ጋዜጠኛ በጨዋታ መሀል «ከተቀጠርሽ ሂጃቡን ታወልቂያለሽ ወይ?» በማለት ይጠይቃታል። «ለምንድነው የማወልቀው?» ሰትለው «ሂጃብ ተለብሶ ቴሌቪዥን ላይ ዜና አይነበብም› አላት።

ልጅቷ ጉዳዩ እንግዳ ስለሆነባት መጥታ ጠየቀችን። ለእኔም አንግዳ ሰለነበር፣ ሳጠያይቅ በወቅቱ በኢትዮጵያ ሴት ሂጃብ አድርጋ በቴሌቪዥን ዝግጅት ስታቀርብ አንደማትታይ ሰማሁ። አንድ ሴት ሂጃብ ለብሳ ዜና ማቅረቧ በፕሮግራሞች ላይ የሚፈጥረውን ተጽዕኖ በተመለከተ ምንም አሳማኝ ምክንያት ሰላልሰማሁ፣ ሂጃብ ለባሽ ፈልገን በማሰልጠን ዜና እንድታነብ አደረግን።

ሂጃብ ለባሽ ሴት የመጀመሪያ ቀን ዜና እንዳነበበች ከፍተኛ የስም ማጥፋት ዘመቻ ተጀመረ። "የአረብ ሚዲያ ነው"፣ "አካሄዳቸው ኦሮሞን እሰላም ለማድረግ ነው። "ኦሮሞ ሚዲያ ኔትዎርክ ሳይሆን ሙስሊም ሚዲያ ኔትዎርክ መባል አለበት"፣ እና የመሳሰሉ ፍረጃዎች ቢደርሱብኝም እኛ ግን በውሳኔያችን ጸናን። ለእኛ የታያን ከሚመመለከተን ማኅበረሰብ ውስጥ ብዙ ሂጃብ የሚያደርግ መኖሩ ነው። ይህ ማኅበረሰብ ደግሞ በOMN መስኮት የራሱን ነፀብራቅ ማየት ይገባዋል። ከሙስሊም ቤተሰብ የተወለደች አንዲት ሕፃን ልጅ በOMN መስኮት ሂጃብ ያደረገች ጋዜጠኛ ሰትመለከት እኔም ነገ እዚያ መድረሰ እችላለሁ፣ ብላ በራስ መተማመን እና ተሰፋ አንድትሰንቅ ያደርጋታል። ይህ የሕዝባችንን የሰው ኃይል አቅም ለማጎልበትና የጋራ ጥንካሬን ለማሳደግ ወሳኝ ነው ብለን አምነን በጽናት ሄደንበት። ብዙም ሳይቆይ የእኛን ፈር ቀዳጅነት በመከተል፣ ውድድር በሚመስል መልኩ በሀገሪቷ ቴሌቪዥኖች ሂጃብ የምታደርግ ሴት ዜና ስታነብ መመልከት አየተለመደ መጣ።

አሥተዳደራዊ መዋቅር ዘርግተን አመራር ከመደብን በኋላ ባቀድነው ቀን ስርጭት ለማሰጀመር ዝግጅታችንን አጧጧፍነው። ሚኒሶታ ማሰባሰብ ከቻልናቸው ጋዜጠኞች እና ባለሙያዎች በተጨማሪ ሩቅያሉ አጋሮችምበቻሉት ሁሉ ተባበሩ። ለምሳሌየካሜራባለሙያው ግርማ ገመዳ ከቶሮንቶ ዓርማ (ሎጎ) እና ለዝግጅት የሚሆን የመግቢያ ቪድየ ሰርቶ ላከልን። ቪድዮ ቀርፆ፣ አርትዖት ሰርቶ ማዘጋጀት ረጅም ሰዓት አንደሚወሰድ ስለማናውቅ መጀመሪያ ላይ የነበረን የቪድዮ አዘጋጅ አሕመድ ያሲን ብቻ ነበር። ነገሩ ሲገባን አሰቀድሜ ቺካጎ የማውቀውን ፉአድ ሲራጅን አግኝቼ 'ቶሎ ድረስልኝ' ስለው የዚያኑ ቀን የሚሰራውን ሥራ በመተው ተቀላቀለን። ፉአድ "Youtube" ባልነበረበት ዘመን ኢንተርኔት ላይ "Oromo First" የሚባል ድረ-ገጽ ከፍቶ፣ ሕዝቡ የአፋን ኦሮሞ ዘፈን አንዲያዳምጥና የጥበብ ሥራዎች አንዲያድጉ ያደርግ ነበር። በሂደትም የሬዲዮ ፕሮግራም ጨምሮ ከፈተ፤ ለመጀመሪያ ጊዜ የሬዲዮ ቃለ-ምልልሰ ያደረኩትም ከእርሱ ጋር ነው።

ቅድመ ዝግጅታችንን በዚህ ሁኔታ ጨርሰን ሰርጭት የምንጀምርበት ቀን እየተቃረበ መጣ። ማርች 1ቀን 2014 ስርጭት ለማስጀመር በሙሉ የራስ መተማመን ለሕዝብ አውጀንና አዳራሽ ተከራይተን ከሚኒሶታ እና ከተለያዩ የአሜሪካ ክፍሎች ሰው ጠርተናል። አንድ ወር አሰቀድመን የምርቃቱን ቀን ስናሳውቅ ቀኑን መወሰኑ ጫና ፈጥሮብን እንድንሰራ ያነሳሳናል በሚል እምነት እንጂ ሁሉም ነገር አልተሟላልንም። ቀኑ ሲደርስ ሁሉንም ነገር አሟልተን አንድ ነገር ብቻ ቀረን፤ ሳተላይት። ከመጀመሪያውም ስንገባበት OMN የኢትዮጵያ መንግሥትን አፈና አልፎ ሕዝቡ ዓይንና ጆሮ መድረስ የሚችለው በሳተላይት በኩል ብቻ እንደሆነ እናውቃለን። ነገር ግን ስለ ሳተላይት ስርጭት አሠራር የሚያውቅ ሰው ከመካከላችን አልነበረም። እውቀቱ አላቸው የተባሉ ሰዎችን አግኝተን ብናማክርም ምንም ሊጠቅሙን ሰላልቻሉ ኤሊያስ ኢብሳ የሳተላይት

ስርጭት እንዴት እንደሚሰራና እንዴት ማግኘት እንደሚቻል ለማጥናት ኃላፊነት ወሰደ።

ኤሊያስ አሜሪካ እንደሄድኩ ከተዋወኳቸው ሰዎች አንዱና ብዙ ሥራ አብረን የሰራን አጋሬ ነው።ሙያው ኢንጂነር ሲሆን፣ በተፈጥሮው ነገሮችን የማቀናጀት እና ችግር የመፍታትችሎታ ያለው ቀልጣፋ ሰው ነው።
ከሰዎች ጋር የመግባባት እና የማሳመን ክኅሎትን የተቸረ በመሆኑ፣ ሁሌም ለገቢ ማሰባሰብ አና ዋጋን ተከራክሮ አስቀንሶ ለመግዛት እናሰማራዋለን። ሰለዚህም የሳተላይቱን ጉዳይ መፍታት የሚችለው ኤሊያስ ብቻ ነው በሚል ተሰማምተን ኃላፊነቱን አስረከብነው። እርሱም በአጭር ጊዜ ለሳተላይት ሰርጭት የሚያስፈልገውን የቴክኒክ ሥራ ተረድቶ፣ የሚያከራዩንን ካምፓኒዎች አነጋግሮ ዝርዝር ሪፖርት ጽፎ አቀረበ።
ከምርቃቱ ቀን አሰቀድመን የሙከራ ሰርጭት ብንጀምርም ሰርጭታችን ግን ሀገር ቤት መድረሰ አቃተው፡ አንዳንዴ ደግሞ ቢደርሰም ጥራት ጎደለው። ችግሩን ለመፍታት ከአንዱ የሳተላይት ኩባኒያ ወደ ሌላኛው ስንሽከረከር ሳይታሰብ የምርቃቱ ዋዜማ ደረሰ። የምርቃቱን ቀን እንዳናራዝም ከፍተኛ ወጪ ወጥቶበታል፣ የተጠራው በርካታ ታዳሚም ከተማ ገብቷል።

ከሁሉም በላይ ለሕዝባችን ቃል በገባነው ቀን መጀመር አለብን ብለን እልሀ ውስጥ ገብተናል። በድንጋጤ እና በእልህ የተለያየ ካምፓኒ ስንምክር ቆይተን በሰተመጨረሻ በምርቃቱ ዋሄማ አኩለ ሌሊት ላይ ተሳካልን።
የOMN ስርጭት በጥሩ ጥራት ኦሮሚያ እየደረሰ መሆኑን ከሁሉም ዞኖች ተመልካቾቻችን አረጋገጡልን። በዕለቱ ደሰታችን ልዩ ስለነበር ኤሊያስ እና ሙሐመድ አብዶሽ ወደያዙት ሆቴል አቅንተን እየተዝናናን የልፋታችን ውጤት የሆነውን ስኬት አጣጣምን።
በሥራ መደራረብ ምክንያት እጅግ በጣም ቢደክመኝም መተኛት ግን አልቻልኩም። የምርቃቱ ቀን ንጋት 10 ሰዓት ሲሆን፣ ሙሐመድ አብዶሽን ቀስቅሼው «ወደ ሰቱዲዮ እንሂድ› አልኩት። ከሆቴሉ ስንወጣ ጎዳናው ላይ የተከመረው በረዶ እግሬን አቀዝቅዞ ንዝረቱ መላ አካላቴን አኮማተረው። ምን ተፈጥሮ ይሆን ብዬ አጎንብሼ ስመለከት ለካስ ጫማ አላደረኩም፣ እግሬ ባዶ መሆኑን ሲያይ ሙሐመድ በሳቅ ተንፈራፈረ።
ጠዋት ረፋዱ ላይ የሀገር ሽማግሌዎች፣ የሀይማኖት አባቶች እና አንጋፋ ታጋዮች ተሰብሰበው ስቱዲዮዋችንን መረቁ። ቃል የተገባው ነገር ተፈጽሞ በማየታቸው ዓይናቸው የደስታ እንባ እያቀረረ ምሰጋናቸውን አደረሱ። ከዚያ በመቀጠል ለዋናው ምርቃት ወደ ሚኒሶታ ዩኒቨርሲቲ አዳራሽ አመራን። ሕዝቡ አዳራሹን ከአፍ አሰከ ገደፉ ሞልቶ ጠበቀን። በዕለቱ ከእንግዶቹ ጋር አንድቀመጥ ታቅዶ ስለነበር ሥራ አልተሰጠኝም። ሆኖም ከአዳራሹ ውሰጥ የሚቀርጸውን ቡድን እና የሳተላይት ማዕከሉን ዕርጭት እንድታቀናጅ የቀጠርናት አንዷት ፈረንጅ ባለሙያ ድንገተኛ አደጋ ሰላጋጠማት፣ በእሷ አግር ተተክቼ የማቀናጀቱን ሥራ ወደ መሥራት ገባሁ።
ዋና አዘጋችን ዶ/ር ብርሃኑ ከአውሰትራሊያ ሆኖ መሰራት ያለበትን ነገር በስልክ እየነገረኝ በአንዱ ጆሮ እሱን እያዳመጥኩ፣በሌላኛው አዳራሽ ውስጥ ያሉትን ጋዜጠኞች እና ካሜራ ማኖች አየሰማሁ ወዲያ ወዲሀ ስሯሯጥ የሆነ ሰው በአጄ ይዤ ስጠጣ የነበረውን ቡና ገጭቶ ልብሴን

ከላይ እስከታች አለበሰው። ከሸሚዝ እስከ ጫማዬ አንድ ሳይቀር በቡና ተለወሰ። ቤት ገብቼ

የምቀይርበት ጊዜ ስላልነበረኝ እዚያው የሰዎችን ልብስ አስውልቄ መልበስ ጀመርኩ። ሸሚዝ ከሙሐመድ አብዶሽ፡ ጃኬት ከኤሊያፅ አና ጫማ ከቂጤሶ ተቀብቆ ለበስኩ።የዚያን ዕለት ያጋጠመኝ ችግር በዚህ ብቻ አላቆመም።ማታ ሳተላይቱ መሥራቱን አንዳረጋገጥንወደ ሆቴል ሄደን የበለነው ፒዛ አልተሰማማኝም ነበርና ዝግጅቱ ላይ ሆኜ በሆድ ቁርጠት እና

ሽንት ቤት በማመላለሰ ይበቀለኝ ጀምር። በዚህ ምክንያት በጊዜያዊ ሰቱዲዮ እና በሽንት ቤት መካከል አሁንም አሁንም አየተጣደፍኩ ለመመላለስ ተገደድኩ። አእምሮይ ስርጭቱን በማስተባበር ይጨናነቃል፡ ሆዴ በተራው በሕመም ያራውጠኛል።

ስርጭቱን የሚሰሩ ልጆች አናግሬ ወደ ሽንት ቤት በመጣደፍ ላይ ሳለሁ መድረኩን ሲመራ የነበረው ዶ/ር ስንታየሁ ስሜን ጠርቶ ንግግር እንዳደርግ ወደ መድረኩ ጋበዘኝ። ሆዴ አጣድደፎኛል፥ ሕዝቡ ተነሰቶ ስሜን እየጠራ ያጨበጭባል። በዚያ ሁኔታ ውሰጥ ወደ ሽንት ቤት መሄድ ስለከበደኝ እንደ ምንም ቻል አድርጌ ወደ መድረክ ወጥቼ ማይክራፎኑን ጨብጬ በጽሑፍ ያዘጋጀሁትን ንግግር ለማውጣት እጄን ወደኪሴ ስሰድ የለም፤ ለካሰ ቡና ከፈሰሰበት ልብስ ጋር አውልቄዋለሁ። ከመድረኩ ወርዶ መፈለግ ሰለማይታሰብ በአፌ ላይ የመጣውን ተናግሬ ለመውረድ ወሰንኩ።

«በሄድንባቸው ከተሞች ሁሉ ቃል የገባንላችሁ አንድ ነገር ነው። ወያኔን በጦር ማስወገድ ቢያቅተንም አሁን ላይ በሚዲያ በኩል የፈጠሩትን የበላይነት ለመስበር ለአንድ ቀንም አንተኛም ብለን ተነሳን። እንዳልነውም ያለ ዕረፍት ሰርተን ሕልማችንን አሳክተናል። ከዛሬ ጀምሮ በኦሮሚያ አየር ላይ ሌሎች ያላቸው የበላይነት ተሰብሯል ። የኦሮሚያን አየር-ሞገድ ነጻ አውጥተናል። ይህ የአየር ሞገድ ነጻነት ወደ ሁለንተናዊ አርነት እንዲሽጋገር ኃላፊነቱ የእናንተ ነው። አየር ላይ የፈጠርናትን ትንሽዬዋን ነጻነት። እንደ ችግኝ ውኃአጠጥታችሁ አፈሩን ኮትኩታችሁ ተንከባክባችሁ ካሳደጋችሁት ወደ መሬት የሚወርድበት ጊዜ ሩቅ አይሆንም›» በማለት እልህ በተለበሰ አነጋገር አስተጋባሁ። የሆዴን ሕመም በመቻል እንደምንም ጥርሴን ነክሼ ለአሥር ደቂቃ ያህል ንግግር አድርጌ ጨረሰኩ። ሕዝቡ ቆሞ አያጨበጨበና በፉጨት ስሜን እየጠራ ባለበት ከመድረኩ ወርጄ ወደ ሽንት ቤት ተፈተለኩ።

ለኦሮሞ ሕዝብ አንድ ጠንካራ ቴሌቪዥን ለማቋቋም የያዝነውን ውጥን በዚሀ መልኩ ከዳር አደረስነው። አብዛኛው ሰው የ"Oromo First" ዘመቻ ላይ ሚዲያ ለማቋቋም ቃል ስንገባ ቢደግፈንም ስኬቱ ለይ ግን ጥርጣሬ ነበረው። መሥራች ኮሚቴዎቹ እንኳን ጉዳዩን በእልሀ ይግፉት እንጂ እንደምናሳካው ያመንነው ጥቂቶቻችን ነን በመሀል ተሰፋ ቆርጠው ትተውን የሄዱም ነበሩ። ለትግሉ ድምፅ የሚሆን ሚዲያ መገንባት ብቻ ሳይሆን፣ የጋራ በራስ መተማመንን ለመመለስ (restoring collective self-esteem) ለቅድነው ዓላማም ትልቅ አርምጃ ነበር።

ከዚሀ ባሻገር ሚዲያ ማቋቋም አንዱ የሰላማዊ ትግል እቅዳችን ስለነበር ዓላማው እውን መሆኑ አንደ ግለሰብም ሆነ አንደ ሕዝብ ለሚቀጥለው ምዕራፍ በልበ ሙሉነት እንድንገሰግስ በር ከፈተ። በድርጅቶች መዳከም ተሰፋ ቆርጦ የነበረው የኦሮሞ ሕዝብ እንደ አዲስ ተሰፋው መለምለም እንዲሁም በአመራሮች ላይ ያጣው አምነት መመለሰ ጀመረ። የሕዝቡ ሞራል ተመልሶ ማንሰራራቱ እና በአመራር ላይ ተስፋ ማሳደሩ ቀጥለን ለሰራናቸው ግዙፍ ሥራዎች

ትልቅ መሠረት ሆኖልናል። ሕዝቡ የምናወጣውን እቅድ እና ስልት በማመን ለአፈፃፀሙ ከእኛ ጎን ተሰለፈ።

አስቀድሜ እንዳነሳሁት OMNን ማቋቋም ስናቅደው ለነበረው የሰላማዊ ትግል ዋነኛ አካል ነው። ሐሳባችን ለአንድ ዓመት የሚዲያ ዘመቻ አድርገን ሕዝቡን አንቅተን ከዚያ በኋላ ወደ ተቃውሞ እርምጃ መግባት ነበር። ያልጠበቅነው ነገር ቢኖር ሕዝቡ አሰቀድሞ በመንግሥት በመከፋት ችዕግሥቱ ተሟጧል። የሚዲያ ዘመቻውን በጀመርን በሁለት ወር ውሰጥ አመጽ ፈነዳ። OMN (OMN) ማርች 1 ቀን 2014 ሥራ ጀምሮ፣ አመጹ ኤፕሪል 25 ቀን 2014 (ሚያዚያ 17 ቀን 2009 አ.ም) በዩኒቨርሲቲዎች ውሰጥ ተቀሰቀሰ። OMN አመጹን በየዕለቱ በመዘገብ እንዲሁም እኔ ፣ነጌሶ ዱቤ አና ፕሮፌሰር ሕዝቅኤል ገቢሳ በየጊዜው ትንታኔ እያቀረብን አቅጣጫ አና ሞራል በመስጠት ተቃውሞውን አቀጣጠልነው።

ወደኋላ ላይ ብዙ ምሁራንን ያካተተ የተንታኞች ቡድን "ራባ ዶሪ። በሚል ስያሜ ተቋቋመ። በራባ ዶሪ ፕሮግራም በተደጋጋሚ ሲተርቡ ከነበሩት ውሰጥ ዶ/ር ጸጋዬ አራርሳ፣ ዶ/ር አወል አሉ፣ ዶ/ር ብርሃኑ ሌንጂሶ፣ ነጌሶ ዱቤ፡ ግርማ ጉተማ፣ አሕመድ ጊሼ፣ ዶ/ር ኢታና ሃብቴ፣ ፕሮፌሰር ሕዝቅኤል ገቢሳ፣ ዶ/ር ደረጀ ሃዋዝ እና ብረሃነመሰቀል ሰኚ ነበሩ፣ አኔም ተሳታፊ ነበርኩ። የቡድኑ አሰተባባሪ ግርማ ጉተማ ሲሆን የOMN ኤዲተር የነበረው ፈርሃን አብዱሰላም ደግሞ በቴክኒክ ያግዛቸዋል። ከፌስቡክ ተሳትፏችን በቀሰምነው ልምድ መሠረት፣ የራባ ዶሪ ቡድን አባላት ትንታኔዎችን በቴሊቪዥን መስኮት ከማቅረባቸው በፊት ሊተላለፍ በታሰበው አጀንዳ ላይ ሰፊ ውይይት በማድረግ ለትግሉ በሚፈይድ መልኩ ያቀርቡ ነበር።

የተለያዩ ሰዎች እና ቡድኖች አሰተያየት OMN ላይ አንዲንጸባረቅ ፍላጎታችን ቢሆንም ደጋግመው የሚቀርቡ ተንታኞችን በሦስት መሰፈርት እንመርጣለን። የመጀመሪያው መስፈርት፣ በተቻለ መጠን በኦነግ የቡድንተኝነት ውዝግብ ውስጥ ትልቅ ሚና የሌላቸው መሆን አለባቸው የሚል ነው። ይሀ መስፈርት በተደጋጋሚ ለትንተና የሚቀርቡ ሰዎች የአንድን ቡድን አመለካከት በማስተጋባት ሚዲያው የአንጃዎች የውዝግብ መድረክ እንዳይሆን በማሰብ የተቀመጠ ነው። ሁለተኛው፣ በኦሮሚያ እና በኢትዮጵያ ውሰጥ ያለውን ተጨባጭ ወቅታዊ መረጃ የሚከታተል እና ለመተንተን የሚያስችል እውቀት ያለው መሆን ነው። አብዛኛው በዲያሰፖራ የሚኖሩ ምሁራን ከሀገር ከወጡ ስለቆዩ ሀገር ውስጥ ካሉ ሰዎች ጋር ያላቸው ትስስር እምብዛም ከመሆኑ የተነሳ በየጊዜው የሚከሰቱ ኹነቶች ላይ ወቅታዊ መረጃ የላቸውም። ወቅታዊ እና ተጨባጭ መረቾዎችን ያላገናዘበ የፓለቲካ ትንታኔ ለትግል አይጠቅምም። ሦስተኛው መስፈርት፣ የሰላማዊ ትግል ስልት እና ዘዴዎችን የሚረዱ ወይም ለመረዳት ፍላጎት ያላቸው መሆን አለባቸው የሚሉ ናቸው። ሚዲያውን ያቋቋምነው ላሰብነው ሰላማዊ ትግል ልሳን እንዲሆን ታሰቦ በመሆኑ የሚቀርበውም ትንተና ይህን ዓላማ የሚደግፍ መሆኑ ነበረበት። በተጨማሪም የሚቀርቡት ተንታኞች የአካባቢ አና የሀይማኖት ብዙኅነት እንዲኖራቸው ጥረት አድርገናል።

በዚሀ መልኩ ስሕተታችንን እያስሰተካከልን፣ እየተማርን እና ያለብንን ጉድለት እየሞላን OMNን አጠናከርነው። ከሚኒሶታ በተጨማሪ፣ አምሰተርዳም፣ ካይሮ፣ ሜልቦርን እና ሲያትል ሰቱዲዮ በመክፈት፤ መጀመሪያ ላይ ሠላሳ ደቂቃዎች ብቻ የነበረውን የቴሌቪዥን ዝግጅት ወደ ሰዐታት አሳደግነው። ሕዝባዊ አመጹ ሲፈነዳ የአመጹ አስተባባሪዎች እና ሚዲያው ተናበው አንዲንቀሳቀሱ አደረግን።

## 6.8 ቃልን በተግባር

ሚኒሶታ ሄጄ OMNን የማቋቋም ሥራ ለመሥራት ቃል በገባሁት መሠረት በሦስት ወራት ውስጥ እንደጨረሰኩ ለተመደቡት የቦርድ አመራር እና ሥራ አስፈፃሚዎች አስረክቤ ወደ ኒው ዮርክ ተመልሼ ትምህርቴን ጀመርኩ። ሚኒሶታ በመሄዴ ያለፈኝን አንድ ሴሚስተር ክረምት በተማርኩት ኮርስ በማካካስ ወደ ኋላ ከመቅረት ዳንኩ። ሆኖም የOMNን ሥራ በየቀኑ ከመምራት ብወጣም ኃሄጠኞቹ እና አሥተዳደሩ በፈለጉኝ ጊዜ ከጎናቸው አልራቅኩም ነበር።

የ2014 አንደኛ ሴሚስተር ትምህርቴን እንደጀመርኩ OMN የመጀመሪያው ቀውስ አጋጠመው። ሥራ እንደጀመርን አካባቢ ሲታይ የነበረው የፐሮግራም ጥራት እየቀነሰ ሄደ። ገቢ የማሰባሰብ ሥራ እና የወጪ ቁጥጥር ትኩረት አጥቶ ወጪ በመብዛቱ ድርጅቱ ያለው ገንዘብ በጣም አሽቆለቆለ። የችግሩ አንዱ ምክንያት አመራሩ በአካል ሚኒሶታ አለመኖሩ ነበር። ዋና ዳይሬክተሩ ግርማ ታደሰ ከዋሽንግተን ዲሲ እና ዋና አዘጋጁ ዶ/ር ብርሃኑ ዲርባባ ከአውስትራሊያ ሆነው ነበር የሚሰሩት። ግርማ ሙሉ ሰዓት የሚሰራው ሥራ አና የሚያሳድጋቸው ትንንሽ ሕጻናት ሲኖሩት፡ዶ/ር ብርሃኑ ደግሞ በአሜሪካ እና በአውስትራሊያ መካከል የጊዜ አለመጣጣም አስቸገረው፣ ሚኒሶታ የሥራ ሰዓት ሲሆን እሱ ጋር አኩለ ሌሊት ይሆናል። ይህ ሁሉ ተደማምሮ ገቢ አና ወጪ ማመጣጠን፣ እንዲሁም ፐሮግራም አዘጋጅቶ በጊዜ ማሰራጨት ላይ ትልቅ ክፍተት ተፈጠረ።

የሥራ አስፈፃሚ ኮሚቴው አባላት ተወያይተው፣ ነገሮች በዚሀ ሁኔታ ከቀጠሉ OMNን በጥቂት ወራት ውስጥ ለመዝጋት እንደሚገደዱ አሳወቁ። ይህን አደጋ ለማስቀረት በአካል ሚኒሶታ ሆኖ የሚሠራ የሙሉ ሰዓት ዳይሬክተር ለመቅጠር በግልጽ የሥራ ማስታወቂያ እንዲወጣና በውድድር እንዲሆን ተወሰነ። እስከዚያ ድረስ ግን ምክትል ዳይሬክተሩ ሙሐመድ አብዶሽ በጊዜያዊነት ወደ ሚኒሶታ ሄዶ ለመሥራት ወሰነ። ሙሐመድ ሚኒሶታ ሄዶ ድርጅቱን በነጻ ለማገልገል ሲወስን በሙሉ ጊዜ ሥራ የሚከፈለውን ትልቅ ደሞዝ ለቆ፣ ልጁን እና የሰባት ወር ነፍሰጡር የነበረችውን ባለቤቱን ትቶ ነው።

ምለመላውን እንዲያሰተባብሩ ተመድበው የነበሩት የቦርድ እና የሥራ አሰፈጻሚ አባላት ለሥራ አሰፈጻሚነት ለመወዳደር ማመልከቻ ያስሰገቡትን ሰዎች ከገመገሙ በኋላ ሚዲያው ያጋጠመውን ችግር መፍታት የሚችል ሰው አለማግኘታቸውን ነገሩኝ። በዚህ ምክንያት ዋና ዳይሬክተር ሆኘ እያንዣበበ ያለውን አደጋ እንድገታ ተማጸኑኝ። የመጀመሪያ አቋሜ አይሆንም የሚል ነበር። እነርሱ ግን እየተፈራረቁ ተመላልሰው ወተወቱኝ። መስማማቴን ስገልጽላቸው የትምህርት ማስረጃዬን እና የሥራ ልምዴን (CV) አዘጋጅተው ውድድሩ ውስጥ አስገቡኝ። የእኔ እና የባልደረቦቼ ልፋት መና እንዳይቀር፡ እንዲሁም ሕዝቡ የሰነቀው ትልቅ ተስፋ እንዳይጨልም ተመልሼ ለመምራት ውሳኔ ላይ ደረሰኩ። ሥራ አስፈጻሚ ለማፈላለግ የተቋቋመው ኮሚቴ ማመልከቻ ያስገቡትን ግለሰቦች እና እኔን ቃለ-መጠይቅ አድርጎ፡ በመጨረሻም እኔን መረጠ።

የተወሰኑ የቦርድ እና የሥራ አሰፈፃሚ ኮሚቴ አባላት በውሳኔው አልተደሰቱበትም ነበር። አንዳንዶቹ ትምህርቱን ለሁለተኛ ጊዜ አቋርጬ መምጣቴ በእኔ እና በቤተሰቤ ላይ የሚያደርሰው ጉዳት አሳሰባቸው። ሌሎቹ ደግሞ በፓለቲካ ተሳትፎዬ አወዛጋቢ በመሆኔ የሚዲያ መሪነቴ ከተለያዩ ቡድኖች "OMN ነጻ ሚድያ አይደለም የሚል ቅሬታ ያስነሳል በሚል ሥጋት አደረባቸው። ከላይ በተጠቀሱት ምክንያቶች የቦርድ አባላትን በግል በማነጋገር የሥራ አስሰፈጻሚነቱን ኃለፊነት እኔ እንዳልይዘው ለማሳመን ግፊት አደረጉ። በእነዚህ ጉዳዮች ላይ ቦርዱ ሰፊ ክርክር ካደረገ በኋላ በአብላጫ ድምፅ የ ዳይሬክተር ሆኜ እንድመደብ ወሰነ። እኔም ለሁለተኛ ጊዜ ትምህርቴን አቋርጬ ወደ ሚኒሶታ ለማቅናት ተገደድኩ።

ለሁለተኛ ጊዜ ትምህርት ለማቋረጥ መወሰኔ ፕሮፌሰሮቹን በጣም አናደዳቸው፣ አሰዘናቸውም። በአካል ሄጄ መናገሩ ሰላሳፈረኝ ኢሜል ላኩላቸው። OMN ቢዘጋ ሕዝባችን ላይ ምን ዓይነት ጉዳት እንደሚያስከትል ሰለማውቅ፣ የፕሮፌሰርቹን ምክር እና ቁጣ አሻፈረኝ ብየ፣ አርፋሴንም አሳምኝ ወደ ሚኒሶታ በድጋሜ ተመለሰኩ። መጀመሪያ OMNን ለማቋቋም ወደ ሚኒሶታ በሄድኩበት ወቅት የድርጅቱን ወጪ ለመቆጠብ ስል አዳማ አብሬው እማር ከነበረው ጓደኛየ አቡበከር ኤደኦ (አቡ) ጋር አፓርታማ ደባል ሆኜ፣ ከመንገድ ላይ ያገኘናትን አሮጌ ፍራሽ አጽድተን ስንተኛባት ነበር፡ አሁንም ለሁለተኛ ጊዜ ተመልሼ ከእሱ ጋር ተዳበልኩ።

ሥራ እንደጀመርኩ OMN ውስጥ ያለውን ችግር ለመቅረፍ ሁለት ተግባራዊ እርምጃዎችን ወሰድኩ። የመጀመሪያው የOMN ሀብት አሰባሳቢ ኮሚቴ (OMN local support) በንቃት እንዲሰሩ በአዲስ ማደራጀት እና ሥልጠና መስጠት ነበር። በዚህ ረገድ በሰሜን አሜሪካ፣ በአውሮፓ፣ በደቡብ አፍሪካ፣ በአውሰትራሊያ እና በአረብ ሀገራት ውስጥ በሚገኙ ስልሳ ሦሰት ከተሞች ውስጥ የድጋፍ አስተባባሪ ኮሚቴዎችን በማቋቋም፣ በፈለግነው ፍጥነት የድጋፍ ማሰባሰቢያ ዝግጅቶችን ለማቀናጀት የሚያስችል አቅም ገነባን። ይህን ያህል ብዛት እና ስፋት ያለው አደረጃጀት መገንባት የቻለ ሌላ የኢትዮጵያ ድርጅት መኖሩን እጠራጠራለሁ። የድጋፍ ኮሚቴዎችን በስፋት ማደራጀት በመቻላችን በጥቂት ጊዜ ውስጥ ድርጅቱን በገንዘብ አቅም ጠንካራ ማድረግ ተቻለ።

ድርጀቱን አቋቁሜ ወደ ትምህርት ቤት ስመለሰ ለዕድሰት ወር የሚበቃ ተቀማጭ ገንዘብ የነበረው ቢሆንም፤ እኔ ስመለስን ግን ወደ አንድ ወር ሰለወረደ፣ በአፋጣኝ እንዲያገግም ማድረግ አሰፈላጊ ነበር። ይህንንም ለማሳካት ለሦስት ወር ባደረግነው አደረጃጀት የማስፋት እና ገንዘብ የማሰባሰብ ዘመቻ ለዓመት የሚሆን ተቀማጭ ገቢ አገኘን። በዚሀ ሁኔታ ከገንዘብ ጋር ተያይዞ ሊከሰት የነበረው ውድቀት ተቀረፈ።

ዋና ሥራ አሰፈጻሚ እንደሆንኩ የወሰድኩት ሌላው እርምጃ በዝግጅት ክፍሉ እና በአስተዳደር ዘርፍ ውሰጥ ረብሻ ሲፈጥሩ የነበሩ ሠራተኞች እንዲስተካከሉ ወይም ለቀው እንዲወጡ በማድረግ የድርጅቱ ውሰጣዊ ሰላም እንዲረጋገጥ ማስቻል ነበር። አመራር በአካል ቦታው ላይ ባለመኖሩ በሠራተኞች መካከል የነበረው ፉክክር፣ ጥርጣሬ እና መናናቅ ሥራውን አዳከመው። ይህን ችግር በምክክር ለመፍታት የተደረገው ሙከራ አንዳንድ ሰዎችን ማስተካከል ስላልቻለ፣ ብሎም ወደ አድማ ማምራት ሰለጀመረ፡ የተወሰኑ ሠራተኞችን ከሥራ ማሰናበት ግዴታ ሆነ። ይህ ውሳኔ ለትልቅ የስም ማጥፋት ዘመቻ ቢያጋልጠንም፣ ድርጅቱን አድኖ ውሰጣዊ ረብሻን በማሰወገድ ሥራ ላይ እንዲያተኩር አድርጓል። የOMNን አንደኛ ዓመት ምሰረታ ሰናከብር

ድርጅቱን ከመውደቅ ሰጋት አውጥተን አስተማማኝ አቋም ላይ አደረስነው። ያጠራቀምነው ገንዘብ ከወርሃዊ ወጪ ተርፎ ለችግር ቀን ተቀማጭ ሆነልን። ሚዲያው ተቋቀሞ ሰድስት ወር እንኳን አይዘልቅም ብለው ሲጠራጠሩ የነበሩ ሰዎችም ቀልባቸው መለስ አለ።

ለአንደኛ ዓመት ምስረታ በዓል ዋዜማ ለሠራተኞች ባቀረብኩት ጽሑፍ ላይ OMN ሚዲያ ብቻ ሳይሆን የትግል ማዕከል እንደሆነ መገንዘብ እንዳለበቸው አስረዳሁ። «ይህን ሚዲያ አንደ ባቡር/አውቶቡስ ብንወሰደው፣ ከተሳፋሪዎች ውሰጥ የተወሰኑት ባሻቸው ቦታ መውረድ ቢችሉም፣ባቡሩ ግን መዳረሻውጋር እስከሚደርስ ድረስ ወራጁን እያራገፈ ጉዞውን ይቀጥላል» ስል በምሳሌ አብራራሁ።
OMN በግራም በቀኝም ያሉት በሮቹ ክፍት አንደሆነ ባቡር ሲሆን፣ አንድ ተሳፋሪ የባቡሩ ፍጥነት፣ የሾፌሩ ወይም የሌሎች ተሳፋሪዎች ፀባይ ካልተሰማማው በፈለገበት ቦታ መውረድ ይችላል። እንዲሁም የአንድ ተሳፋሪ ፀባይ ለሾፌሩ ወይም ለተቀሩት ተሳፋሪዎች ካልተመቻቸው ማስውረድ ይችለሉ። የወረደው ተሳፋሪም ሌላ ቀን ተመልሶ መሳፈር ከፈለገ በሩ ክፍት ነው። ተሳፋሪው በራሱ ፍለጎት ሲወርድ ወይም በተሳፋሪዎች/በሾፌሩ እንዲወርድ ሲደረግ፣ ጭቅጭቅ እና ግብግብ በመፍጠር ቂም መያዝ የለበትም። ምክንያቱም አንድ ቀን በሰለም የወረደ ወይም እንዲወርድ የተደረገ፣ ነገ ለመመለስ አይቸገርምና። ብዙ ሰዎች ከOMN ወጥተው የስም ማጥፋት ዘመቻ ሲከፍቱ ድርጅቱ አንድም ቀን ማስተባበያ ያልሰጠው ይህን መርህ ስለምንከተል ነበር።
በዚሀ መልኩ በተለያዩ አንጃዎች እና ግለሰቦች የሚደረግብንን የስም ማጥፋት ዘመቻ በትዕግሥት እና በብልኃት አለፍነው። ከውጪ ደግሞ ከኢትዮጵያ መንግሥት እና ከአማራ ኃይሎች የሚቃጣብንን ዘመቻ በመመከት OMNን ከውድቀት አትርፈን፣ በየቀኑ የሀገሪቷን የፖለቲካ አጀንዳ የሚፈጥር ትልቅ ሚድያ ማድረግ ቻልን።
የኢትዮጵያ መንግሥት የOMN ስርጭት ሕዝቡ ጋር እንዳይደርስ ለመግታት ይጠቀምበት የነበረው ዋናው ስልት ሳተላይት ላይ እንዳይተላለፍ በማድረግ ነበር። መጀመሪያ የሳተላይት ስርጭቱን ማፈን (jamming) ላይ አተኮረ። መንግሥት የእኛን ጣቢያ ለማፈን በሚወስደው እርምጃ በሳተላይቱ ላይ ያሉ ሁሉም ጣቢያዎች ሰለሚታፈኑ የሳተላይት ኩባኒያዎቹ ጣቢያችንን ያስወጡታል። ከአንድ ሳተላይት ላይ ካወረዱን በኃላ ሌላ ኩባኒያ አግኝተን ዋጋ ተስማምተን የእኛን እና የእነሱን ሲስተም አቀናጅተን ስርጭት ለማስጀመር ጊዜ ይወሰዳል። ይህን ስለተረዳን በአንዱ ሳታላይት እያሰራጨን በጎን ከብዙ ኩባንያዎች ጋር ኮንትራት ተፈራርመን በመጠባበቅ፡ ከአንዱ ሳተላይት ሲያወርዱን ወዲያው ቀድመን ካዘጋጀናቸው ኩባንያዎች በአንዱ ማሰራጨት እንጀምራለን።
ከተወሰነ ጊዜ በኋላ ዩቴልሳት (eutelsat) የተባለ ኩባኒያ የመንግሥትን አፈና ሊቋቋም የሚችል የሳተላይት ቴክኖሎጂ አምጥቶ እፎይ ስንል መንግሥት በአዲስ ሰልት ብቅ አለ። ከሀያ በላይ የሚሆኑ የፌደራል አና የክልል ቴሌቪዥን ጣቢያዎችን በዩቴልሳት ለማሰተላለፍ የአምስት ዓመት ኮንትራት ፈረመ፤ጣቢያው የOMNን ስርጭት ካስቀጠለ መንግሥት ኮንትራቱን ሰለሚያቋርጥ ኩባንያው ሀያ አምሰት ሚሊየን ዶለር ያጣል ማለት ነው።

መንግሥት ገሚሱን በማፈን፡ ሌላውን በገንዘብ በማማለል፣ ሰርጭታችንን ወደ ኢትየጵያ

በቀጥታ ከሚያሰተላልፉ ሳተላይቶች ማሳገድ ቻለ። እኛም ተሰፋ ሳንቆርጥ ተመልካቾች በቤታቸው ጣሪያ ባለው ዲሽ ላይ "LNB" የተባለ እቃ በመግጠም ወደ ኢትዮጵያ በቀጥታ በሚያሰተላልፉ ሳተላይቶች ላይ ስርጭታችንን ማግኘት እንደሚችሉ ተረዳን። ይሀንንም ለሕዝቡ አሳውቀን ሰርጭታችንን ስንጀምር የመንግሥት ፖሊሶች እና ሚሊሻዎች ሁለት "LNB" ያላቸውን ዲሾች በየቤቱ ጣሪያ ላይ ወጥተው ማውረድና ባለቤቶቹን ማንገላታት ጀመሩ። ስንቱን ቤት ዘረው ይዘልቁታል? በወቅቱ ሰርጭታችን ወደ ዘጠኝ ሚሊዮን በሚደርሱ ቤቶች ይደርስ ሰለነበረ ሁሉንም ማውረድ አልቻሉም፡ በሳተላይት ጉዳይ ከመንግሥት ጋር የነበረብንን ችግር በዚሀ መልኩ በአሸናፊነት ተወጣን።

OMNን በማቋቋም እና በማሳደግ ውስጥ በርካታ የማይረሱ ገጠመኞች አሉኝ። የተወሰኑትን ላካፍላችሁ አንድ ቀን ለገቢ ማሰባሰቢያ ፕሮግራም ሳን ዲዬጎ ካሊፎርኒያ ሄድኩ። ዝግጅቱ አንደተጀመረ አንጋፋ የኦሮሞ ታጋይ የሆኑት ሐጂ ቃሲም የሚባሉ ሽማግሌ መድረኩን ከሌሎች ሽማግሌዎች ጋር መርቀው ከፈቱ። የገቢ ማሰባሰቢያ ዝግጅቱ ሲጀመር ታዳሚው መስጠት የሚችለውን የገንዘብ መጠን ቆሞ እየተናገረ መለገስ ጀመረ። የሐጂ ቃሲም ልጅ በተራው ተነስቶ ገንዘብ ሳይሰጥ በፊት ምርቃቱን ማሽጎድጎድ ጀመረ። ልጁ አየመረቀኝ እያለ አባቱ ሐጂ ቃሲም በከዘራቸው ወደ ልጃቸው አየጠቆሙ <ልጄ፣ ምርቃት አንደሆነ የእኔ ይበቃልና ብሩን ሰጥተሀ ቆጥ በል›› አሉት። ተሳታፊዎቹ በከፍተኛ ድምፅ ስለሳቁ ልጁ ተሸማቆ ተቀመጠ።

በሌላ የገቢ ማሰባሰቢያ ፕሮግራም አንድ ፕሮፌሰር ተነስቶ ሀያ ደቂቃ ያክል ካወራ በኋላ ሁለት መቶ ዶላር ሰጥቶ ቁጭ አለ። ከእሱ በፊት ሲሰጥ የነበረው ትንሹ የገንዘብ መጠን አምስት መቶ ዶላር ነበር። አንዲት ሴት ከተቀመጠችበት ተነሰታ ስሟን ከተናገረች በኋላ የፅዳት ሥራ እየሰራች እንደምትተዳደር ገለጸች። አሰከትላም <<ከእኔ በፊት የተናገረው ፕሮፌሰር የገንዘብ ችግር ያለበት ይመሰላል።

ያቺ ችንሸ ገንዘብ በዚህ ትልቅ ምሁር ሰም መመዝገብ ሰለሌለባት ሁለት መቶ ዶላሩን መልላሱለት። እኔ በእሱ ስም አንድ ሺ ዶላር ይኸው ሰጥቻለሁ>> ብላ ቼክ መፃፍ ጀመረች። ድርጊቷ ሰውዬውን ለማዋረድ መሆኑን በመረዳት ከታዳሚዎቹ የተወሰኑት ተይ ቢሏትም፣ እሷ ግን ቼኩን ገንዘብ ለሚሰበሰቡት ሰጥታ ሁለት መቶውን ተቀብላ ለፐሮፌሰሩ መለሰችለት። ፕሮፌሰሩም በኅፍረት ተነሰቶ ወጣ። የሰውዬውን ሞራል ለመጠበቅ «ማንም የፈለገውን ይሰጥ ተውት› ብዬ ስናገር ሴትይዋ «ዝም በል አያገባሀም>> ብላ ፀጥ አሰኘችኝ። ከምስረታው ጀምሮ አመራርነቱን እሰከለቀኩበት ድረሰ የOMN ሰማንያ በመቶ (80%) የሚሆነው ድጋፍ ዝቅተኛ ገቢ ካላቸው የፅዳት ሠራተኞች፣ የታክሲ ሾፌሮች እና ፋብሪካ ውሰጥ የጉልበት ሥራ ከሚሰሩ ደጋፊዎቻችን የሚገኝ ነው። አብዛኞቹ ደግሞ ሴቶች ነበሩ፡ በኦሮሞ ትግል ውሰጥ ሴቶች ለሚጫወቱት ጉልህ ሚና ይህ አንዱ ማሳያ ነው።

ሌላው ገጠመኝ፣ ዲሴምበር 2015 የማሰተር ፐላን ተቃውሞ ለሁለተኛ ጊዜ ሲቀሰቀስ፡ ምዕራብ ሸዋ እና ምዕራብ አርሲ ከፍተኛ ተቃውሞ ሲደረግ አንዲሁም መሥዋዕትነት ሲከፈል ነበር። ገበሬዎች ወደ አመጹ በመቀላቀል የቀበሌ አሥተዳደሮችን እያባረሩ ትጥቅ ማሰፈታት ጀመሩ። ወጣቶች እጃቸውን አጣምረው እሰከ አፍንጫው ከታጠቀው የአጋዚ ጦር ፊት ይቆሙ ነበር። መንግሥት በጭንቀት ደጋግሞ አዋጅ ያወጣል፣ OMNም የተቀጣጠለውን እሳት በየቀኑ ያራግባል። ማታ ሰቱዲዮ አድሬ መረጃ አሰባስቤ እጠብቃለሁ፣ ጋዜጠኞቹ ጠዋት መጥተው

ዜናውን ጽፈው ያነባሉ። የሆነ ቀን አንድ ጋዜጠኛ ከሥራ ቀረ፤ ሌላኛው ቢመጣም ሥራ ትቶ ተክዞ ተቀምጧል። ጠርቼ ምን እንደሆነ ሰጠይቀው «የዛሬውን ዜና ማንበብ አልችልም። ቤተሰቦቼን እያሰፈራሯቸው ነው›› አለኝ። እሺ ተውና ሂድ አልኩት። ሦስተኛው ጋዜጠኛ ቡና ገዝቼ መጣሁ ብሎ በዚያው ቀረ። ዜና የሚያነብ ሰው ስናጣ እኔ ጽፌው ካሜራ ማናችን ፉአድ ሲራጅ አነበበው።

በወቅቱ የኢትዮጵያ መንግሥት ብቻ ሳይሆን፣ የአሜሪካም ጫና እየበረታ መጣ። የኢትየጵያ መንግሥት በተደጋጋሚ ስሞታውን ለአሜሪካ ሰለሚያቀርብ፤ ምክር አዘል የማስጠንቀቂያ መልዕክቶች ይደርሱናል። ይህ ደግሞ «የአሜሪካ መንግሥት ጀዋርን አስሮ OMNን ሊዘጋ ነው» የሚል ሀሜት እንዲናፈስ አደረገ፤ ሀሜቱን ያጠናከረው ደግሞ ፖሊሶች ወደ ሚዲያው ግቢ መማላለሳቸው ነበር።

ሀሜቱ ሕዝቡ ውስጥ ተሰራጭቶ ሰለነበር፤ ሌላ ጊዜ እኛን ለማበረታታት እና ዜና ለመስማት በሚመጡ ሰዎች ይሞላ የነበረው ቢሯችን ባዶ ሆነ። ሌላው ቀርቶ እንጀራ እና አንባሻ ከኦሮሞዎች ሱቅ ለመግዛት ስሄድ ሰው ከእኔ ጋር ላለመታየት ዞር ማለት ጀምረ። ከኢትዮጵያ መንግስት በሚደርሳቸው ስሞታ ምክንያት፣ የአሜሪካ ባለሰልጣናት፣ በOMN እና በፌሰቡክ የማደርገውን የሚዲያ ዘመቻ ለዘብ እንዳደርግ በተደጋጋሚ ይወተውቱኝ የነበረ ቢሆንም፣ የአካባቢው ፖሊሶች ወደ OMN የሚመላለሱበት እውነተኛው ምክንያት ግን የተለያዩ ማስፈራሪያዎች ይደርሱን ሰለነበረ ደኅንነታችንን ለማረጋገጥ ነው።

እንደዚህ አይነት ብዙ ውሰጣዊ እና ውጫዊ ጫናዎችን እያለፍን ን አቋቁመን፣ ደግፈን፣ አሳድገን በኦሮሞ ትግል ውሰጥ ያን የሚያክል ድርሻ እንዲጫወት ማድረጋችንን ወደኃላ ተመልሼ ሳሰበው ተዓምር ይመሰለኛል። ሚዲያ የመምራት ልምድ ሳይኖረን፣ በዚያች ትንሽየ ገንዘብ የኢትዮጵያን ፖለቲካ አንቀጥቅጠን፡ ያን አሰከፊ ሥርዓት መቀየር እውነትም ተዓምር ነው። ይህ ተዓምር እንዲሁ በቅፅበት የመጣ ሳይሆን በስልት፡ በመሥዋትነት እና በጠንካራ ሥራ የተገኘ ነው። OMNን እንዳቋቋምን በሚዲያ ሥራ እንዲሳካልን ሦሰት ወሳኝ መርሆዎችን (Guiding Principles) መከተል እንዳለብን አሳስብ ነበር። እነዚህ «3p» የምላቸው መርሆዎች የሥራ ፍቅር (passion) ፣ ብቃት (performance) እና የሥራ ሥነ-ምግባር (professionalism) ናቸው።

1. የሥራ ፍቅር (passion) ፡ ለሚዲያ ሥራ ያለን ከፍተኛ መነቃቃት፡ ሞራል እና ጥልቅ ፍለጎት ብለን መፍታት እንችላለን። በተለይ 32 ውሰጥ የሚሰራ ሰው ከሚዲያ ሥራ ባሻገር ለትግሉ ትልቅ ፍላጎት እና ሞራል ሊኖረው ይገባል። የሕዝባችንን እውነት አውቆ ለውጥ ለማምጣት የትኛውንም መሥዋዕትነት መክፈል አማራጭ ሳይሆን ግዴታ መሆኑን መቀበል ግድ ይለል። በተጨማሪም ሚዲያ በትግል ውስጥ ያለውን አቅም አውቆ ለመጠቀም ተፈጥሯዊ ተነሳሽነት (innate desire) ሊኖረው ይገባል። በአጠቃላይ የትግል ሚዲያ ውስጥ ሰርቶ ሕዝቡን ማገልገል የሚፈልግ ሰው ሚዲያው የተቋቋመለትን የፖለቲካ ዓለማ አጥብቆ የሚያምን፣ የጋዜጠኝነት ፍቅር ያለው እና በሚሰራውም ነገር ከልቡ ደሰተኛ መሆን መቻል አለበት።

2. ብቃት (performance) ፤ የተሰማሩበትን ሥራ በተቀመጠው ጊዜ እና ጥራት መፈጸም መቻል ማለት ነው። የሚዲያ ፍላጎትም ሆነ ለሕዝባችን ያለን ክብር እና ፍቅር ወደ ተጨባጭ ሥራ ካልተቀየረ ጥቅም የለውም። ስለሆነም ሁለተኛው መርህ በጽናት እና በጥንካሬ መሥራትን ይጠይቃል። ጊዜን እና አቅምን መሥዋዕት በማድረግ ተጽዕኖ የሚፈጥሩ ዝግጅቶችን በትንሽ ወጪ መሥራት አለብን፣ ይህም ያለ ብቃት ግቡን መምታት አይችልም። የሚዲያ ሥራ ውጤት የሚያመጣው ወቅታዊ፡ ተዓማኒ እና ማራኪ ሲሆን ነው። ይህ የሚሳካው ተለዋዋጭ በሆነ የፖለቲካ ሁኔታ ውስጥ ሐሳብ ሳይከፋፈል መረጃ መሰብሰብ እና መመርመር፡ ከዚያም በፍጥነት እና በጥራት መሥራት ከተቻለ ብቻ ነው።

3. የሥራ ሥነ-ምግባር (professionalism) ፤ ይህ ደግሞ የሚዲያ ሥራን ለማካሄድ የሚያስፈልገውን መልካም ባሕርይ እና ሥነ-ምግባር መላበስ እና በዚያም መመራት ነው። አዘጋጅተን የምናቀርባቸው ዝግጅቶች ከሚዲያ የሚጠበቀውን ደረጃ (standard) የሚያሟሉ ይዘታቸው እና ጥራታቸው ለተመልካች ክብር የሚመጥኑ መሆን አለባቸው። ትልቅ የሥራ ፍቅር ኖሮን ሌት ተቀን ብንሰራም፡ ሥራው ሙያው በሚጠይቀው ሥነ-ምግባር ካልተመራ የታለመለትን ዓላማ ሊያሳካ አይችልም። የሚዲያ ሙያ ስንል ሁለት ነገር ያካትታል። እነርሱም ሥነ-ምግባር እና የቴክኒክ ችሎታ ናቸው። ሥነ-ምግባር ዓለም የሚመራበትን የሚዲያ መስፈርት መጎናጸፍ ብቻ ሳይሆን የምናገለግለውን ማኅበረሰብ ባሕል ማወቅንም ያካትታል። ቴክኒክ ደግሞ መረጃን ሰብስቦ በማቀናጀት የማቅረብ እውቀት እና ብስለት ነው። ቴክኒክን ትምህርት ቤት ስንማረው፣ የሥራ ሥነ-ምግባር እና መመሪያን የሚያሰቀምጠው ድርጅቱ ነው። ከባዱ ነገር ሥነ-ምግባርን እና ቴክኒክን ቀጣይነት ባለው መልኩ ወደ ሥራ መተርጎም ነው። የኦሮሞን ትግል ለመደገፍ በተቋቋመ ሚዲያ ውሰጥ የሥራ ሥነ-ምግባር (professionalism) ማለት የጋዜጠኝነትን ሥነ-ምግባር፣ ከኦሮሞ ልማድ እና የትግል ዓላማ ጋር አጣጥሞ በጠንካራ የቴክኒክ እውቀት አግዞ መሥራት ማለት ነው።

OMN በሶስቱ መርሆዎች መመራቱ ሕዝቡ ውስጥ ብቻ ሳይሆን የምናራምደውን ፓለቲካ በሚቃወሙት ዘንድ ሳይቀር እንዲከበር እና እንዲደመጥ አደረገ። አዲስ ሠራተኛ ሲቀላቀለን በሦሰቱ ነጥቦች ላይ መመሪያ (orientation) ይሰጠዋል። ሦስቱን ያሟላ ሰው ይቀጠራል ማለት እይደለም። ፍላጎት ያለው ሙያ ሊጎድለው፣ ሙያ ያለው ደግሞ መሥዋዕትነት መክፈል ላይ ሊሰንፍ ይችላል። ከፍተኛ ችሎታ ያላቸው ነገር ግን ይህንን ችሎታ በተጨባጭ ሥራ መቀየር ደካማ የሆኑ ሰዎችን አይተናል። በብሔርተኝነት ልባቸው የተቃጠለ ነገር ግን ሙያ እና ተሰጥዖ የሌላቸውም አጋጥመውናል። እነዚያን ሰዎች ድክመታቸውን እንዲያሻሽሉ በጣም እንጥራለን። ስንቀጥራቸው ኮንትራት ሳይፈርሙ በፊት ለሦስት ወር እንደ ሙከራ (probation) እንዲሰሩ እናደርጋለን። በዚያ ጊዜ ደካማ ጎናቸውን በማረም ላይ ተሰፋ ካሳዩ በቋሚነት እንቀጥራለን፡ ካላሻሻሉ እንሸኛቸዋለን።

በሌላ በኩል አንዳንድ ሰዎች ረጅም ጊዜ ከሰሩ በኋላ የሙያ ፍላጎት ወይም የሥራ ትጋት እያጡ ሄደው መሻሻል ካቃታቸው ላበረከቱት አስተዋጽዖ አመስግነን እናሰናብታለን። ከሦሰቱ መፅፈርቶች በአንዱ ወይም ከዚያ በላይ ችግር የታየባቸው እና ለማሻሻል የማይሞክሩ ሠራተኞችን በድርጅቱ ውሰጥ ማቆየት ድክመታቸውን ወደ ሌሎች በማጋባት ድርጅቱን

ይጎዳሉ። ሁለት በሬ ጠምደን አንዱ ከተኛ ወይም ከተንጓተተ ያኛውን አንደሚያዳክመው ሁሉ፣የአንድ ሠራተኛ ስንፍና እና ብልግና ውሎ አድሮ ወደ ሌሎችም ተሰፋፍቶ የሥራ ቦታውን በመመረዝ ከፍተኛ ጉዳት ያስከትላል። ስለዚህ ማረም ካልተቻለ በጊዜ ማሰናበት ያስፈልጋል።

እንደዚያ ዓይነት ሰዎችን ማረም አቅቶን በሸኘናቸው ቁጥር ቅሬታ ይቀርብብናል። የተባረሩት በራሳቸውድክመት ሳይሆን በአሥተዳደራዊ መድሎ አስመስለው ሕዝቡ ውሰጥ ሀሜት ይነዛሉ። እኛ ደግሞ ቀደም ብዩ በጠቀሰኩት የባቡሩ መርህ ሰለምንመራ ያሰናበትነውን ወይም ለቆ የወጣን ሠራተኛ ድክመት ለሕዝቡ አንገልጽም። ለቅሬታ እና ለሀሜት ምላሽ አለመስጠታችን ለትችት እና ለሰም ማጥፋት ቢያጋልጠንም፡ ከድርጅታችን የወጡትን ባለማቁሰልና ግንኙነታችን እንዳይበጠሰ በማድረግ ድክመታቸውን ካሰተካከሉ እንደገና አብረን የመሥራት ዕድል እንዲኖረን በሩን ክፍት ያደርጋል። ለዚሀ መርህ ጠቃሚነት ማስረጃው በተለያየ ጊዜ ከOMN ተሰናብተው ወይም በራሳቸው ወጥተው የነበሩ ሰዎች በሌላ ጊዜ ተመልሰው መሥራታቸው ነው።

ከላይ ከተጠቀሱት ሦስቱ የሥራ መርሆዎች (Guiding principles) በተጨማሪ ፣ OMN «የኦሮሞን እውነት በእውነተኛ መንገድ ብቻ›› በሚል እሳቤ ይመራል። ይህን ሐሳብ ያፈለቀው የድርጅታችን ዋና አዘጋጅ ዶ/ር ብርሃኑ ዲርባባ ነው። «የኦሮሞ ሕዝብ እውነት አለው። ከዚሀ እውነት ውስጥ የተነገረው በጣም ትንሹ ነው። ሰለሆነም የኦሮሞን ሕዝብ ለመጥቀም ምንም ዓይነት ውሸት መጨመር አያስፈልግም። የሕዝቡን እውነት እውነተኛ በሆነ መንገድ ብቻ ጥሩ አድርጎ አዘጋጅቶ መዘገብ በቂ ነው›› ይል ነበር። ይህን መመሪያ መከተሉ የሚዲያውን ተዓማኒነት (credibility) በማሳደግ ረገድ በጣም ጠቅሞታል።

OMN ዶ/ር ብረሃኑ ዲርባባ ባስቀመጠው አቅጣጫ «የኦሮሞን እውነት በእውነተኛ መንገድ ብቻ›› በማቅረብ ከኦሮሞ ትግል ተጻራሪ የቆሙ ኃይሎች በሚዲያ በኩል የነበራቸውን የበላይነት መስበር ቻለ። ከዚያም አልፎ ለቁሮ ትግል ሰትራቴጂያዊ የግንኙነት መድረክ (strategic communication platform) በመሆን፣ በአጭር ጊዜ ውሰጥ ዓለምን ያስደነቀ ውጤት አሰገኘ።

በOMN ውሰጥ ከተጫወትኩት የመሪነት ሚና እና የስድሰት ዓመት የሥራ ልምድ በመነሳት፤ የብዙዎች ሥጋት «ተተኪ አመራር አላፈራሀም፣ OMN ከአንተ ውጪ ቆሞ መሄድ አይችልም፤ ይወድቃል» የሚለው ነበር። ይሁን እንጂ ወደ ሀገር አንደተመለሰኩ በሚዲያው ውሰጥ ያለኝ ሚና እየቀነሰ ሄደ። የድርጅቱን ሥራ ቶሌራ ፍቅሩ አንደ ማናጀር እና ደጀኔ ጉተማ ዋና ኤዲተር በመሆን አሰቀጠሉት። አልፎ አልፎ ሐሳብ በመሰጠት እና ሚዲያውን ለማንቀሳቀስ የሚያሰፈልገውን ገንዘብ በማሰባሰብ አግዛቸው ነበር። በኋላ ላይ ወደ ፖለቲካ ፓርቲ ለመቀላቀል ስወሰን ከዋና ሥራ አሰፈጻሚነት ራሴን አግልዬ ግርማ ጉተማ ዋና ዳይሬክተር ሆኖ በእኔ እግር ተተካ።

ከታሰርኩ በኋላ መንግሥት የፊንፊኔውን ስቱዲዮ ቢዘጋም፣ በውጭ ሀገርም የሐሰት ክሰ በእጅ አዙር አስከፍቶ እና ብዙ ገንዘብ አውጥቶ ሰፊ ጥረት ቢያደርግም OMNን ማጥፋት አልቻለም። ለረጅም ጊዜ የእኔ ምክትል ሆኖ ሲሰራ የነበረው ሙሐመድ አብዶሽ ለሦስተኛ ጊዜ ሥራውን እና ቤተሰቡን ጥሎ የዋና ዳይሬክተርነትን ኃላፊነት በመረከብ፡ በዚያ ወሳኝ ጊዜ ሥራውን አስቀጥሏል።

ምናልባት ፊንፊኔ የሚገኘው የOMN ቅርንጫፍ ከተዘጋ ብለን በናይሮቢ ትንሽ ሰቱዲዮ ከፍተን ነበር። እንደፈራነው ታሰሬ የፊንፊኔው ስቱዲዮ ሲዘጋ የናይሮቢውን አጠናክረው ቀጠሉበት። ከእኔ በኋላ የመጡት የOMN አመራሮች በራሳቸው ስልት እና ሰትራቴጂ በመመራት ድርጅቱን ከውድቀት ታድገው ማስቀጠለ ችለዋል። ለነገሩ ከ2018 በኋላ OMN ቢቀጥለም ቢወድቅም የቆመለትን ዓላማ አሳክቷል። አስቀድሞ እንደተገለጸው OMN የተቋቋመው ለሕዝባችን ላሰብነው የሰላማዊ ትግል ልሳን ይሆን ዘንድ ነው፣ ይህንን ደግሞ ከዳር አድርሷል። በግሌ OMNን ለማቋቋም እና ለመምራት ስል ከሙሉ ሰኮላርሺፕ ጋር የተሰጠኝን ጥሩ የዩኒቨርሲቲ ትምህርት አቋርጫለሁ። የግል ኑሮዬም አደጋ ላይ ወድቋል፤ የስም ማጥፋት ዘመቻ ያለማቋረጥ ተደርጎብኛል። ይህ ሁሉ ቢደርሰብኝም እኔም ሆንኩ ባልደረቦቼ ሚዲያውን በማቋቋም እና በማሳደግ ውስጥ ለከፈልነው መሥዋዕትነት አንፀፀትም።

# 6.9 የትግል ወቅት ጉዞ ገጠመኞች

OMNን በመራሁባቸው አራት ዓመታት ብዙ ጊዜ ከሐሙስ ጀምሮ እስከ ሰኞ ገንዘብ ለማሰባሰብ እና ስብሰባዎች ላይ ለመሳተፍ ከሚኒሶታው ዉጪ እጓዝ ነበር። ሐሙስ ከቤት ወጥቼ ዓርብ ማታ፣ ቅዳሜ እና እሑድ የገቢ ማሰባሰቢያ አከናውኜ፤ ሰኞ ጠዋት ወይም እሑድ ማታ ተመልሼ የቀሩትን ሦሰት ቀኖች ቢሮ እሰራለሁ። በቀን የምተኛው ቢበዛ ሦሰት ሰዓት ሲሆን እሱም በሥራ ብዛት የተቆራረጠ ይሆናል። በዚህ የተነሳ በጣም ይደክመኝ ሰለነበር አንድ ቀን ሐሙስ እና ዓርብ ተምታቱብኝ። ወደ ቶሮንቶ ለመጎዝ አየር ማረፊያ ሄጀ ፓስፖርት ስሰጣቸው <ዛሬ በሚሄደው አውሮፕለን ትኬት የለህም> ሲሉን አለኝ ብዩ ክርክር ገጥሜ ማናጀሩ ተጠራ። ለካ መሄድ የነበረብኝ ሐሙስ ሲሆን እኔ የምክራከረው ዓርብ ሄጄ ነው፣ ሰሕተቴን አምኜ ሌላ ትኬት ገዛሁ። ትኬቱ ግን በቀጥታ ወደ ቶሮንቶ የሚወሰድ ሰላልነበር ከሚኔሶታ ኒው ዮርክ ወርጄ አውርፕላን መቀየር ነበረብኝ።

ኒው ዮርክ ደርሼ ከአውሮፕላኑ አንደወረደኩ ወደ ቶሮንቶ ለመሳፈር የአውሮፕላን መግቢያ በር ላይ መጠበቅ ጀመርኩ። የቶሮንቶ አውሮፕላን መጥቶ መንገደኞች ሲሳፈሩ አያለሁ፣ በዓይኔ እያየሁ ሁሉም ተሳፍረው አልቀው እኔ ብቻ ቀረሁ። የበረራ አሰተናጋጇ ስሜን በማይክራፎን ጠራች። ተሳፋሪዎች የሚቀመጡበት በታም መጥታ ተጣራች«። እየሰማሁ ግን መልስ አልሰጠሁም፣ አልተኛሁም ነገር ግን አልነቃሁም። ስሜ ሲጠራ ሕልም ውሰጥ አንዳለ ሰው ይሰማኛል።

አውሮፕላኑ ከሄደ በኋለ እንደመደንገጥ ብዬ ሮጬ በር ላይ ያለችውን ልጅ አናገርኳት። «ምን ሆነሃል? እዚሁ እያለሕ፣ ስምህን እየጠራሁ፣ አውሮርፕላኑ አመለጠህ ያምሃል እንዴ?» ብላ ተቆጣችኝ። ብዙ ቀን አንዳልተኛሁ ነግሬያት አዝናልኝ በቀጣዩ አውሮፕላን ያለ ክፍያ አሳፍራኝ ወደ ቶሮንቶ አቀናሁ።

ስለድካም እና አንቅልፍ ማጣት ከተነሳ አይቀር፡ ሰቱዲዮ እያለሁ እቃ የተሰረቀብንም ሌላ የማይረሳ ገጠመኝ ነው። የ#oromoProtests ጊዜ ውሎ እና አዳሬ ቢሮ ነበር። እዚያው OMN ቢሮ ፍራሽ አንጥፌ እተኛለሁ፤ ምግብ የማሞቅበት ኩሽናም እዚያው ነው። ጆዌ (ሀሰን) የሚባል ልጅ በበጎ ፈቃድ እንደ ጥበቃ (security) እና ሾፌር ሆኖ ያገለግለኛል፣ ምግብም የሚያመጣልኝ እሱ ነበር። ምሽት ላይ ሠራተኞቹ ሲወጡ እኔ ጋር ያድራል፡ እሱ ለሌላ ጉዳይ ከሄደ ብቻዮን ቢሮ ውሰጥ እሰራለሁ። ለእኔ እና ለስቱዲዮው ደኅንነት ሲባል ቢሮ ውሰጥ እና ውጪ ላይ የደኅንነት ካሜራ ተገጥሟል። ቢሮ ውሰጥ እና አካባቢው ላይ የሚካሄዱ ነገሮችን ቢሮዬ ውስጥ ባለው የኮምፒዩተር ስክሪን እመለከታለሁ። ጆዌ ከሌለ እና ሰው ቢሮ ከመጣ በካሜራው አይቼ አውቶማቲክ በሩን እከፍታለሁ።

አንድ ቀን ሰው መጥቶ፣ በሩን ከፍቶ ካሜራ፡ ኮምፒዩተር እና የመሳሰሉ እቃዎችን ሰርቆብን ሄደ። ለካ እኔ ቁጭ እንዳልኩ ጭልጥ ያለ እንቅልፍ ውስጥ ገብቼ ነበር። ሰውዬው እኔው ጋር

መጥቶ ካሜራው እንዳይቀርጽ አድርጎ፣ ሲገባ የተቀረጸውንም አጥፍቶ እና የስቱዲዮውን እቃ ሰርቆ ሄደ። የሚገርመው የሚሆነው ነገር በሙሉ በሰመመን ይታየኛል፣፡ የወሰድኩት ግን እንደ ሕልም ነው። ዘረፋውን የፈጸመው የእኛው ሠራተኛ ነበር፤ እርምጃ እንዳልወሰድ ደግሞ የቪድዮ ማሰረጃ እንዳይኖር አጥፍቶታል፣ትውስታዬ ደግሞ አንደ ሕልም ደብዛዛ ነው። በእርግጠኝነት የሆነውን ማስረዳት አልችልም፣ ለማስረዳት ብሞክር እንኳን «ንብረት ሲዘረፍ እያየህ ለምን ዝም አልክ?» በሚል የሚያምነኝ ሰው ውስን ነው ብየ ሰላሰብኩ ተውኩት። የስርቆቱ ክስተት የገዛ ሕይወቴ አደጋ ላይ እንዳለ ሰላመላከተኝ አካባቢውን ፖሊሶች በየሰዓቱ እየመጡ እንዲቃኙ እና ቢያንሰ አንድ ሰው ሁሌም ከአጠገቤ እንዳይጠፋ አደረግን።

አንድ ሌላ ከበረራ ጋር የተያይዘ ገጠመኝ ልጨምር። የኢሕአዴግ መንግሥት እና እኔን የሚቃወሙ ቡድኖች በእኔ ላይ ሲያደርጉ የነበረው የሰም ማጥፋት ዘመቻ በተወሰነው የማኅበረሰብ ክፍል ዘንድ ምን ያህል ሰለእኔ የተሳሳተ ግንዛቤ እንደፈጠረ የተረዳሁት አንድ ቀን ኒዋርክ (Newark) አውሮፕላን ጣቢያ ውሰጥ ሳልፍ ትውልደ ኢትዮጵያውያን የሆኑ ዕድሜያቸው ገፋ ያለ ባል እና ሚስት ባገኘሁበት ወቅት በተፈጠረ ክስተት ነው። ጥንዶቹ አዛውንቶች ከፊንፊኔ ተነሰተው ወደ ሎስ አንጀለስ (Los angeles) እየሄዱ ነበር። አውሮፕላኑ ከፊንፊኔ አምጥቶ ኒዋርክ ካወረዳቸው በኋላ ወደ ሎስ አንጀለስ የሚጓዙበት አውሮፕላን አመለጣቸው። በአጋጣሚ እኔም የራሴ በረራ አምልጦኝ ቀጣዩን በመጠባበቅ ላይ ሳለሁ ቡና ልጠጣ ካፌ ሳፈላልግ፣ አዛውንቶቹ ከኤርፖርቱ አሰተናጋጆች ጋር በቋንቋ መግባባት አንደቸገራቸው አሰተዋልኩና ወደ እነሱ ጠጋ ብዬ እንድተረጉምላቸው ጠይቄ ፈቀዱልኝ። የተፈጠረውን ችግር ተረድቼ ሌላ በረራ እንዲያዝላቸው አድርጌ የበረራ ሰአቱ እሰኪደርሰ ምሳ ጋብዢያቸው ስናወራ ቆየን።

ወቅቱ የቄሮ ትግል ተቀጣጥሎ ሀገሪቷን የሚንጥበት ነበር። ሁለቱም ሰለ ሀገር ውስጥ ሁኔታ ሲያወጉኝ "ቄሮ የሚባል እኩይ ኃይል" በሀገሪቱ ላይ እያደረሰ ያለውን አደጋ ይነግሩኝ ጀመር። እነዚህን እኩይ ኃይሎች ጀዋር ሙሐመድ የሚባል እዚህ ሀገር (አሜሪካ) የሚኖር አሸባሪ እንደሚያሰማራ በቁጣ ነገሩኝ። ፈጣሪ እንዲያጠፋውም ደጋግመው ረገሙት። የአሜሪካ መንግሥት ማስቆም ባለመቻሉም ቅሬታ አቀረቡ። ጀዋርን አውቀው እንደሆነ ሲጠይቁኝ ፖለቲካ ብዙም እንደማልከታተል እና ስሙን ግን ሰምቼው እንደማውቅ ነገርኳቸው። ይህን ያደረኩት ጀዋር መሆኔን ይቅርና በቅርበት እንደማውቀው እንኳን ከገለጽኩ ንግግራቸውን ሊያቋርጡ ስለሚችሉ እና ነጻ ሆነው በማውራት እየተካሄደብኝ የነበረው ፕሮፓጋንዳ የፈጠረውን አመለካከት የበለጠ መስማት ሰለፈለግሁ ነበር።

እንዲሁ እያወራን ቆይተን የበረራ ሰዓታቸው ሲደርስ ወደ መግቢያ በር ወስጄ ስሜ አና ስልክ ቁጥሬ ያለበትን ካርድ (ቢዝነሰ ካርድ) ሰጥቻቸዋለሁ በጉዞው ወቅት ችግር ካጋጠማቸው እንዲደውሉልኝ ነገርኳቸው። ትንሸ ወደ ፊት እንደተራመድኩ ከጀርባ ጠሩኝ። ባልየው የሰጠሁትን ካርድ እየተመለከተ "ይሀ ያንተ ሰም ነውን" አለኝ። እኔም ፈገግ ብዬ በቅንድቤ አረጋገጥኩለት። እርሱም "ሰምህ ቅድም ሰለሱ ካወራነው ሰው ጋር ይመሳሰላል? " ሲል ግራ በተጋባ ስሜት ጠየቀኝ። እንደገና ጭንቅላቴን ነቅንቄ አረጋገጥኩለት።

ቀጥሎም ስሞቹ እንዴት እንደዚሀ ሊመሳሰሉ እንደቻሉ ጠየቀኝ። "ቅድም ሰለሱ ያወራነው ጀዋር እኔው ነኝ። ብዮ ፈገግ አልኩ። ድንጋጤ እና ጥርጣሬ በተቀላቀለ ስሜት "በፍፁም

ሊሆን አይችልም" አሉ። "አትደንግጡ። ቅድም ያወራነው ጀዋር የፖለቲካው ነው። ይህ የምትመለከቱት ደግሞ እውነተኛው የግል ማንነቱ ነው። በሁለቱ መሃል ልዩነት ሊኖር ይችላል" አልኳቸው። እነሱ ግን እያልኩ ያለሁት ነገር የገባቸው አይመስልም። እየቀለድኩ ከድንጋጤ ስሜት ላሰወጣቸው ሞክሬ ሁለቱንም አቅፌ ተሰናብቻቸው ሄድኩ። ሎስ አንጀለስ ደርሰው ለልጆቻቸው የሆነውን ሲነግሯቸው ልጆቹ ደውለው እናት አና አባታቸውን ሰለረዳሁ አመስግነውኝ ሰላሰቀየሙኝ ደግሞ ይቅርታ ጠየቁን። እኔ ግን ወላጆቻቸው የተናገሩት ከሚዲያ የሚሰሙትን እንጂ በእኔ ላይ በግል ጥላቻ ኖሯቸው ስላልሆነ አንዳልተከፋሁ እና ምንም ይቅርታ እንደማያስፈልግ አረጋግጥኩላቸው። ያደረኩላቸው እርዳታም ሌላ ሰው እናቴ ተቸግራ ቢመለከት ሊያደርግ የሚችለውን እንደሆነ ነገርኳቸው። ከዚያ በኋላ ለረጅም ጊዜ በተደጋጋሚ እየደወሉ ጤንነቴን ይጠይቁኝ ነበር።

በትግሉ ወቅት ከተለያዩ ቡድኖች እና መንግሥታት ጫና ይደረግብኝ ነበር። እኛም ገና ከጅምሩ እንዲህ ዓይነት ጫና ሊመጣ እንደሚችል ስለገመትን፣ የትግል መስመራችንን ሊያሰት ለሚችል ተጽዕኖ ተጋላጭ እንዳንሆን ቅድመ ጥንቃቄ እናደርጋለን። ከጥንቃቄ እርዎጃዎቹ ውሰጥ ዋናው የOMNም ሆነ ሌላ ወጪ ሙሉ በሙሉ ከዲያስፖራው የኦሮሞ ማኅበርሰብ በምንሰበሰብው ገንዘብ እንዲሆን በማረጋገጥ፣ በፋይናንሰ ምክንያት በማንኛውም ድርጅትም ይሁን መንግሥት ላይ ተለጣፊ እንዳንሆን መጠንቀቅ ነበር። ከውጪ ኃይሎች ይቅርና ከኦሮሞ የፖለቲካ ድርጅቶች ወይም ከእነሱ ጋር ጠንካራ ትሰስር ካላቸው ባለሃብቶች እንኳን ገንዘብ ላለመቀበል እንጠነቀቃለን።27 ይህ በሕዝባችን መዋጮ ብቻ የመንቀሳቀሰ ውሳኔ፡ የሕዝባችንን ጥቅም ብቻ ያማከለ ትግል ለማካሄድ በማስቻል ለስኬታችን ጉልህ አሰተዋጽዖ አድኋል።

ከዚሁ ጋር በተያያዘ በየዘመኑ የሚነሱ የኢትዮጵያን መንግሥት የሚቃወሙ ኃይሎችን በመደገፍ የምትታወቀው ግብጽ እንደሌሎች የፖለቲካ ድርጅቶች እና ሚዲያ ተቋማት ሁሉ OMNንም የጥቅሟ አራማጅ ለማድረግ ሞክራለች።

ከአሜሪካ ውጪ ባሉ አንደ አምስተርዳም፣ ሜልቦርን አና ሎንዶን ባሉ ከተሞች የOMNን ጣቢያዎች ለመክፈት ስንወስን፣በካይሮም ለማቋቋም አሰብን። ካይሮን የመረጥንበት ምክንያት ብዙ ጋዜጠኞች በስደት እዚያ ሰለሚኖሩ እና የኑሮ ውድንቱ የተሻለ በመሆኑ ወጪ ለመቆጠብ ነበር። ከዚሁ በመነሳት፡ እዚያ ባሉ የኦሮሞ ስደተኞች በኩል ፈቃድ ጠይቀን ተፈቅዶልን ሥራ ጀመርን። ከተወሰነ ጊዜ በኋላ ግን በሚዲያው የፕሮግራም ይዘት ላይ በቀጥታ እና በተዘዋዋሪ መንገድ ጫና የማድረግ ሙከራ ጀመሩ። አሻፈረኝ ብንልም የሚዲያውን ሽፋን እና ተደራሽነት የበለጠ ለማስፋት እንዲቻለን ዳጎሰ ያለ የገንዘብ ድጋፍ ማድረግ አንደሚፈልጉ ከእነሱ ጋር ትሰሰር ባለቸው ሰዎች በኩል ነገሩኝ። ይህኛው ማማለያ አልሰራ ሲላቸው ጋዜጠኞችን ማዋከብ እና የጣቢያውን ሥራ አስኪያጅ በተደጋጋሚ ማሰር ተከተለ።

በዚሁ መሀል የሚዲያው የምሰረታ በዓል ሲከበር በሌሎች ከተሞች በሚዘጋጁ መድረኮች ላይ

27 ሜዲያው የገንዘብ እጥረት በጋጠመው አንድ ወቅት የOMN ቦርድ አባል የሆነ ሰው ያለማናጅመንት እውቅና ከአንድ የኦሮሞ ፖለቲካ ድርጅት 5000 ዶላር ተቀብሎ ወደ OMN አካዉንት ያስገባል። ቆየት ካለ ጊዜ በኋላ OMN ያንን የፖለቲካ ድርጅት ያስቀየመ ዘገባ ባቀረበበት ወቅት፣ የቦርድ አባሉ ድርጅቱ የሚዲያው ባለውለታ ወሆኑን እና ማስከፋት እንደሌለብን በምክንያት ሲያሰረዳ ያንን የገንዘብ ልገሳ ይጠቅሳል። እኔም የቦርድ አባሉ ያን ገንዘብ ማስገባቱ እና አሁን ደግሞ በሚዲያው ዘገባ ላይ ሚና ለመፍጠር ያደረገው ሙከራ ከፖለቲካ ድርጅት ገንዘብ ላለመቀበል አስቀድመን የወሰንበትን ምክንያት ትክክለኛነት ያረጋገጠ መሆኑን አበክሬ ተናገርኩ። ከዚያም ገንዘቡ ለለጋሹ ተመላሽ እንዲሆን ታዘዘ።

እንደምሳተፈው ሁሉ፡ ለካይሮው ዝግጅትም ተጋብዘን ፕሮፌሰር ሕዝቅኤል ገቢሳ ቀድሞኝ ከደረሰ በኋላ ዝግድቱ ሁለት ቀናት ሲቀሩት እንዳይከናወን መታገዱን ሰማን።

እኔም የቆረጥኩት ትኬት ከሚባክን ዝግጅቱ ቢቀርም ደርሼ ጋዜጠኞቹን እና ኮሚኒቲውን አበረታትቼ ልመለስ ወደዚያው አቀናሁ። ነገር ግን ካይሮ ኤርፖርት እንደደረስኩ ያልጠበኩት ድራማ አጋጠመኝ። ለኢሚግሬሽን ሠራተኛው ፓስፖርቴን ሥሠጥ አንድ ሁለት ጥያቄ አንደጠየቀኝ ወታደሮች መጥተው ከጎኔ ቆመው ለተጨማሪ ጥያቄ እንደሚፈልጉኝ ነግረውኝ ወደ አንድ ትንሽ ቢሮ ወሰዱኝ።

ሕገ-ወጥ ሚዲያ በሀገራቸው ውሰጥ አቋቁሜ በሸብር ወንጀል ላይ እንደተሳተፍኩ በመናገር፣ ለረጅም ጊዜ በሀገራቸው ከምታሰር እና ለኢትዮጵያ መንግሥት ተላልፌ ከመሰጠት አንዱን እንድመርጥ እየተፈራረቁ በኃይለ ቃል ደነፉብኝ። እኔ ግን ምንም ወንጀል አንዳልፈጸምኩ እና ሚዲያውም ሕጋዊ ፈቃድ እንዳለው በመከራከር፣ የአሜሪካ ዜጋ ሆኜ ሳለ ለኢትዮጵያ መንግሥት ተላልፌ የምሰጥበት አግባብ አንደሌለ ነገርኳቸው። እንሱ ግን ከየመን ታፍኖ ለኢትዮጵያ መንግሥት ተላልፎ የተሰጠውን የግንቦት ሰባቱን አንዳርጋቸው ጽጌን ዜጋዋ ቢሆንም እንግሊዝ ምንም እንዳላደረገችለት በመግለጽ እኔንም አሜሪካ ምንም አንደማትረዳኝ አስጠነቀቁኝ።

የሚደነፉት ወታደሮች ወጡና ሲቪል የለበሰ ጎልማሳ ገብቶ ከመንግሥታቸው ጋር ለመተባበር ብስማማ ነገሮች በቀላሉ እንደሚፈቱልኝ ያዘነልኝ በሚመስል ድምጽ መከረኝ ፣ እኔ ግን በአቋሜ ጸናሁ። እምቢ ካልክ የራሰሀ ጉዳይ ብሎ ሲሄድ ከነበርኩበት ቢሮ አውጥተው ብዙ መንገደኞች ታጭቀው ወደታሰሩበት እሰር ቤት ወረወሩኝ። እዚያም ከእስረኛቹ መካከል ሦሰቱ ለመደብደብ አና ለመግደል እየዛቱ ያሰፈራሩኝ ጀመር። እነዚያ ገላጋይ መስለው የገቡ ሰዎች ደግሞ ቀደም ሲል ሌሎች እስረኛ አጠገባቸው ክፉ ጥቃት እንደደረሰባቸው ነግረውኝ፣ እንደምንም ብዬ በመውጣት ሕይወቴን እንዳተርፍ መከሩኝ። እኔ ግን ሸሂድ (መስዋትነት) ለመሆን (ለሞት የተዘጋጀሁ) ታጋይ መሆኔን በመግለጽ የመሸበር ገፅታ ሳላሳይ፣ የስጋት አና የንዴት ስሜቴን ዋጥ አድርጌ ኮሰተር ባለ ፊት ተጋፈጥኳቸው።

የደረስኩት እኩለ ሌሊት አካባቢ ሲሆን የጠዋቱ አዛን በመሰማቱ ሌሊቱ እየነጋ መሆኑን እሰክተረዳሁበት ጊዜ ድረሰ በዚህ መልኩ ሲያዋክቡኝ ቆይተው፣ድንገት ከእሰር ቤቱ አስወጡንና ፊታቸው አዲስ የሆኑ ሰዎች ተረክበውኝ በስህተት መታሰሬን በመግለጽ ቦርሳዬን እና ፓሰፖርቴን መልሰው አለቆቻቸው በአካል ይቅርታ ሊጠይቁኝ እንደሚፈልጉ ነግረውኝ አንድ ዘመናዊ የኮንፈረንሰ ክፍል አስገቡኝ። እዚያም ሦስት ሱፍ የለበሱ ሰዎች ገብተው ይቅርታውን ከደገሙ በኃላ ምግብ እና ሻይ እንዲመጣለኝ አዘዙ። ከመካከላቸው አንዱን በሚዲያ እንደማውቀው ስነግረው፣ ደንገጥ ብሎ ተመሳሰሎብኝ እንጂ ላውቀው እንደማልችል ነገረኝ ፤ ማንነቱን እየደበቀ መሆኑ ስለገባኝ ተውኩት።

የይቅርታ ሸንገላው ካለቀ በኋላ እየተፈራረቁ በጥያቄ ላይ ጥያቄ ያዥጎደጉዱብኝ ጀመር። ለሰለስ ባለ አቀራረብ ጀምረው እያጠናከሩ ሄደው ወደ ማፋጠጥ ተሸጋገሩ። መጀመሪያ አንደያዙኝ ያቀረቧቸውን ውንጀለዎች ትተው ከፍ ያሉትን ይዘው ብቅ በማለት በሀገራቸው ተካሂዶ በነበረው ሕዝባዊ አብዮት ተሳትፎ እንደነበረኝ ፡ አመጹን የመሩትን ወጣቶች ሳሰለጥን እንደነበር መረጃው እንዳላቸው ነገሩኝ። ይሀንን ያደረኩትም በሀገራቸው ውሰጥ

ቀውስ በመፍጠር፣ በዓባይ ውኃ ላይ የግብጽን ጥቅም ለመጉዳት በማሰብ መሆኑን፣ ይህን ለማሳካትም ከኢትዮጵያ መንግሥት ጋር እንደምሰራ ተናገሩ። እንደማስረጃም በዓባይ ውኃ ጉዳይ የጻፍኳቸውን እና በሚዲያ የተናገርኩትን አቀረቡ28። ግብጽ የኦሮሞን ሕዝብ የነጻነት ትግል የምትደግፍ ሆና ሳለ ከትግራይ ጨቋኝ አገዛዝ ጋር መቆሜ እንዳሳዘናቸው ነገሩኝ። ከዚያ በፊት በሄድኩባቸው ሀገራት ስብሰባ ላይ ሲጋራ ሲጨስ አይቼ ስለማላውቅ፣ ግብጾቹ ጠያቂዎቼ እንደዘ ባማረ ዘመናዊ የስብሰባ አዳራሽ (executive board room) ውስጥ በላይ በላዩ እየለኮሱ ሲያጨሱ ሳይ ዘገነነኝ።

መልስ እንድሰጥ ዕድል ሲሰጡኝ፣ በሀገራቸው አመጽ ማስነሳት ስለተባለው ጉዳይ ከተለያዩ ሀገራት የተውጣጡ ወጣቶችን በሰላማዊ ትግል ስልት ሥልጠና ላይ ማሳተፌን በመግለጽ፣ ከሰልጣኞቹ መካከል ግብጾች ይኑሩ አይኑሩ እንደማላስታውስ፣ ሥልጠናውም ለጠቅላላ እውቀት እንጂ በአንድ ሀገር ላይ ያነጣጠረ እንዳልነበረ ገለጽኩ። በአረብ ስፕሪንግ አመጽ ወቅት በሚዲያ ሳቅርብ የነበረውን ትንታኔ አምጥተው ፊቴ ሲደቅኑ ደግሞ ይሄ በሚዲያዎች ተክፍሎኝ ሳደርግ የነበረ ሙያዊ ሥራ መሆኑን እና የግብጽን ብቻ ሳይሆን የሊቢያን፣ ሲሪያን፣ ቱኒዚያን እና ሌሎችን ስተነትን እንደነበር ገለጽኩ።

በናይል ወንዝ ጉዳይ በጻፍኩት እና በተናገርኩት ጉዳይ ግን ቆፍጠን ያለ መልስ ሰጠኋቸው። የተፋሰሱ ሀገራት ሁሉ ፍትሃዊ በሆነ መልኩ የመጠቀም መብት እንዳላቸው ከልቤ የማምንበት ጉዳይ እንደሆነ ነገርኳቸው። በተለይ ኢትዮጵያ አብዛኛው የወንዙ ውኃ የሚመነጨባት ሀገር ሆና ሳለ ዝቅተኛዋ ተጠቃሚ መሆኗ፣ ድርሻዋን ለማሳደግ ስትሞክር ደግሞ ለመከልከል መሞከር አግባብነት እንደሌለው አስተያየቴን ሰጠሁ። እነሱም 'ግብጾች ኢትዮጵያ አትጠቀም የሚል አቋም እንደሌላቸው፣ የሚቃወሙት ሕጋዊ ስምምነቶችን በመጣስ የግብጽን ህልውና ለአደጋ ማጋለጧን ነው' እሉ። ለዚህም መልስ ስሰጥ የተጠቀሱት ስምምነቶች በቅኝ ገዥዎች ፍጹም የበላይነት የተጫኑ እንጂ በተፋሰሱ ሀገራት መካከል በተደረገ ነጻ ድርድር ስምምነት ላይ የተደረሰባቸው ስላልሆኑ ዛሬ ላይ ተቀባይነት ሊኖራቸው እንደማይችል ተናገርኩ። "እናንተስ ብትሆኑ በኮሎኒያል ጊዜ በተደረገ ስምምነት ሲተዳደር የነበረውን ስዊዝ ካናል ስምምነቱን በመጣስ አልነበረም አውሮፓውያኑን አባርራችሁ የጠቀለላችሁት?" በማለት መከራከሪያዬን ለማጠናከር ሞከርኩ።

የኦሮሞን ትግል ከዚህ በፊት ከመደገፋቸው ጋር አያይዘው ላነሱት ጥያቄ፣ እውነትም የኦሮሞ ሕዝብ የተጨቆነ ቢሆንም፣ የዓባይ ተፋሰስ ጉዳይ ከውስጣዊ የብሔር እሰጣገባ በላይ የሆነ ሀገራዊ ጉዳይ መሆኑን ከዚህ በፊት በጻፍኩት እና አሁን እነሱ እንደማስረጃ ባቀረቡት ጽሑፍ

28 የሕዳሴ ግድብን መገንባት የተጀመረ አካባቢ አንዳንድ በውጪ ሀገር ያሉ የተቃዋሚ መሪዎች እና አንቂዎች ሲያጣጥሉት ሳይ፣ ዓባይ ትለቅ ሀገራዊ ጉዳይ በመሆኑ የውስጣዊ የፖለቲካ ልዩነት ሳይገድበን በአንድነት መቆም እንደሚያስፈልግ የሚተነትን ጽሑፍ እሳትሜ ነበር። Mohammed, Jawar. "Why Oromos Should Care about the Nile Politics." OPride, 16 Dec. 2010, www.opride.com/2010/12/16/why-oromos-should-care-about-the-nile politics/

የመጀመሪያውን ጽሑፍ እንዳሳተምኩ፣ እንዳንድ ሰዎች ጽሑፉ ለኢትዮጵያ መንግሥት ያደላ እና ግብጽን የሚያስከፋ በመሆኑ ትግሉን እንደሚጎዳ በመግለጽ ላቀረቡት ትችት " የናይል ጉዳይ ኦሮሞን ለምን ይመለከተዋል?" በሚል ርዕሰ መልስ ሰጥቼ ነበር።

Mohammed, Jawar. "Ethiopia's Internal Cohesion Key to Advancing Interest in the Nile. OPride, 9 Dec. 2010, www.opride.com/2010/12/09/ethiopias-internal- cohesion-key-to-advancing-interest-in-the-nile/

ውስጥ ያለውን መከራከሪያ ደገምኩት። ከኢትዮጵያ የሚፈሰው የናይል ውኃ አብዛኛው መነሻው ከኦሮሚያ የሚነሱ መጋቢ ወንዞች መሆኑን በመጥቀስ፣ ማንኛውም የኦሮሞ አመራር የዛሬውን የኢትዮጵያን አገዛዝ ለመጣል ከግብጽ ጋር ቢተባበር እንኳን፣ ነገ ሥልጣን ሲይዝ ዓባይ ወንዝን በተመለከተ አሁን ካለው መንግሥት የጠነከረ እንጂ የላላ አቋም ሊኖረው እንደማይችል ገለጽኩ። መፍሔውም ሁሉንም የተፋሰስ ሀገራትን ክፉኛ የማይጎዳ እና ፍትሃዊ ክፍፍልን የሚያረጋግጥ ስምምነት ላይ መድረስ እንደሆነ ነገርኳቸው። በዚህ መልኩ ለሰዓታት ስንዳረቅ ቆይተን ከቀትር በኋላ ወደመጣሁበት ሀገር እንድመለስ ወስነው በአመጣኝ አየር መንገድ መልሰው ሰደዱኝ። ከዚያ በኋላም ገረሱ ቱፋ፣ ሳሊሀ ሳሚ እና ሌሎች ከOMN ጋር ግንኙነት የነበራቸውን ሰዎች በካይሮ ኤርፖርት ሲያልፉ ማዋከብ፣ ማሰር እና ወደመጡበት ማባረሩ ቀጠለ።

ከዚሁ ከናይል ፖለቲካ ጋር በተያያዘ ሌላም ክስተት ነበር። የቄሮ ትግል መገባደጃ አካባቢ የሕወሓት ሊቀመንበርና ምክትል ጠ/ሚ የነበረው ዶ/ር ደብረጽዮን ገብረሚካዔል የኮምፒውተር መረጃዎች ተሰብረው በውስጡ የነበሩ መረጃዎች በሙሉ እጃችን ገብተው ነበር። ዶ/ር ደብረጽዮን በወቅቱ ከሳይንስና ቴክኖሎጂ ሚኒስቴርነት በተጨማሪ የኢትዮጵያ ኤሌክትሪክ ኃይል የቦርድ ሰብሳቢ ስለነበር የታላቁ ሕዳሴ ግድብ አፈጻጸምን የተመለከቱ አጠቃላይ ሪፖርቶች በየሳምንቱ ይቀርቡለት ነበር። መረጃው የመጣው እንግሊዝ ከሚገኝ አጋራችን ሲሆን የደረሰን ፋይል ከተለያዩ አካላት ጋር ከተደረጉ ፖለቲካ ነክ የኢሜል ልውውጦች በተጨማሪ ግድቡንና የዓባይ ጉዳይን የሚመለከቱ ሰነዶችን ያካተተ ነበር።

የሚኒስትሩ ኮምፒውተር መሰበሩ አገዛዙን ለማዳከም እና ትግሉን ለማፋፋም በጊዜው ጠቃሚ የነበረ ቢሆንም፣ ከፍተኛ ጥበቃ የሚሹ የሕዳሴ ግድብ ፕሮጀክት ሀገራዊ ምስጢሮች እንዲህ በቀላሉ ሊሰበር በሚችል የኮምፒውተር ሲስተም መያዙ በጣም አሳሰበን። እነዚህ ሚስጢራዊ ሰነዶች ግብጽ እጅ ቢገቡ የሚያስከትለው ሀገራዊ አደጋ በእጅጉ ስላሰጋን፣ የሕዳሴው ዶሴ ለወትሮው ከመንግሥት ሾልከው የሚወጡ መረጃዎችን ለማካፍላቸው የትግል ጓዶቼ እንኳ እንዳይደርስ መጠንቀቅ ነበረብን። በወቅቱ ለትግሉ አጋዥ የሆኑ ምስጢራዊ የመንግሥትና የፓርቲ ሰነዶች ይደርሱት ከነበረውና ከእኔ ጋር መረጃና ሐሳብ ይለዋወጥ ከነበረው ሚካኤል ጨቡድ ማሞ ጋር ተወያይተን እነዚህ ሰነዶች በአጠቃላይ ተመልሰው ሊገኙ በማይችል መልኩ እንዲወድሙ አደረግን።

የወቅቱ የኢትዮጵያ ጠቅላይ ሚኒስተር ኃይለማርያም ደሳለኝ ግብጽ "ብር በጆኒያ" እንደምትሰጠን በሚዲያ ወጥቶ ቢወነጅለንም፤ እነሱም በተለያዩ መንገዶች ሊያማልሉን ቢሞክሩም፣ ለOMNም ሆነ ለሌላ ሥራ ሰባራ ሳንቲም ሳንቀበል ትግሉን በድል ማጠቃለል ቻልን።

# ክፍል ሰባት - ትግል አና ድል

## 7.1 ሙከራ አንድ፡ #BoycottBedele

አንድን አምባገነን ሥርዓት በሰላማዊ የትግል ስልት ለመቀየር ወደ ሙሉ ግብግብ (full scale confrontation) ከመግባት በፊት፣ መጀመሪያ ሕዝቡን የማነቃቃት ሥራ መሥራት ያስፈልጋል። በመቀጠል ቀለል ያሉ ጥያቄዎችን ማንሳት እና ትናንሽ ዘመቻዎችን (campaigns) ማካሄድ ተገቢ ነው። በሰላማዊ ትግል ለውጥ መጥቶ በማይታወቅበት ሀገር ውስጥ ሕዝቡ በሰላማዊ ስልት ውጤታማነት ላይ ጥርጣሬ ይኖረዋል። በቀላሉ ማሸንፍ የሚቻሉ ቀለል ያሉ ጥያቄዎችን ማንሳት እና በአጫጭር ዘመቻዎች ማሰመለስ ሕዝቡ ከሰላማዊ ትግል ጋር እንዲለማመድ እና ውጤታማነቱን በማየት ተሰትፎውን እንዲያጠናክር አጋዥ ነው። እኛም በሙሉ አቅማችን ወደ ቄሮ ትግል ከመግባታችን በፊት፡ አነስ ያሉ ዘመቻዎችን በማካሄድ ሕዝቡን ከሰላማዊ ትግል ጋር እያዕተዋወቅን ሄድን። ከእነዚሀ ዘመቻዎች ውስጥ #boycottbedele አንዱ ነበር።

የቄሮ ሰለማዊ ትግል በአንድ ጊዜ ከሁለት ኃይሎች ጋር የተደረገ ፍልሚያ ነበር። በአንድ በኩል የሕወሐት/ኢሕአዴግ መንግሥትን እየተጋፈጠ፣ በተመሳሳይ ጊዜ በጎን ከአማራ የፖለቲካ ቡድኖች ጋር ተፋልሟል። ሕወሓት/ኢሕአዴግ የፖለቲካ ሥልጣንን በእጁ የጨበጠ ኃይል እንደመሆኑ የኦሮሞን ሕዝብ ከላይ ወደታች ሲጨቁን፣ ቄሮ ደግሞ ሥርአቱን ለመለወጥ ከታች ወደ ላይ ይታገላል። በተመሳሳይ ጊዜ የአማራ ኃይሎች ከኦሮሞ ትግል ጋር የርዕዮተ-ዓለም ቅራኔ ስላላቸው በጎን (horizontally) ሲከፍቱበት የነበረውን ዘመቻ መከላከል ነበረበት። ለውጡ ሊመጣ አካባቢ "ኦሮማራ"። በሚል ስያሜ ለአጭር ጊዜ ታክቲካዊ ጥምረት (tactical alliance) የተፈጠረ ቢሆንም፣ የአማራ የፖለቲካ ኃይሎች ከመንግሥት ባልተናነሰ ለረጅም ጊዜ በቄሮ ትግል ላይ የፕሮፓጋንዳ ዘመቻ አካሂደዋል።

በኦሮሞ እና በአማራ የፖለቲካ ኃይሎች መካከል አከራካሪ ከሆኑ ጉዳዮች ዋናው የታሪክ ትርክት አጀንዳ ነው። ኦሮሞው ቀደም ብለው ሥልጣን ላይ የነበሩ የአማራ ገዢ ቡድኖች በድለውኛል ይላል፣ የአማራ ኃይሎች ይህንን ይክዳሉ። የሚክዱበት ምክንያትም የትላንት መሪዎች የፈጸሙትን በደል ማመን ዛሬ ላይ እንደ ኦሮሞ ያሉ ብሔሮች የሚያነሱትን ጥያቄ ተቀባይነት እንዲያገኝ ሰለሚያደርግ፤ ሀገሪቷ የሥልጣን ክፍፍል ላይ ለአማራው አሉታዊ ውጤት ያስከትላል ከሚል ግምት ነው። ከዚሁ እሳቤ በመነሳት ከቅርብ ጊዜ ወዲሀ የትላንት በደልን ከመካድ አልፈው ኦሮሞ የሚከስሳቸውን ነገስታት ማወደስ አበዙ። ከእነዚሀ ውዳሴዎች መካከል የምኒሊክን ሚና በአዲሰ ለመሳል (image rehabilitation)

ሲደረግ የነበረው ሥራ አንዱ ነው።

የምኒሊክን ሰብዕና በአዲስ የመገንባት ሙከራ ዕውቁ የአማርኛ ሙዚቀኛ ቴዲ አፍሮ (ተዎድሮስ ካሳሁን) "ጥቁር ሰው"፣ ብሎ በዘፈን አቀረበው። ይህ ደግሞ በኦሮሞ እና በአማራ የፖለቲካ ኃይሎች መካከል በታሪክ ጉዳይ ሲካሄድ የነበረውን ውዝግብ አጋጋለው። የዘፈኑ አላማ የሕዝቦች የጋራ ገድል የሆነውን የአድዋ ድል ተጠቅሞ የምኒሊክን በጎ ጎን አግዝፎ በማቅረብ፡ ንጉሡ የሚከሰሰባቸውን ወንጀሎች ማሳነስ ነበር።

ቴዲ ከፍተኛ ተደማጭነት ያለው ዘፋኝ ስለሆነ ምኒሊክን መልሶ ፃድቅ በማድረጉ ፕሮጀክት ትልቅ አስተዋጽዖ ሊኖረው ይችላል። ዘፈኑ ትልቅ ገንዘብ ወጪ ተደርጎበት ማራኪ በሆነ መልኩ ስለተሠራ ብዙ ሰዎች፣ በተለይ ወጣቶች፣ የግጥሙን መልዕክት ሳይረዱ በዜማው ብቻ በመሳብ ዘፈኑ ለታቀደለት የአእምሮ ማጠብ (brainwash) የሚጋለጡበት አጋጣሚ ነበር። የቀድሞ ነገስታት በኦሮሞና በደቡብ ብሔሮች ላይ ያደረሱትን በደል መሸፋፈን ከተቻለ የብሔር ትግል ትርክት (narrative) ቅቡልነት አይኖረውም።

በ2013 የፈረንጆች ዓመt መገባደጃ ላይ ዘፈኑ የኦሮሞ እና የአማራ ፖለቲካ ጎራዎችን እያከራከረ ባለበት ወቅት ቴዲ ለአንድ የሀገር ውሰጥ መጽሔት ቃለ-ምልልስ ሰጠ። ምኒሊክ በኦሮሞ እና በደቡብ ብሔሮች ላይ ያደረገው ወረራ <ቅዱስ ጦርነት ነውን> ተብሎ የመጽሔቱ የፊት ገጽ ሆኖ በኦንላይን ተሰራጨ።

ይህ አባባል ዘፋኙ ለምኒሊክ ያለውን አድናቆት ለመግለጽ ብቻ ሳይሆን በብሔሮች ላይ ያካሄደውን አስከፊ ጦርነት አንደ ቅዱስ ድርጊት ለማወደስ የተሠራና ግልጽ የፖለቲካ ዓላማ ያለው እንደሆነ አመላከተን። እኛም ይህን በኦሮሞ አና በሌሎች ጭቁን ሕዝቦች የትግል ታሪክ ላይ ያነጣጠረ ድርጊት ከኢንተርኔት የሐሳብ ክርክር ባለፈ መሬት ላይ በሚደረግ ተግባራዊ እርምጃ መመከት የሚያስችለንን ዕድል አገኘን። ይኸውም ቴዲ በወቅቱ በብዙ የኢትዮጵያ ዋና ዋና ከተሞች ትልልቅ ኮንሰርቶች ለማዘጋጀት የነበረውን እቅድ ማክሸፍ ነው።

ኮንሰርቶቹ ሄኒከን (heineken) በሚባል የቢራ አምራች ድርጅት ስፖንሰር የሚደረጉ ሲሆን፡ ድርጅቱ የበደሌ ቢራ ፋብሪካን በመግዛት በባለቤትነት ያከፋፍላል። ሰለዚሀ ለዘፋኙ መልዕክት ያለንን ተቃውሞ ለማሳየት እና ኮንሰርቱን ለማሰቆም በሁለት መንገዶች እርምጃ ለመውሰድ እቅድ አወጣን። አንደኛው ኮንሰርቱ በታቀደባቸው ከተሞች እንዳይካሄድ መሬት ላይ ዘመቻ (grassroot campaign) ማካሄድ ሲሆን፣ ሁለተኛው ደግሞ ሰፓንሰርነቱን ለማሠረዝ በሄኒከን ላይ ዘመቻ ማድረግ ነበር። ለመጀመሪያው እቅድ ወጣቶች የከተማ አሥተዳደሮቹ ጋር በመሄድ አዳራሽም ሆነ ስታዲየም እንዳይፈቀድ እንዲያደርጉ አደረግን። ለሁለተኛው ደግሞ በበደሌ ቢራ ላይ ያነጣጠረ የተቀናጀ የማኅበራዊ ሚዲያ ዘመቻ ማካሄድን መረጥን።

ለዚሀም ፌሰቡክ ላይ #Boycottbedele የሚል ዘመቻ አቀጣጠልን። ሀገር ውስጥ ሰዎች በደሌ ቢራ አለመጠጣታቸውን የሚያሳዩ የፎቶ አና የቪዲዮ ማስረጃዎችን ይልኩልናል። ለምሳሌ ወጣቶች ወደ ግሮርሰሪዎች በመሄድ ከተደረደሩ የቢራ አይነቶች ውሰጥ በደሌን በመተው ሌሉቹን ያዛሉ። በደሌ ሲሰጣቸው በቃላት እያጣጣሉ በቪድዮ ይልኩልናል፣እኛ ደግሞ በማኅበራዊ ሚዲያ ላይ እንለጥፋን። በደሌ ቢራ አሮሚያ ውሰጥ ያለ እና በብዛትም እዚያው ክልል የሚጠጣ ሰለሆነ ለተቃውሞ ዘመቻው የተጋለጠ ነበር። በዘመቻው ተጠቃሚዎችን ብቻ ሳይሆን አከፋፋዮችን አሳተፍን። በተለይም በኦሮሚያ ዞኖች የሚገኙ አከፋፋዮች ፊንፊኔ

የሚገኘው የሄኒከን ዋና መሥሪያ ቤት በመደውል እየተካሄደ ያለው ዘመቻ የበደሌ ምርቶች ሽያጭ ላይ ተጽዕኖ እያሳደረ መሆኑንና ፈጣን መፍትሔ ካልተሰጠ ስርጭታቸውን ለማቆም እንደሚገደዱ ያስጠነቅቃሉ።

በውስጥም በውጭም በተቀናጀ ሁነታ የሚካሄደው ዘመቻ እየተጠናከረ ሄዶ የሀገሪቱ አብይ የጸጥታ አጀንዳ ሆነ። በዘመቻው ወቅት አንድ ጡረተኛ የኦሮሞ ወታደራዊ መኮንን ለዘመቻው እንዴት አስተዋጽዖ ማድረግ እንደሚችል ጠይቀኝ ዘዴ ዘየድን። መኮንኑ ዩኒፎርሙን ከሰቀለበት አውርዶ ለብሶ ሄኒከን ቢሮ በመሄድ «ለምንድነው ሀገር የምትረብሹት?›» አላቸው። ያነጋገሩት ሰዎች ጡረታ መውጣቱን እንኳን ሳያውቁ መንግሥት እንደዘተባቸው አድርገው በመውሰድ ድንጋጤ ውስጥ ገቡ። ጉዳዩ ገፍቶ የመንግሥት ትኩረት እንዳገኘ ለኩባንያው ከፍተኛ አመራር አባላት አሳወቁ። ውጪ ሀገርም ኦሮሞ ሄኒክን ቢራ መግዛት ማቆሙን ለማሳየት ዲያስፖራዎች ጠርሙሱን እየሰበሩ ፎቶ እና ቪድዮ እየላኩልን ስንለጥፍ ነበር።

ዘመቻው በዚህ መልኩ ተፋፍሞ ኢትዮጵያ ያለውን በደሌ ቢራ ብቻ ሳይሆን አውሮፓ የሚገኘውንም የሄኒከን ዋና መሥሪያ ቤት ድንጋጤ ውሰጥ ከተተ። በማኅበራዊ ሚዲያ የሚደረገው ዘመቻ ላይ ስሜ ይጠቀስ ሰለነበር የሄኒከን ሰዎች ደውለውልኝ «የቴዲን ስፖንሰርሺፕ እንሠርዛለን፣ ዘመቻውን አቁሙ ብለው ተማጸኑኝ። ውሳኔያቸውን በግልጽ አሳውቀው የቴዲን አድናቂዎች ማስቀየም ሰላልፈለጉ ሐሳባቸው ሰፖንሰርሺፑን በድብቅ ማቋረጥ ነበር።

ይህን ስለተረዳሁ «የሰፖንሰርሺፕ ስምምነቱን ለሕዝብ ያሰተዋወቃችሁት ብዙ ሚዲያዎች በተጋበዙበት ዝግጅት ላይ ነበር። በተመሳሳይ መልኩ በግልጽ ወደ ሚዲያ ቀርባችሁ ኮንሰርቱ መሠረዙን ለሕዝብ መግለጽ አለባችሁ› አልኳቸው፣ልንሰማማ አልቻልንም። የእነርሱ መደወል ዘመቻችንን በደንብ ጫና እየፈጠረ መሆኑን ሰለተረዳንበት ይበልጥ አጧጧፍነው። ለሁለት ቀናት ካቅማሙ በኋላ በመጨረሻ ኣጅ ሰጡ።

በ2014 የፈረንጆች አዲሰ ዓመት ዋዜማ (ዲሴምበር 31፡ 2013) ውሳኔያቸውን በተቋማቸው ድረ-ገጽ ላይ ለጥፈው፡ ዘመቻውን እንዳሰቆም በስልክ እና በኢሜል ተደጋጋሚ ሙከራ አደረጉ። ውሳኔያቸውን አሰቀድሜ ሰለሰማሁ ስልኬን ዘግቼ ጠፋሁባቸው።እነሱ ከቀናት በፊት ስንወተውታቸው ጀሮ ዳባ ልበስ እንዳሉት እኔም በተራዩ ቂሜን ተወጣሁ።

ፊንፊኔ ያሉ የበደሌ ቢራ አመራሮች እና አምዕተርዳም ካለው የሄኒከን ዋና መሥሪያ ቤት እየደወሉ እንዲሁም የድምፅ መልዕክት እየተዉ ተማጸኑኝ፣ እኔ ግን ዝምታን መረጥኩ። በኋላ በግልጽ ለሚዲያ መግለጫ ሲልኩ #BoycottBedele ዘመቻ መቆሙን በተለያዩ ድረ-ገፆች አሳወቅን።

የዘመቻው ቀጥተኛ ዓላማ ኮንሰርቱን በማስቆም የቀድሞ ነገስታት በኦሮሞ እና በሌሎች ብሔሮች ላይ ያደረሱትን ወንጀል ለመካድ የሚደረገውን ሙከራ ማጋለጥ እና ማክሸፍ ነበር። ያንን ዘመቻ ያካሄድንበት ዋና ዓላማ ግን በአጭር ጊዜ ውጤት ሊያሰገኙ የሚችሉ ትንንሽ ዘመቻዎችን በማካሄድ ሕዝቡን ከሰለማዊ ትግል ጋር ለማለማመድ ብሎም በሚገኙት ድሎች ሞራሉን ለማነቃቃት ነው።እንዳሰብነውም #BoycottBedele ዘመቻ ወዳጅ እና ጠላትን ባሰደመመ መልኩ:-

በጥቂት ጊዜ ውስጥ ድርጅቱ ላይ ተጽዕኖ ፈጥሮ ኮንሰርቱን ማሠረዝ ቻለ። ይህም ለመጀመሪያ ጊዜ የማኅበራዊ ሚዲያ ዘመቻን መሬት ላይ ከሚደረግ ሥራ ጋር አቀናጅቶ ማሸነፍ እንደሚችል ለኦሮሞ ሕዝብ አረጋገጠ።

የዘመቻው ሰኬት በ#Oromoprotests ስም ለተከተለው የቄሮ ትግል መሠረት፣ ልምድ እና ጠንካራ ሞራል ሆነ። በእንዲህ ዓይነቱ ዘመቻ ተጨባጭ ለውጥ ማምጣት እንደሚቻል በማረጋገጥ ሕዝቡ በሰላማዊ ትግል ውጤታማነት ላይ የተሻለ ግንዛቤ እንዲያገኝ ረዳው። ለእኛም እየነደፍን የነበረውን የሰላማዊ ትግል ስልት በመሬት ላይ የምንፈትሽበትን ዕድል ሰጠን።

# 7.2. ቄሮ

የኦሮሞ ሕዝብ ከሃምሳ ዓመታት በላይ ከጭቆና ለመላቀቅ ሲታገል የቆየ ቢሆንም እንደ ቄሮ እንቅስቃሴ በፍጥነት ለውጥ ያመጣ አልነበረም። በአራት ዓመታት ውስጥ ያለ ፖለቲካ ድርጅት እና ጦር መሣሪያ በሕዝባዊ ተቃውሞ ብቻ የመንግሥት ለውጥ ማምጣት መቻል ተዓምር ነው። በዚህ የተነሳ ቄሮ የሚለው ቃል በኦሮሞ እና በኢትዮጵያ ፖለቲካ ውስጥ ትልቅ እውቅና አገኘ። የቄሮ እንቅስቃሴ ለኦሮሞ ትግል ይጠቅማል ብዬ ያጠናሁትን አና የተመራመርኩትን ሰልት ወደ ሥራ የቀየርኩበት፡ እንዲሁም በሕዝብ ዘንድ እውቅና እና ፍቅር ያሰገኘልኝ፣ በአንዳንድ የፖለቲካ ቡድኖች ዘንድ ጥላቻና ባላንጣ ያበዛብኝ ነበር።

‘’ቄሮ" ቀጥተኛ ትርጉሙ አዳጊ ተመንዳጊ ወንድ ወጣት ማለት ሲሆን፣ ቃሉ አንድን ሰው በነጠላ ለመግለጽ እንዲሁም በጉርምሰና ዕድሜ ውሰጥ ያሉ ወንዶችን በጋራ ለመግለጽ ሊውል ይችላል። ለምሳሌ «አቶ ገመቹ ፈረስ በሚገርም ሁኔታ የሚጋልብ ቄሮ ልጅ አለው» በማለት በነጠላ የአቶ ገመቹን አንድ ወጣት ልጅ ለመግለጽ እንጠቀማለን። እንዲሁም «የማዶ ሰፈር ቄሮ በጭፈራ አይቻልም» በማለት በቡድን ያሉ ወጣቶችን መግለጽ እንችላለን።

ቄሮ የሚለው ቃል በስፋት መስማት የጀመረው ከማስተር ፕላን ተቃውሞ ጋር ተያይዞ ቢሆንም፣ በኦሮሞ ፖለቲካ ውሰጥ ጥቅም ላይ ሲውል ግን የመጀመሪያ ጊዜው አይደለም። የታሪክ ማስረጃዎች እንደሚያሳዩት ቢያንሰ ከአሥራ ስድስተኛው ክፍለ ዘመን ጀምሮ ቄሮ በኦሮሞ ማኅበረሰብ ፖለቲካዊ እና ወታደራዊ እንቅስቃሴ ውሰጥ የወታደራዊ ክንፍ መጠሪያ ሆኖ ሥራ ላይ ሲውል ቆይቷል።

በአሥራ ዘጠነኛው ክፍለ ዘመን መገባደጃ ላይ ምኒሊክ በኦሮሞ ሕዝብ ላይ የወረራ ጦርነት በከፈተበት ወቅት ቄሮ በሚል ስም የሚጠራ አደረጃጀት ወረራውን በመከላከል ላይ ሲሳተፍ መቆየቱ ይነገራል። ለምሳሌ በጨለንቆ ጦርነት ጊዜ በቄሮ ስም የተደራጀ ኃይል መሳተፉን እናያለን።

በጨለንቆ ጦርነት 1887) ወቅት በበከር ዋሬ የሚመራው የኦሮሞ ሠራዊት በሦስት ቡድን የተደራጀ ነበር። የመጀመሪያው ሙርቲ ጉቶ የሚባል ሲሆን፣ በግንባር ቀደምነት ጦርነቱ ላይ የተሳተፈ ኃይል ነው። ራሬ ተብሎ የሚጠራው ሁለተኛው ቡድን የፈረሰኞች ጦር ነው። ሦስተኛው ቡድን "ቄሮ” ይባል የነበረ ሲሆን፣ ሚናቸው ሰላም ማስከበር (የአካባቢ ፖሊስ) ነው። የሙርቲ ጉቶ አና የራሬ ቡድኖቸ ከጠላቶቻቸው ጋር በጦር ሜዳ ሲዋደቁ፣ የቄር ቡድን ወደኋላ ቀርተው የቀዬውን ሰላም ከማስጠበቅ በተጨማሪ ጠላት በሌላ አቅጣጫ ቆርጦ እንዳይገባ ይከለክሉ እንደነበር ይወሳል። ይህ የቄሮ ቡድን ገና ለጋ ከሆኑ እና አስቀድሞ የውጊያ ልምድ ከሌላቸው ወጣቶች የተዋቀረ ነው። ለቡድኑ የሚሰጠው ሥልጠና ትግል፡ እንደ ወይራ ያሉ ዛፎችን በቡጢ መነረት፣ የቀስት ውርወራ እና የመሳሰሉትን የሚያካትት ሲሆን፡ ቡድኑ የሚዋጋባቸው የጦር መሣሪያዎች ቀስት፣ ዱላ፣ ወንጭፍ፣ ጦር፡ ድንጋይ እና የመሳሰሉትን ያጠቃልላል።

በመቀጠል ቄር የሚለው ስም በኦሮሞ ፖለቲካ ውሰጥ የታየው በ1560ዎቹ ነው። ከአፍረን ቀሎ፡ ሜጫና ቱለማ እንዲሁም ከባሌ ንቅናቄዎች የተረፉ ታጋዮች በ1960ዎቹ መገባደጃ ላይ የትጥቅ ትግል በዘመናዊ እና በተደራጀ መልክ ለማድረግ ኤደን/የመን ተሰባሰቡ። በኤሌሞ

ቂልጡ እና ጃራ አባ ገዳ መሪነት ወታደራዊ ሥልጠና ወስደው ወደ ኦሮሚያ ለመመለስ ጉዞ ጀመሩ። ኤሌሞ የዲፕሎማሲ እና የቁሳቁስ አቅርቦት ለማደራጀት ወደ ኋላ ሲቀር፣ጃራ ሠላሳ ስድስት አባላት የያዘውን ስብስብ ይዞ በኖቬምበር ወር 1969 ቀይ ባሕርን በመሻገር ወደ ኦሮሚያ አመራ። ያሰቡበት ቦታ ሳይደርሱ በሱማሌ መንግሥት ተይዘው ታሰሩ። ይህ የሠላሳ ስድሰቱ ሰዎች ሰብሰብ «ቄይሮ ገነማ›› (የጠዋቱ ቄሮ) በመባል ይታወቅ ነበር፣ቄሮ በሐረርጌ ኦሮሞ ዘዬ ቄይሮ ይሰኛል።

> «qeeyroo mataa tuutaa,
> Hin jarjartu suuta»
> «ቄይሮ ጸጉሩ የተከመከመ፣
> ይመጣል እያዘገመ።›

የሚለው እና በኦሮሞ ትግል ውስጥ የታወቀ ዝማሬም ከዚሁ ቡድን የመነጨ ነው። የቄሮ ገነማ ቡድን በሱማሊያ መንግሥት ሲታሰሩ፣ የቀሩት ጓዶች በኤሌሞ ቂልጡ መሪነት በአፋር በኩል ወደ ኦርሚያ ገብተው ጨርጨር አውራጃ ጢሮ የምትባል ቦታ ላይ የትጥቅ ትግል ጀመሩ። ለኦሮሞ ነጻነት ሠራዊት መፈጠርም መሠረት ጣሉ። ስለዚህ አንደ አሁኑ ሰፊ እውቅና ባይኖረውም የኦሮሞ ትግል መሥራቾች ቄሮ የሚባለውን ስም ገና ከጅምሩ ይጠቀሙት ነበር ማለት ነው።

ከ1997 ዐ.ም ምርጫ በኋላ በኦሮሚያ በተቀሰቀሰው የተማሪዎች አመጽ ወቅት ቄሮ የሚለው ቃል በኦሮሞ ትግል ውስጥ በድጋሚ ብቅ አለ። አመጹ የተቀናጀው በኦነግ ሥር በሚገኝ «ቄሮ ቢሊሱማ ኦሮሞ» የተባለ የወጣቶች መዋቅር ነበር። በኋላ እሰር ቤት የተገደለው ኢንጂነር ተሰፋሁን ጨመዳ እና ጓዶቹ ሲመሩት እንደነበር ይነገራል። በቄሮ ቢሊሱማ ኦሮሞ ሲካሄድ የነበረው አመጽ በጊዜው አገዛዙን መለወጥ ባይችልም ለቀጣይ እንቅሰቃሴ ጠንካራ ልምዶችን አስገኝቶ አልፏል።

በሚያዚያ 2006 ዐ.ም በተቀናጀ የአዲዕ አበባ ማሰተር ፕላን ስም የመንግሥትን የመሬት ወረራ እቅድ በመቃወም የተማሪዎች አመጽ ተቀሰቀሰ። ተቃውሞው በፍጥነት ወደ ሁሉም የኦሮሚያ ዞኖች ተዛመተ። መሬት ላይ ከሚደረገው ተቃውሞ በተጨማሪ በማኅበራዊ ሚዲያ በተለይም በፌሰቡክ የመረጃ ልውውጥ እና ቅንጅት ተጀመረ።

አመጹ ከመፈንዳቱ በፊት መንግሥት ማስተር ፕላኑን እያዘጋጀ እንደሆነ መረጃ ሲደርሰን፣ የማኅበራዊ ሚዲያ ዘመቻ በማካሄድ ስንቃወም ነበር። OMN ማርች 1 ቀን 2014 (የካቲት 22/2006 ዓ.ም) ሲጀመር ዘመቻውን በስፋት አጧጧፍነው።

ሚያዚያ መጨረሻ አካባቢ ተቃውሞው በዩኒቨርሲቲዎች ሲፈነዳ በ#BoycottBedele ዘመቻ የተሳተፉ አንቂዎችን በማሰባሰብ የሀገር ውስጥ ተቃውሞውን በማኅበራዊ ሚዲያ እና በተለያዩ ሚዲያዎች በተቀናጀ መልኩ መደገፍ በሚቻልበት ሁኔታ ላይ በመወያየት የማቀናጀት ሥራ ጀመርን። ተቃውሞው ዓለም አቀፍ ድጋፍ ማግኘት እንዲችል የማኅበራዊ ሚዲያ ዘመቻው ዲፐሎማቶች እና የውጭ ሚዲያዎችን መሳብ በሚችል መልኩ #oromoProtests የሚለውን ሀሽታግ መጠቀም ጀመርን። በአጠቃላይ ትግሉን ለመግለጽ ደግሞ «የኦሮሞ ቄሮ ንቅናቄ› የሚለውን ለመጠቀም ወሰንን።

## 7.3 **የአንጃዎችን ጥቃት መቋቋም**

በአንድ ወቅት አቶ ሌንጮ ለታ "እንኳንም መሰደብን ወርሰኸኝ እፎይታ ሰጠኸኝ" በማለት ቀለደብኝ። ሌንጮ ለታ ከ1990ዎቹ ጀምሮ ከኦሮሞም ሆነ ከሌሎች የኢትዮጵያን ፖለቲካ ጉዳይ ከሚያወሩ ሰዎች ምላስ ላይ የማይጠፋ ስም ነበር።

አንዱ ወገን ኦነግን በመምራት ኢትጵዮያን ለማፍርስ በመስራት ሲከሱት፣ የኦሮሞ አንጃዎች ደግሞ በ1992 ኦነግ ከቻርተሩ መውጣቱን ተከትሎ የተፈጠረውን ቀውስ በሙሉ ደፍድፈውበት "የኦሮሞን ትግል ሸጠ" በማለት ይረግሙታል። በፖለቲካዊ ስብሰባ ብቻ ሳይሆን፣ እንደ ሰርግ፣ ለቅሶ፣ ጫትና መጠጥ ቤት የፖለቲካ ውይይትና ክርክር ከተነሳ የሌንጮ ስም አይቀርም። ታዲያ የኔ ፖለቲካዊ ተሳትፎ እና ተሰሚነት እየጨመረ ሲሄድ፣ ከሀያ አመታት በላይ በግራና ቀኝ ሌንጮ ላይ ሲዘምቱ የነበሩ ሁሉ፣ ልክ የተወያዩ ይመስል ወደኔ መዞራቸውን የተረዳሁት ሽማግሌው "የስድብ ወራሼ ነህ" ብሎ ሲያሾፍብኝ ነው። እውነትም በኢትዮጵያ ፖለቲካ ውስጥ እንደ ሁለታችን በሁሉም ወገን ለረዥም ጊዜ የስም ማጥፋት ዘመቻ የተደረገበት ሰው ያለ አይመስለኝም።

በቄሮ ትግል ወቅት፣ ከሕወሓት/ ኢሕአዴግ አገዛዝ ከምናደርገው ትግል ጎን ለጎን፣ ከተቃዋሚው ጋር የምናደርገው የጎንዮሽ ፍትጊያም ቀላል አልነበረም። በአንድ ወገን ከውጪ የርዕዮተ-ዓለም ልዩነት ከነበረን "የአንድነት/ኢትዮጵያኒስት" ኃይሎች ጠንካራ ተቃውሞ ሲደርስብን፣ ከውስጥ ደግሞ ከኦሮሞ ድርጅቶችም ጋር ስንናቆር ነበር። ከውጫዊ ኃይሎች ውስጥ በተለይ ግንቦት ሰባት በግንባር ቀደም ሲፋለምን ቆይቷል። ለዚህም ሁለት ምክንያቶች ነበሩ። አንደኛው እራሳቸውን ሁሉንም የኢትዮጵያ ሕዝብ እንደሚወክሉ እና ነጻም እንደሚያወጡ ስለሚያስቡ እና በብሔር ተደራጅቶ መታገልን አጥብቀው ስለሚቃወሙ ነበር። ሁለተኛው ደግሞ የግንቦት 7 መስራቾች በምርጫ 97 ተሳትፈው ያሰቡት ስላልተሳካ ኤርትራ ገብተው የትጥቅ ትግል ስለጀመሩ እኛ የምንከተለው የሰለማዊ ትግል የማያዋጣ ብቻ ሳይሆን ሕዝቡን የትጥቅ ትግል እንዳይደግፍ ያነሳሳዋል ብለው ስለሚሰጉ ነበር።

ከዚህ የተነሳ በትግሉ መጀመሪያ አካባቢ የቄሮ ንቅናቄ ብሔርን መሰረት ያደረገ መሆኑን በማጥላላት እና እንዲሁም "በሰልፍ ለውጥ አመጣለሁ ብሎ ማሰቡን" በማጣጣል የሚዲያ ዘመቻ ያደርጉ ነበር። በተለይ የእኔን ተክለስብዕና ማጠልሸት ላይ በማነጣጠር የብሔር ብቻ ሳይሆን የሀይማኖት አክራሪ እንደሆንኩ በግልጽ በሚዲያ፣ ከጀርባ ደግሞ ለዲፕሎማቶች እኔን መፈረጅ ላይ ተሰማሩ። "ከ አንድ ሰሞን ግርግር አያልፍም" ባማለት ሲያጣጥሉት የነበረው የቄሮ ትግል እየተፋፋመ ሲሄድ፣ እነሱም የራሳቸውን ሰልፍ በአዲስ አበባ በመጥራት ሊፎካከሩ ቢሞክሩም ሊሳካላቸው አልቻለም።እኛ በበኩላችን "ከአንድነት" ቡድኖች የሚቃጣብንን የማጥላላት ዘመቻ እንምከት ነበር። በተለይ OMN ከተቋቋመ በኋል፣ ቀድሞ የነበራቸውን የሚዲያ የበላይነት ስላጡ የቄሮን ንቅናቄ ብዙም ሊጎዱ አልቻሉም።

አገዛዙ "እንደ እሳትና ጭድ" በሚያያቸው የአማራ እና የኦሮሞ ሕዝቦች መካከል ግጭት በመፍጠር ትግላችን በጎንዮሽ ሽኩቻ እንዳይዳከም በማሰብ ፤ በማንነታቸው ከሚታገሉ

የአማራ ወጣቶች ጋር መቀራረብ እና የትግል ትብብር ለመፍጠር መስራትን መረጥን። በኢትዮጵያ ስም የተቋቋሙ ሚዲያዎች በአብዛኛው "ለአንድነት" ኃይሉ ይወግኑ ስለነበር እና በአማራነት የሚታገሉ አንቂዎችን እንደሚያገልሏቸው ስለምናውቅ OMNን እንዲጠቀሙ ዕድል ሰጠናቸው። በወቅቱ የትግላቸው ዋና ጉዳይ የነበረውን የወልቃይት የማንነት ጥያቄ ኮሚቴ አጋርነት ማሳየታችን የበለጠ አቀራረበን። ከሁለት ዓመት በፊት በኦሮሚያ ተቀጣጥሎ እየተፋፋመ የነበረው ሕዝባዊ አመጽ ሐምሌ 2016 በአማራ ክልልም ፈነዳ። የአማራ ወጣቶች "የኦሮሞ ደም ደማችን ነው" የሚል መፈክር አንግበው አደባባይ በመውጣት ለቄሮ ትግል አጋርነታቸውን ገለጹ።

የአማራ እና የኦሮሞ ወጣቶች ያጧጧፉት አመጽ አገዛዙን ብቻ ሳይሆን የብሔር አደረጃጀት እና የሰላማዊ ትግልን ውጤታማነት ሲያጣጥል የነበረውን "የአንድነት" ካምፕ ያስደነገጠ ነበር። ከዚህ በመነሳት ሲከተሉት የነበረውን ማግለል በመተው ከሕዝባዊ አመጹ ጀርባ ድርጅታቸው ያለ ለማስመሰል መግለጫዎችን በመስጠት ራሳቸውን የስኬቱ ባለቤት አድርገው ማቅረብ ጀመሩ። መሬት ላይ የአማራ እና የኦሮሞ ወጣቶች የትግል ትብብር እየተጠናከረ በመሄድ፣ የኦሕዴድ እና ብአዴን አመራሮች እንዲደጋገፉ በማስቻል ከአመታት በፊት ከያሬድ ጥበቡ ጋር ተመኝተነው የነበረው "ኦሮማራ" የተባለው ስልታዊ ትብብር ይፋ ሆነ።

እንደ "አንድነቱ" ሁሉ በውስጥ ደግሞ የኦሮሞ ፖለቲካ ድርጅቶች ጋር የነበረን ፍትጊያ የበለጠ ፈታኝ እና አድካሚ ነበር። ከድርጅቶቹ፣ በተለይ ከኦነግ ጋር ለነበረው እሰጣገባ ብዙ ምክንያቶች ያሉ ቢሆንም ዋና ዋናዎቹ፣ ከትጥቅ ይልቅ ሰላማዊ ትግልን መምረጣችን፣ ኦሕዴድን በጠላትነት ከመፈረጅ ይልቅ አጋር ማድረግ ይሻላል ማለታችን፣ ከሁሉ በላይ ደግሞ ሕዝባዊ አመጹ በፖለቲካ ድርጅት ቁጥጥር ስር መሆን የለበትም የሚለው አቋማችን ነበር። የቄሮ ትግል እየተፋፋመ ሲሄድ የእኔ ሚና እየገነነ መምጣቱ ልዩነታችንን አባባሰው እንጂ፣ ከኦነግ አንጃዎች ጋር የነበረት ሽኩቻ ጅማሮው የቆየ ነው። ባለፉት ምዕራፎች እነደተገለጸው ገና አሜሪካ ሄጄ የዓለም አቀፍ የኦሮሞ ወጣቶች ማኅበር (IOYA) ካቋቋምንበት ጊዜ አንስቶ በውጪ ያሉ አብዛኞቹ የኦነግ መሪዎች እና አባላት እንቅስቃሴዬን ለማደናቀፍ ይሞክሩ ነበር። ለዚህም ምክንያታቸው ኦነግን የትግሉ ብቸኛ ድርጅት (vanguard) አድርገው ስለሚያስቡ፣ ወጣቶችም ሆነ ሌሎች የማኅበረሰብ ክፍሎች፣ በኦነግ ቁጥጥር ስር እንደ አንድ ቅርንጫፍ እንዲደራጁ እንጂ ራሳቸውን ችለው መንቀሳቀሳቸው ኃይል በመበታተን ትግሉን ያዳክማል ብለው ስለሚሰጉ ነበር። እኔ ግን ኦነግ ሰፊ ቅቡልነት እና ድጋፍ ያለው ቢሆንም፣ በውስጣዊ ቀውስ ምክንያት ስለተሽመደመደ፣ ማኅበራዊ ድርጅቶችን አቅፎ መቆየት ቀውሱ እንዲጋባባቸው ከማድረግ ውጪ ፋይዳ የለውም የሚል እምነት ነበረኝ። ከዚህ የተነሳ የኦነግ መዳከም ከግምት ውስጥ ሲገባ የወጣቶች ራሳቸውን ችለው መደራጀት የተቀዛቀዘውን ትግል እንዲያንሰራራ የሚረዳ መፍትሔ ሊሆን ይችላል የሚል ጽኑ እምነት ነበረኝ።

ወጣቶችን በማደራጀት ጉዳይ የጀመረው ልዩነት፣ በ2009 ኦነግን የተቸሁበትን ረጅም ጽሑፍ ለንባብ ሳቀርብ ሙሉ በሙሉ በጠላትነት ተፈረጅኩ። ስሜን ለማጥፋት ሲነዙ ከነበሩት ሀሜቶች ውስጥ "ኦሮሞን ለመከፋፈል እና ኦነግን ለማፍረስ ወያኔ በስኮላርሺፕ ስም የላከው

29 ለዚህ ጥሩ ማሳያ በወቅቱ የግንቦት7 ሊቀመንበር የነበረው ፕሮፌሰር ብረሃኑ ነጋ በጎንደሩ ተቃውሞ ማግስት

ነው" የሚለው ቀዳሚው ነው። የኦሮሚያን መገንጠል ባለመደገፌ ደግሞ "ኢትዮጵያኒስት/ Ethiopianist" የሚል ታርጋ በመለጠፍ ብሔርተኝነቴን ጥያቄ ውስጥ ለማስገባት ያላሰለሰ ሙከራ ተካሄደ። አንዳንዶቹ ደግሞ አክራሪ ሙስሊም መሆኔን እና ጽንፍ የያዘ የሀይማኖት ፖለቲካ እንደማራምድ ለፈረንጆች እና ለሌሎች የኢትዮጵያ ብሔሮች በመንገር የፖለቲካ ስብዕናዬን የመግደል ሥራ ላይ ተጠመዱ።

እኔ እና ባልደረቦቼ ግን የኦሮሞን ትግል በውስጣዊ ቀውስ ተተብትቦ መንቀሳቀስ ካቃተው ኦነግ ቁጥጥር ስር ለማውጣት አቅደን እየሠራን የነበረ ቢሆንም፣ ከድርጅቱ ጋር የፕሮፓጋንዳ ጦርነት ውስጥ መግባት ከጥቅሙ ጉዳቱ እንደሚያመዝን በማሰብ፤ የስም ማጥፋት ዘመቻውን የምናከሽፍበትን ሌላ ስልት ቀየስን። እነሱ ለሚያነሷቸው አሉታዊ ትችቶች ተመሳሳይ አሉታዊ መልስ ከመስጠት ይልቅ ተቃራኒውን አማራጭ ወሰድን። ይህም ኦነግ እና መሪዎቹን ከማጥላላት ይልቅ ለትግሉ ያደረጉትን አስተዋጽኦ በማጉላት አዎንታዊ መልዕክት ማስተላለፍ ነበር። በዚሁ መሰረት በOromo First እና OMN ዝግጅቶቻችን ላይ ኦነግ በኦሮሞ ትግል ውስጥ ያለውን ሚና ከፍ አድርገን በመናገር እና አንጋፋ የድርጅቱን ታጋዮች በልዩ ሁኔታ በሕዝቡ ፊት ሞገስ እንዲያገኙ እውቅና መስጠት ላይ አተኮርን።

ለአሉታዊ ዘመቻቸው አዎንታዊ መልስ መስጠት የመረጥነው ያለ ምክንያት አልነበረም። አንደኛ፣ በኦሮሞ ፖለቲካ ውስጥ ገና ብቅ እያልን ስለነበርና ያካበትነው የፖሊቲካ ካፒታል ዝቅተኛ ስለሆነም፣ ዕድሜ ጠገቡ፣ ድልብ የፖሊቲካ ካፒታል ያለውን እና የፕሮፓጋንዳ ጦርነት የተለማመደውን ኦነግ መግጠም አዋጭ አይሆንም። ሁለተኛ፣ የኦሮሞ ሕዝብ የኦነግ መዳከም ቢያስከፋዉም በሆዱ ይወደዋል ይሳሳለታል። በኦሮሞ ቤተሰብ ውስጥ ምንም ያህል አባትዬው ጥፋተኛ ቢሆን በልጁ ሲሰደብ መስማት አይፈልግም። በባሕላችን ልጅ የአባትን ወቀሳ ሰምቶ ከተቻለ ለመታረም ቃል ገብቶ ካልሆነም ቢያንስ መልስ ሳይሰጥ አጎንብሶ መሄድ ይጠበቅበታል። ሦስተኛ፣ ከኦነግ ጋር አንድ ማኅበራዊ መሰረት (social base/ constituency) ስለምንጋራ እና ከእነሱ ጋር ግልጽ የፖሮፓጋንዳ ጦርነት ውስጥ መግባት ሕዝባችንን በመከፋፈል እያቀድን ለነበረው ትግል አቅም ያሳጣናል። ከእነዚህ ምክንያቶች በመነሳት፣ አሉታዊው ሳይሆን አዎንታዊ ግብረ-መልስ መስጠታችን፣ በሕዝቡ ውስጥ የሞራል የበላይነት ስላጎናጸፈን ድጋፋችን እየሰፋ እንዲሄድ አስቻለን።

በቄሮ ትግል ወቅት "ኦነግ ያደራጀውን የቄሮ ትግል ጠለፈ (hijack)" ብለው ፈርጀውኝ ስለነበር በእኔ እና በኦነግ መካከል የነበረው ቅራኔ ተባባሰ። ባለፈው ምዕራፍ እንደተገለጸው እውነትም ከ2005/6 ጀምሮ በቄሮ ስም የተደራጀ የኦነግ የወጣቶች ክንፍ ነበር። ኅዳር 2011 የማስተር ፕላኑ ተቃውሞ ከፈነዳ በኋላ በኦነግ ሥር የሚገኘው የቄሮ መዋቅር በመንግሥት የደኅንነት ሰርጎ ገቦች ቁጥጥር ሥር መውደቁን ስለደረስንበት፣ ትግሉን የሚያቀናጅ ሌላ የወጣቶች አደረጃጀት በኅን ለማዋቀር ወሰንን።

መጀመሪያ ላይ ከኦነግ ጋር አተካሮ ውስጥ ላለመግባት "ቄሮ" የሚለውን ስም መጠቀም ፍላጎታችን አልነበረም። እነሱ ግን በእኛ ላይ የሚያደርሱትን ዘመቻ ማቆም አልፈለጉም። ችግራቸው ከስሙ ብቻ ሳይሆን ከእነሱ ቁጥጥር ነጻ ሆኖ መታገል የሚችል የወጣቶች እንቅስቃሴ አለመፈለግ መሆኑን ተረዳን። ስለዚህ "ቄሮ" የሚለውን ስም ወደ መጠቀሙ ገባን። ኦነጎች "ቄሮ ቢሊሱማ ኦሮሞ" የሚለውን ይጠቀሙ ስለነበር፤ በእኛ በኩል የሚወጣውን መግለጫ

ከእነሱ ለመለየት ስንል "ቄሮ ኦሮሞ" ማለትን መረጥን። የሆነ ዘመቻ ስናውጅ እኛን የሚቃረን መግለጫ በማውጣት ለማክሸፍ ጥረት ያደርጋሉ። Success has many fathers but failure is an orphan እንዲል አባባሉ እኛ ያወጅነው ዘመቻ ሲሳካ ደግሞ ቀድመው የተቃወሙትም ቢሆን ባለቤትነቱን ለመውሰድ ይሞክራሉ። ለምሳሌ ኦገስት 6 (ሐምሌ 30) ታላቁ ሰልፍ ሲታወጅ "ሕዝቡን ሊያስፈጁት ነው" በማለት ሕዝቡ ሰልፉ ላይ እንዳይሳተፍ መግለጫ አወጡ። በማግስቱ ሰልፉ ሲሳካ ራሳቸው እንዳደራጁት በማስመሰል ሌላ መግለጫ አወጡ።

በወቅቱ አሉታዊ ቅስቀሳ ሲያደርግብኝ የነበረው የኦነግ አንጃ በአቶ ዳውድ ኢብሳ የሚመራው ብቻ አልነበረም። በጄኔራል ከማል ገልቹ የሚመራው እና የለውጡ ኦነግ (ABO Jijjiiramaa) ፣ በኋላ ላይ የኦሮሚያ ሉዓላዊነት ግንባር (Adda Walabummaa Oromiyaa) የተባለ አንጃም ያብጠለጥለን ነበር። በተለይ አዲስ መጠቀም የጀመሩትን ባንዲራ በዝግጅቶቻችን ላይ እንዳይታይ መከልከላችን በጣም እንዳስከፋቸው አስታውሳለሁ። ያንን እርምጃ የወሰድነው በወቅቱ ሀገር ቤት በሚደረጉ ሰልፎች ላይ ሁሉም ነባሩን የኦነግ ባንዲራ ያውለበልብ ስለነበረ፤ አዲስ ባንዲራ ጨምረን በማስተዋውቅ ብዥታ እና ክፍፍል መፍጠር ስላልፈለግን ነው። ሁለት ባንዲራዎች በሰልፍ ላይ ማውለብለብ፣ ኦነግን ያዳከመው የአንጃ ፍክክር ወደ ቄሮ ሊያጋባ ይችላል ብለን ሰጋን።

ከውጪም ከውስጥም ሲካሄድብኝ የነበረውን ዘመቻ ተቋቁሜ ትግሉን መቀጠሌ እና ውጤታማ ማድረጌ በሕይወቴ ከረካሁባቸው ድሎች አንዱ ነው። ለዚህ ስኬት ዋናው ምክንያት ከልጅነቴ ጀምሬ ትችት እና ስድብን ለመቋቋም የሚያስችል "የአዞ ቆዳ" ሳዳብር ማደጌ ነው። ዱሙጋ "ፉቶታ" የሚባል ልማድ ነበር። ወጣቶች ጠዋት ልክ ሰማዩ ወገግ ሲል ወደ ጉሊት ገበያ በመሄድ ገበሬዎች ሌሊቱን ከእርሻ ቆርጠው የሚያመጡትን ሸንኮራ ለመብላት ይሰበሰባሉ። ታዲያ ሙቀቷ እየበረታ የምትሄደዋ ጸሐይ ላይ ቁጭ ብለው የሚያኙኩት ሸንኮራውን ብቻ አልነበረም። ከመካከላቸው አንድን ሰው ነጥለው ሁሉም ይሳለቁበታል። መልኩን፣ ቤተሰቡን፣ ልብሱን፣ አረማመዱን እና አነጋገሩን ሳይቀር በመተቸት ለማብሸቅ ተራ በተራ ይዘምቱበታል። አንዱ ሲተርበው የተቀረው ላንቃው እስኪዘጋ እያስካካ በመሳቅ ነገር ያሟሙቃል።

በዚህ ሂደት ባለተራው ተፎጋሪ ተናዶ ከሰው ከተጣላ፣ ተከፍቶ ካለቀሰ ወይም መቋቋም አቅቶት ከቦታው ከሄደ እንደተሸነፈ ተቆጥሮ ነገም ሌላ ተተራቢ መምረጡ ይቀርና እሱኑ ማብሸቁ ይቀጥላል። ቀኑ ደርሶ ለፉገራ የተመረጠ ሰው ትዕይንቱን በአሸናፊነት ለመወጣት የሚወረወረውን እያንዳንዱን የቃላት ሸንቆጣ ታግሶ በፈገግታ ማለፍ ይጠበቅበታል። መጀመሪያ ተራ የደረሰው ዕለት ውርጅብኙን መታገስ የሚችል ሰው የለም፤ በሂደት ግን ስሜቱ እየተላመደ እና እየደነደነ ሲሄድ ትዕግሥት በማዳበር የአዞ ቆዳን መላበስ ይጀመራል። በእንደዚህ ዓይነት ልማድ ውስጥ ማለፌ ከፖለቲካ ቡድኖች እና ግለሰቦች የሚሰነዘርብኝን ትችት ችዬ በሥራዬ ላይ እንዳተኩር ረድቶኛል።

የፕሮፓጋንዳ ዘመቻን ለመቋቋም የቻልኩበት ሌላው ምክንያት የኢትዮጵያን የፖለቲካ ድርጅቶች ተቋማዊ ባሕል ማጥናቴ እና መረዳቴ ነው። መነሻቸው ከኮሚኒስት/ ስታሊኒስት ርዕዮተ-ዓለም የሆኑ የፖለቲካ ድርጅቶች ስም ማጥፋት (character assassination) እንደ ወሳኝ የፖለቲካ ስልት ይቆጥሩታል። ከእነሱ ጋር የሐሳብ ልዩነት

ያላቸው ሰዎች ላይ ገደብ የለሽ የስም ማጥፋት ዘመቻ በማካሄድ በግለሰቡ ላይ የሥነ-ልቦና ጫና በመፍጠር ወይም በሕዝብ እንዲጠላ በማድረግ ከፖለቲካ ምህዳር ያስወጡታል። ይህንን ገና በጠዋቱ ስለተረዳሁ በእኔ ላይ ሊደረጉ የሚችሉ የስም ማጥፋት ዘመቻዎችን እንዴት መቋቋም እንዳለብኝ አእምሮዬን አዘጋጀሁ።

አንድ የፕሮፓጋንዳ ጥቃትን ለመቋቋም ሁለት ነገሮች ያስፈልጋሉ። የመጀመሪያው በትችት እና በስድብ የቀላሉ የማይረበሽ ስሜት ማዳበር ሲሆን፣ ሁለተኛው ስልት ለሚሰነዘሩ ትችቶችና ስድቦች በፍጥነት እና በቀጥታ አጸፋዊ ምላሽ ላለመስጠት ስሜትን መቆጣጠር ነው። ትችቶች እና ዘለፋዎች ስሜቶቻችንን ስለሚኮረኩሩ፣ ተፈጥሮዓዊ ዝንባሌያችን ወድያውኑ መልስ በመስጠት ራስን መከላከል ነው። ይህን መልስ የመስጠት ስሜታዊ ግፊት ለመቋቋም፣ የአእምሯችንን ትኩረት ከዚያ ትችት ይልቅ ወደ ሌሎች ጉዳዮች ላይ እንዲያተኩር ማዛወር (re-channeling) ያስፈልጋል። ለምሳሌ ትችቶችን ደጋግመን ከማንበብ/ ማዳመጥ በመታቀብ እንዲሁም በአዕምሯችን መመላለሱን ለመግታት፣ ከጉዳዩ ጋር የሚያያዝ እና ሊያስታውሰን ከሚችል ሥራ ይልቅ ሌላ ነገር ላይ ማተኮር ጠቃሚ ነው።

በውሸት ስማችን ሲጠፋ እና ስንሰደብ መጀመሪያ ወደ አእምሯችን የሚመጣው እርምጃ እራሳችንን መከላከል ነው። ነገር ግን በፖለቲካ ውስጥ ለሐሰት ፕሮፓጋንዳ እና ለስድብ ሁሌ ምላሽ መስጠት የሚካሄድብንን ዘመቻ እንዲሳካ ማድረግ ነው። ስለዚህ ለትችት እና ለዘለፋ ወዲያው በቀጥታ ምላሽ ከመስጠት ይልቅ ጊዜ ወስዶ፣ አእምሮን አረጋግቶ ፕሮፓጋንዳውን የሚያከሽፉ ተግባራት ላይ ማተኮር ይመረጣል። "ከመጥፎ ሰዎች ጋር ንትርክ ውስጥ አትግባ፤ ምክንያቱም ወደራሳቸው ደረጃ ቁልቁል ይጎትቱሀና በልምዳቸው ያሸንፉሃል (Never argue with stupid people, they will only drag you down to their level and then beat you with experience)" የሚለውን የማርክ ትዌይን አባባል እንደ መመሪያ እጠቀም ነበር። ስለዚህም በአንጃዎችም ሆነ በግለሰብ ደረጃ በእኔ ላይ ለሚነዙት ፕሮፓጋንዳ ምላሽ ከመስጠት ይልቅ በሥራ በልጦ በመገኘት ማክሸፍን መረጥኩ። በዚህ ስልትም ስኬታማ በመሆን እራሴንም ትግሉንም መጥቀም ችያለሁ።

## 7.4. ማስተር ፕላን

የአዲስ አበባ ከተማን የተቀናጀ ማስተር ፕላን የማዘጋጀት ሐሳብ በድብቅ ሲካሄድ ከቆየ በኋላ ለግልጽ ውይይት ቀረበ። በአገዛዙ ውስጥ ያሉ ሰዎች ለውጭ ምሁራን እና ታጋዮች አስቀድመው ተናግረው ስለነበር እንዴት ማስቆም እንደሚቻል ቅድመ ዝግጅት ማድረግ ተጀምረ። ቀጥሎ በተገለጹት ምክንያቶች ይህ ጉዳይ ትግሉን ለማቀጣጠል ትልቅ ዕድል እንደሆነ ተረዳን።

1. የመሬት ጉዳይ በኦሮሞ ዘንድ አንገብጋቢ (sensitive) ስለሆነ የሕዝቡን ስሜት ለመቀስቀስ እና በአንድነት ለማነሳሳት ይረዳል። በምኒሊክ ጦር ከተሸነፈ ጀምሮ ኦሮሞ ከመሬቱ እየተፈናቀለ፤ የተቀረው ደግሞ እርቦና ሢሶ እየከፈለ ሲመዘበር ስለነበር ያልሻረ ቁስል አለው። ማስተር ፕላኑ መሬቱን የመዝረፍ እቅድ እንደመሆኑ ቁስሉን መንካት እንደሚያስቆጣው ግልጽ ነው።

2. የፊንፊኔ ባለቤትነት ጉዳይ ዋና ዋና ከሆኑ የኦሮሞ ጥያቄዎች ውስጥ አንዱና ሕዝቡ ከዳር እስከዳር የሚስማማበት አጀንዳ ከሆነ ሰነባብቷል። የኦሮሞ ሕዝብ በፊንፊኔ ላይ ያለው የባለቤትነት ጥያቄ ይመለስልኛል ብሎ ሲጠበቅ መንግሥት ተጨማሪ መሬት ቆርሶ ለማስፋፋት ማሰቡ፣ ሕዝቡን ለባሰ ቁጣ የሚዳርግ ንቀት ነበር።

3. በፊንፊኔ እና አካባቢው ያለው መሬት ለገዢው ፓርቲ ባለሥልጣናት እና ካድሬዎች ዋና የገቢ ምንጭ እንዲሁም በመካከላቸው ለሚካሄደው ሽኩቻ ምክንያት መሆኑ ይታወቃል። ካሰብናቸው ስልታዊ ሥራዎች ውስጥ አንዱ ኦሕዴድ እና ሕወሓትን መለያየት ስለሆነ፤ የመሬት ዘረፋን ጉዳይ ትልቅ አጀንዳ ማድረጉ ሁለቱን ቡድኖች ለማጋጨት እና ለማራራቅ ዕድል ይፈጥራል።

የተቀናጀ ዘመቻ በማኅበራዊ ሚድያ ማካሄድ እንደጀመርን ብዙም ሳይቆይ የዩኒቨርሲቲ ተማሪዎች ተቃውሞ ፈነዳ። እቅዳችን ሕዝቡን በሚዲያ እና በትናንሽ ዘመቻዎች አንቅቶ ወደ ሙሉ ተቃውሞ ለማስገባት ከስድስት ወር እስከ አንድ ዓመት ሊፈጅ ይችላል የሚል ነበር። ከፌስቡክ ዘመቻ በተጨማሪ OMN ተከፍቶ ሰፊ ሽፋን በማግኘቱ፤ የማስተር ፕላኑ ጉዳይ ኢንተርኔት ለሌለው ማኅበረሰብ በየቤቱ ተደራሽ ለመሆን ቻለ። በዚህም የተነሳ ሁለት ወር ባልሞላ ጊዜ ውስጥ ተቃውሞው ፈነዳ፤ ሕዝቡ ከገመትነው በላይ ዝግጁ እንደነበር አመላከተ። መንግሥት ከውስጥ እና ከውጪ ሲነሳ የነበረው ቅሬታ በዚያ ፍጥነት ወደ አመጽ ይቀየራል ብሎ አልገመተም። ስለዚህም ማስተር ፕላኑንን የማስፈጸም ዓላማውን ገፍቶበት ተቃውሞውን በፓርቲ መዋቅር ለማክሸፍ መካከለኛ ካድሬዎችን ሲሰበስብ ያልጠበቀው ተቃውሞ ገጠመው። የገዢው ፓርቲ ካድሬዎች በውስጥ ስብሰባ ላይ ያሰሙት ተቃውሞ ሾልኮ ወጥቶ በሚዲያዎች መተላለፉ ሕዝቡ የበለጠ ታቃውሞውን እንዲያጠነክር አደረገ።

መጀመሪያ በዩኒቨርሲቲዎች የተቀሰቀሰው ሕዝባዊ አመጽ ብዙም ሳይቆይ ወደ አንደኛ እና ሁለተኛ ደረጃ ትምህርት ቤቶች ተዛመተ። ሚያዚያ 22 ቀን 2006 ዓ.ም በአምቦ በተካሄደው ተቃውሞ የተደናገጠው መንግሥት ባዶ እጁን የወጣ ሕዝብ ላይ በመተኮስ የበርካታ ንጹሀንን ሕይወት ቀጠፈ።

የአምቦው ግድያ መላው ኦሮሚያን አስቆጥቶ ከፍተኛ ተቃውሞ ቀሰቀሰ። ሁኔታው ያስደነገጠው መንግሥት፣ ማስተር ፕላኑን ሕዝቡ እስኪወያይበት ድረስ ለጊዜው ማቆሙን የሚገልጽ መግለጫ ለማውጣት ተገደደ። መግለጫውን ተከትሎም ተቃውሞው ለተወሰኑ ወራት እንዲቆም ተደረገ። ተቃውሞው እንዲቆም የተወሰነው በሚቀጥሉት ሦስት ምክንያቶች ነበር።

መንግሥት ማስተር ፕላኑን አቁሜያለሁ ካለ በኋላ ተቃውሞው እንዲቀጥል ማድረግ በሕዝብ እይታ ምክንያታዊ ያልሆነ እንዲመስል በማድረግ የሕዝቡ አስተሳሰብ ወደ መንግሥት እንዲያጋድል ሊያደርግ ስለሚችል።

1. መንግሥት ማስተር ፕላኑን ለጊዜው ማቆሙን ማስታወቁ፤ ተቃውሞው በፍጥነት እየተስፋፋ ስለነበር፤ ሂደቱን ለመገምገም እና ስሕተቶቹን ለማረም ጠቃሚ ዕድል ስለሆነ።

2. እስከዚያ ቀን በተከናወኑ ተግባራት የመንግሥት የመረጃ ክፍል ወደ ቄሮ መዋቅር ዘልቆ መግባቱ ስለተጠረጠረ፤ ይህን ማጥራት ለቀጣይ ሥራ አስፈላጊ ስለሆነ ነው። ተቃውሞው ለጊዜው ቢቆምም የማስተር ፕላኑ ጉዳይ የኢትዮጵያ ፖለቲካ ዋነኛ አጀንዳ ሆኖ ቀጠለ። በእኛ በኩል ግምገማ የማካሄድ፣ ሥልጠና የመስጠት እና የማደራጀት ሥራው ቀጠለ። የኅብረተሰቡን ግንዛቤ የበለጠ ለማሳደግ በሀገር ውስጥ እና በውጪ ሀገራት በርካታ የውይይት መድረኮች ተካሄዱ። OMN እነዚህን ውይይቶች በዜና እና በትንታኔ መልክ አሰምሮ በማቅረብ ላይ በስፋት ሰራ። መንግሥት በበኩሉ ማስተር ፕላኑን ለጊዜው የተወው ቢመስልም ውስጥ ውስጡን ግን ተግባራዊ ለማድረግ ዝግጅቱን አጠናክሮ ገፋበት። ካድሬዎችን በምሥጢር በመሰብሰብ ወደ ሕዝቡ ወርደው እንዲያሳምኑ የተለያዩ ስብሰባዎችን ያካሄድ ነበር። በአገዛዙ ወስጥ ያሉ እና ለሕዝባዊ ትግሉ ተቆርቋሪነት ያላቸው፤ ከቻሉ ይህንን ሤራ በግልጽ በመቃወም፣ ካልቻሉ ደግሞ ውጪ ላለነው መረጃ በማቀበል ላይ በረቱ። ስለማስተር ፕላኑ ለመወያየት በተጠራ አንድ ስብሰባ ላይ ኢንጂነር ታከለ ኡማ «ፊንፊኔ በታሪክም በሕግም የኦሮሞ ለመሆኗ ሙሉ ማስረጃ አለን፤ የኦሮሞን ሕዝብ የማይጠቅም እቅድ ተግባራዊ መሆን የለበትም» በማለት በግልጽ ተቃወመ። ይህ ተቃውሞ በኦሮሚያ ቴሌቪዥን ፕሮግራም አየር ላይ ዋለ። OMN የመንግሥት ሚዲያ የዘገበውን ወስዶ በተለያዩ ትንታኔዎች እያጀበ ትልቅ አጀንዳ አደረገው። መንግሥት ማስተር ፕላኑን አቁሜያለሁ ያለው ሕዝቡን ዋሽቶ ተቃውሞውን ለማርገብ እንጂ ከልቡ እንዳልሆነ፤ በምሥጢር የሚያካሄዳቸው ስብሰባዎች ማስረጃ መሆናቸው ቀርቦ በተደጋጋሚ ተተቸ።

በዚያው ሰሞን በሐዋሳ ከተማ በተካሄደ ስብሰባ ላይ በወቅቱ የፌደራል ጉዳዮች ሚኒስትር የነበረው እና ከሕወሓት ከፍተኛ አመራሮች አንዱ አቶ አባይ ፀሐዬ «ወደዳችሁም ጠላችሁም ማስተር ፕላኑ ተግባራዊ ይሆናል፤ ይህንን የሚቃወም አካል ካለ ልክ እናስገባዋለን» በማለት ዛተ።

የዚህ ዛቻ ቅጂ በድብቅ ተቀርፆ ወደ እኔ ተላከ፤ ቅጂውን ለተወሰነ ጊዜ ደብቄ ትልቅ ጥቅም ማምጣት የሚችልበትን ጊዜ መጠባበቅ መረጥኩ። መንግሥት አቁሜያለሁ ያለውን ማስተር ፕላን ለማስጀመር እንቅስቃሴ ሲጀምር በምሥጢር የተላከውን ድምፅ በOMN በኩል እንዲለቀቅ አደረኩ። የአባይ ፀሐዬ የንቀት ንግግር መንግሥት ማስተር ፕላኑን ለጊዜው ማቆሙን ካስታወቀ

ወዲህ የተቀዛቀዘውን የሕዝብ ስሜት እንደ አዲስ ቀሰቀሰ። OMN ያንን የአባይ ፀሐዬን ንግግር በሁሉም ዜናዎች እና ፕሮግራሞች መሀል ደጋግሞ ማሰማቱን ቀጠለ።

የአባይ ፀሐዬን ንግግር ደጋግምን ስናቀርብ የነበረው የሕዝቡን ስሜት ለመቀስቀስ ብቻ አልነበረም። ቀደም ብዬ እንደገለጽኩት መለስ ዜናዊ የሕወሓት መድሏዊ አምባገነንነት ሰዋዊ ምስል (personification) ሆኖ ያገለገለ ሲሆን፣ እሱ ሲሞት ችግር ገጠመን። ይህን ችግር የምንወጣበትን መንገድ እያሰብን ሳለ ነበር መፍትሔ እንዲሆነን የአባይ ፀሐዬ ንግግር የደረሰን። አባይ ፀሐዬ ከሕወሓት አመራሮች መካከል በመሆኑ፣ በመለስ ቦታ በመተካት የትግል አጀንዳችንን እንድንቀጥልበት ረዳን።[30]

የአባይ ፀሐዬን ድምፅ ደጋግመን ማሰማት የሕዝቡን ቁጣ በማገንፈል ለሌላ ዙር ተቃውሞ አዘጋጀው። የመንግሥት ሰዎች የሕዝቡን ቁጣ ለማብረድ በተለያዩ ከተሞች ስብሰባዎችን ማድረግ ጀመሩ።

በሱሉልታ ከተማ በተካሄደ ስብሰባ ላይ በወቅቱ የጨፌ ኦሮሚያ አፈ-ጉባኤ የነበረው አቶ ለማ መገርሳ «ማስተር ፕላኑ ወርቅ ቢሆን እንኳን ሰማይ ዝቅ ይላል ምድር ከፍ ትላለች እንጂ የኦሮሞ ሕዝብ ካልፈለገው ይቀራል» ብሎ ተናገረ። ይህ ንግግር በምሥጢር ተቀድቶ ተላከና አየር ላይ አዋልነው።

በOMN እና ፌስቡክ ላይ በምናቀርበው ዕለታዊ ትንታኔ ኦሕዴድ ውስጥ ያሉ ብሔርተኞች ማስተር ፕላኑን በመቃወም ከሕዝቡ ጎን መቆማቸው ተረጋገጠ በማለት አስተጋባን። ይህም በአገዛዙ ውስጥ ያሉ ኦሮሞዎችን እና የቄሮ እንቅስቃሴን አቀራርበን በማቀናጀት አገዛዙን ከውስጥ እና ከውጪ ለማስጨነቅ ላወጣነው ስልት ትልቅ እገዛ አደረገልን። በተጨማሪም ንግግሩ ለማ መገርሳን የውስጥ ትግሉ መሪ በማድረግ የሕዝቡ ዓይን ውስጥ እንዲገባ አደረገው። እኛም ለማን የውስጣዊ ትግሉ መሪ አድርጎ የማየት አመለካከት (perception) እንዲጠናከር በተለያየ መንገድ አጥብቀን ሰራንበት። ለዚህ ደግሞ ሦስት ምክንያቶች ነበሩን።

1. ሕዝቡ ትግሉ መሀሉ ባሉ ሰዎች እንደሚመራ በማሰብ እንደትናንቱ ከውጪ አመራር በመጠበቅ እንዳይዘናጋ ስለሚረዳን፤
2. «የውጪ ኃይሎች ናቸው ሀገር የሚበጠብጡት» የሚለውን የመንግሥት ፕሮፓጋንዳ ለማክሸፍ፤
3. የኦሕዴድ አባላት ተቃውሞው በራሳቸው ሰው እንደሚመራ በማሰብ፣ የሚመጣው ለውጥ የበለጠ የሚጠቅማቸው እንጂ የሚያጠፋቸው እንዳልሆነ ገምተው ከትግሉ ጋር እንዲተባበሩ ለማስቻል ናቸው።

በዚህ እሳቤ ላይ ተንተርሰን ለማን እንደትግሉ መሪ ለመሳል የሠራነው ዘመቻ በሂደት ለትግሉ ከፍተኛ ጠቀሜታ ነበረው። ጥቅሙ የሁለተኛው ዙር ተቃውሞ ወዲያውኑ እንዲቀጣጠል ከመርዳት ይጀምራል።የአባይ ፀሐዬ የንቀት ንግግር ሕዝቡን ሲያስቆጣ፣ በተቃራኒው የለማ መገርሳ ንግግር ተስፋ

30 ለውጥ መጥቶ ሀገር ቤት ከተመለስኩ በኋላ፣ በሕወሓት እና በጠ/ሚ አቢይ መካከል አየተካረረ የመጣውን ውጥረት ለማርገብ አሞክር በነበረበት ወቅት፤ አንድ ቀን ከአባይ ፀሐዬ ጋር በስልክ እያወራን በቄሮ ትግል ወቅት በአሱ ላይ አነጣጥረን ያደረግነውን ዘመቻ ፍትኃዊ (fair) እንዳልነበረ ነገረኝ። እሱ ላይ ያነጣጠርንበትን ሰልታዊ ምክንያት ነግሬው፤ ፖለቲካዊ እንጂ ምንም ግለሰባዊ ጉዳይ ከእሱ ጋር እንደሌለኝ አረጋገጥኩለት። በግል ደረጃ ለደረሰበት ሞራላዊ ጉዳትም እንደማዝን ገለጽኩለት።

እንዲሰንቅ በማድረግ የትግል ስሜት በሥርዓቱ መዋቅር ውስጥ እና በውጪ እንዲስፋፋ በማድረግ፤ ኅዳር 2 ቀን 2008 ዓ.ም የሁለተኛው ዙር የማስተር ፕላን ተቃውሞ በምዕራብ ሸዋ ጊንጪ ከተማ ፈነዳ። ከመጀመሪያው ዙር ጠንካራ እና ደካማ ጎኖች በመማር ለሁለተኛው ዙር ጥሩ ዝግጅት ተደርጎ ስለነበር፣ በጊንጪ የተቀሰቀሰው አመጽ በፍጥነትም በስፋትም ጥሩ ውጤት ማስገኘት ጀመረ።

ከጊንጪ ቀጥሎ ወደ ጉሊሶ (ምዕራብ ወለጋ) ተሻግሮ በተቃውሞው ከረሳ ጫላ እና ጉቱ አበራ የተባሉ ተማሪዎች በአሠቃቂ ሁኔታ ተገደሉ። የግድያው ቪድዮ በOMN እና በማኅበራዊ ሚዲያዎች መሰራጨቱ ሕዝባዊ አመጹ በፍጥነት ኦሮሚያን እንዲያዳርስ አደረገ። ኅዳር 2 የጀመረው አመጽ በሁለት ሳምንት ውስጥ ሁሉንም የኦሮሚያ ዞኖች አዳረሰ። መንግሥት በኃይል ለማፈን እስርና ግድያውን ባጠናከረ ቁጥር ተቃውሞው በተቃራኒው የበለጠ እየተስፋፋ ሄደ፣ መጀመሪያ ላይ በተማሪዎች ሲካሄድ የነበረው ተቃውሞ ገበሬዎች እና የመንግሥት ሠራተኞችን በመሰቡ የሰልፈኞች ቁጥር በከፍተኛ ሁኔታ ጨመረ።

በተለይ እንደ ምዕራብ ሸዋ እና ምዕራብ አርሲ ባሉ ዞኖች አርሶ አደሩ የመንግሥትን አሥተዳደራዊ መዋቅር አፍርሶ የነጻነት ባንዲራ አውለበለበ። በፊንፊኔ አቅራቢያ ባሉ ዞኖች ላይ ተቃውሞ እንዲበረታ በአትኩሮት ሰራን። ለዚህ ስልታዊ ምክንያቶች ነበሩን። ፊንፊኔ የፖለቲካ እና የዲፕሎማሲ እምብርት ከመሆኗም ባሻገር አብዛኛው የሀገሪቷ ኢኮኖሚያዊ እንቅስቃሴ የሚከናወነው ለዋና ከተማው ቅርብ በሆኑ ዞኖች ውስጥ ነው። ስለዚህም በእነዚህ አካባቢዎች የሚደረግ የተቃውሞ እንቅስቃሴ ድርብርብ ፖለቲካዊ፣ ዲፕሎማሲያዊ እና ኢኮኖሚያዊ ጫናዎችን ለማሳደር ይረዳል።

መጀመሪያ ከፊንፊኔ በመቶ ኪሎ ሜትር ራዲየስ ውስጥ ማነጣጠር አለብን የሚል ሐሳብ ሲነሳ የአካባቢው ማኅበረሰብ ለመንግሥት ቁጥጥር ቅርበት ያለው በመሆኑ ለተቃውሞ የሚያመች የፖለቲካ ንቃት የለውም፣ ጊዜ እና ጉልበት ማባከን ይሆንብናል የሚል ግምት ወሰደን ነበር። ነገር ግን አካባቢውን ሳናንቀሳቅስ አስፈላጊውን ውጤት ማስመዝገብ አዳጋች እንደሆነ በመረዳት ተሠራበት። ሕዝቡም በመጀመሪዎቹ ሳምንታት ብቻ ባሳየው ተቃውሞ የነበረንን ግምት መሠረተ-ቢሥነት አረጋገጠልን። ኅዳር ሁለት የጀመረው የሁለተኛው ዙር ተቃውሞ፣ በታኅሣሥም ተጧጡፎ በመቀጠል በክልሉ አሥራ ሰባት ዞኖች ውስጥ ከአራት መቶ በላይ በታዎች ላይ ተካሄደ። ተቃውሞው የመባባስ እንጂ የመቀነስ አዝማሚያ ሳይታይበት ቀጠለ። የ2016 የፈረንጆች አዲስ ዓመት ሰሞን መንግሥት የላካቸው ሰዎች አግኝተውኝ ተቃውሞውን እንዳስቆም የማስፈራራት እና የመደለል ዓይነት ይዘት ያለው መልዕክት ነገሩኝ። መልሴ ማስተር ፕላኑ ሙሉ በሙሉ እስካልተሠረዘ ድረስ የሚቆም ተቃውሞ አይኖርም የሚል ነበር። በዚሁ ተለያይተን ከአንድ ሳምንት በኋላ መንግሥት ለጥያቄያችን መልስ ለመስጠት መዘጋጀቱን ፍንጭ የሚሰጥ መልዕክት ላኩልኝ። ጃንዋሪ 12 ቀን 2016 (ጥር 3/2008 ዓ.ም) ማስተር ፕላኑ ሙሉ በሙሉ መሠረዙን የኦሕዴድ ማዕከላዊ ኮሚቴ ባወጣው አስቸኳይ መግለጫ አሳወቀ። በሦስት ወር ያልተቋረጠ ትግል፣ ከ250 በላይ ሰዎች በግፍ ተገድለው እና ሺዎች ታስረው በመጨረሻም መንግሥትን ማንበርከክ ተቻለ። መንግሥት ማስተር ፕላኑን መሠረዙን ተከትሎ በፌስቡክ በለጠፍኩት መልዕክት የተገኘው ድል ገዢው ፓርቲ በነጻ የሰጠን ሳይሆን ታላቁ የኦሮሞ ሕዝብ ባካሄደው መራራ ትግል እና ልጆቹ በከፈሉት መሥዋዕትነት የተገኘ

መሆኑን በመግለጽ፤ ሕዝባችን የመንግሥትን መግለጫ እንዳይተማመንና የቀሩ መብቶቹንም ለማስከበር ትግሉን መቀጠል እንዳለበት አሳሰብኩ።

ማስተር ፕላኑን በማሠረዝ የተገኘውን ድል ለሚቀጥለው ዙር ትግል ሞራል ግንባታ በሚረዳ መልኩ እየተጠቀምንበት፤ ሕዝቡም ለተወሰነ ጊዜ ከድል ጽዋው እየተጎነጨ ዕረፍት እንዲያደርግ ወሰንን። መንግሥት ማስተር ፕላኑን መሠረዙ ተቃውሞውን የሚያስቆም መስሎት ተስፋ አድርጎ ነበር።

እኛ ግን ድል ማድረጋችንን ብናውጅም ትግሉ እንደሚቀጥል በማሳወቅ፣ ለሕዝቡ ዕረፍት መስጠት እና ባለፉት ሦስት ወራት የተከናወኑ ሥራዎችን ከመገምገም ጎን ለጎን፤ ለሚቀጥለው ዙር ተቃውሞ ማቀጣጠያ የሚሆን ጉዳይ (triggering cause) በመምረጥ ላይ ነበርን። የፖለቲካ እስረኞች ይፈቱ የሚለውን ጥያቄ ለሚቀጥለው ዙር ሕዝቡን ለማሥነሳት ይረዳል ብለን ወሰንን። ባለፉት ሦስት ወራት ተጋድሎ ወቅት በሺዎች ስለታሰሩ ድሉን ያመጡትን እስር ቤት ትተን በድሉ መደሰት ተገቢ አይደለም የሚል ሐሳብ አጋራን። ታኅሣሥ ውስጥ አዳማ ላይ በተደረገው ሰልፍ ላይ ታስሮ የነበረውን አቶ በቀለ ገርባን የፖለቲካ እስረኞቹ ተወካይ አድርገን ዘመቻውን አጧጧፍነው። በሰላማዊ ትግል የሕዝብ ግንኙነት ስትራቴጂ ውስጥ በመቶ የሚቆጠሩ ተበዳዮችን ከመዘርዘር፣ አንድን ተበዳይ እንደምሳሌ መርጦ በከፍተኛ ትኩረት ማስተዋወቅ የተሻለ ውጤት እንደሚያስገኝ ተምረናል።

የሚመረጠው ሰው የኋላ ታሪኩ እና ስብዕናው የተቀሩትን እስረኞች ሊወክል የሚችል ቢሆን ይመረጣል። በቀለን የመረጥነው መስፈርቱን ስለሚያሟላ ነው። ከፍተኛ የተቃዋሚ አመራር በመሆኑ ታዋቂ ከመሆኑም በተጨማሪ፤ በተደጋጋሚ መታሰሩ "የፖለቲካ እስረኛ" የሚለውን ሐሳብ በጥሩ ሁኔታ ይወክላል። በተጨማሪም መምህር በመሆኑ የማኅበረሰቡ መካከለኛ መደብ አካል ነው። በቀለ በሰላማዊ ትግል እንደሚያምን አስቀድሞ የታወቀ ጉዳይ መሆኑ፣ መንግሥት የፖለቲካ እስረኞችን የሚወነጅልበትን የ«አሸባሪ» ክስ ለማርከስ ይረዳል። በወቅቱ በጉዳዩ ላይ ስንወያይ አንድ ሰው «ፊቱ እራሱ ምስኪን ኦሮሞ ይመስላል» በማለት እንደተናገረው፤ ለዘመቻችን ጥሩ ምርጫ እንደሆነ ተስማማን። በአሜሪካ የሚኖረው ያዴሳ በጂዓ እነዚህን ሁሉ ሐሳቦች አካቶ በቀለን የፖለቲካ እስረኞች ሁሉ ተወካይ የሚያደርግ ሥዕል ሥሎ ነበርና በስፋት ተጠቀምንበት።

"የፖለቲካ እስረኞች ይለቀቁ" የሚለውን የማኅበራዊ ሚዲያ ዘመቻ እንደጀመርን ሕዝቡ በማስተር ፕላኑ ላይ በተቀዳጀው የድል ወኔ ከጎኑ የታሰሩትን ለማስለቀቅ ወደ ተቃውሞ ተመለሰ። በቂ ዝግጅት ተደርጎ ስለነበር የካቲት 2008 ዓ.ም ከበፊቱ የበለጠ ጠንካራ ተቃውሞ በሁሉም ዞኖች ተጀመረ።

በዚህኛው ዙር የገበሬው ተሳትፎ በከፍተኛ ደረጃ ጨመረ፤ መንግሥትም በከተሞች ተወስኖ የነበረውን እሥራት እና ግድያ እስከ ገጠር አፋፋመ። ለምሳሌ በምዕራብ አርሲ ዞን ሻሸመኔ አካባቢ፣ አባሮ በተባለ ሰፈር አንዲት ነፍሰጡር እና የዘጠኝ ልጆች እናት በቤቷ መግደሏ ከፍተኛ ቁጣ በማስከተሉ የሀገር ሽማግሌዎች በይፋ መንግሥት ላይ ጦርነት አወጁ። አመጹን ለማዳፈን የአጋዚ ክፍለ ጦር ወታደሮች ወደ ቦታው ተሰማርተው በጅምላ ሰው በመጨፍጨፋቸው፤ የአጄና ሻላ አካባቢ ገበሬዎች ባለ በሌለ መሣሪያቸው ለመከላከል ተገደዱ። አጋዚዎች ዲሽቃ እና ባዙቃ የመሳሰሉ ከባድ መሣሪያዎችን ተጠቅመው ብዙ ሰዎችን ፈጁ።

«ማስተር ፕላኒ» የተሰኘው የጫላ ቡልቱሜ ዘፈን ተቃውሞው ከተጀመረ አንስቶ የትግል

ዜማ ሆኖ ነበር። በድግስ ቦታ፣ በሱቆች እና በመሰሰሉት ቦታዎች ይከፈታል፤ OMN እየደጋገመ ያስደምጣል። እዚህ ላይ በቀለ ገርባ ደጋግሞ የሚያወራው ቀልድ ነበር። «አንዱ ፓስተር ሙዚቃ ቤት ሄዶ መዝሙሮችን መርጦ በሲዲ እያስገለበጠ "የጫላን ጫንልኝ ቤቴ ስደርስ እሰርዘዋለሁ" በማለት ተናገረ» ያለው፤ ከእውነት የራቀ አይመስልም።

መንግሥት ዘፈኑ ሕዝቡን በማነሳሳት ረገድ ያለውን ሚና ተገንዝቦ ለማገድ ወሰነ። በሥራ ቦታ እና በትራንስፖርት ላይ ዘፈኑን ሲከፍቱ በተገኙት ላይ ድብደባና እሥራት አጠናክሮ ቀጠለ። በሰርግና መሰል ማኅበራዊ ድግሶች ላይ የጫላ ዘፈን ተመራጭ ከመሆኑ የተነሳ ዝግጅቶቹ የጥቃት ኢላማ ሆኑ። ለምሳሌ በኢሉ አባቦር ዞን አንድ ሰርግ ላይ የጫላ ዘፈን ተከፍቶ ሳለ የመንግሥት ወታደሮች ደርሰው በተፈጠረ ግብግብ ሙሽሮቹ ተገደሉ። በተመሳሳይ ሁኔታ ሻሸመኔ አካባቢ ሰርገኞችን የጫነ መኪና ዘፈኑን እያዘፈነ ሲሄድ የመንግሥት ወታደሮች ተኩስ ከፍተው ሙሽራዋን እና ሌሎች የሰርገኞቹን አባላት ገደሉ። ይህም ከፍተኛ ቁጣ አሥነስቶ ተቃውሞ እና ብጥብጥ ቀሰቀሰ፤ ሙሽሮቹን የገደለው የአጋዚ ጦር እና የኦሮሚያ ፖሊስ ተጋጭተው ተታኮሱ። የኦሮሚያ ፖሊስ አባል የነበረው ኮንስታብል ሙስጠፋ ሁሴን አፈ-ሙዙን ሕዝቡን እየገደሉ ወዳሉት የአጋዚ ወታደሮች በማዞር በርካቶችን ገድሎ ሌሎችን በማቁሰል በመጨረሻም ተሰዋ።

የኦሮሚያ ፖሊስ የአገዛዙ የጭቆና በትር ሆኖ እንዳይቀጥል ቀድሞውኑ ውስጥ ውስጡን ሰፊ ሥራ ሲሰራ ነበር። ይህ ሥራም በአጋዚ እና በኦሮሚያ ፖሊስ መካከል እያደር መቃቃር እና ጥርጣሬን በመፍጠር የሥርዓቱን የጸጥታ ኃይል ከፋፍሎ የማፈን አቅሙን ማዳከም ነበር።

በሚዲያ በኩል ሲደረግ ከነበረው የማማለል ዘመቻ ጎን ለጎን፤ ኅብረተሰቡ የኦሮሚያን ፖሊስ በማቅረብ የአጋዚን ጦር እንዲጸየፍ ተሰራ። ፖሊስ የሕዝብ ወዳጅ፣ አጋዚ ደግሞ የመንግሥት የጭቆና መሣሪያ መሆኑን በስፋት አሰራጨን።

በውስጥም አንዳንድ ለትግሉ አጋርነት ያላቸው የኦሮሚያ ፖሊስ ከፍተኛ አዛዦች አባሎቻቸው ሕዝብን ከመጉዳት እንዲቆጠቡ እና ለገዛ ሕዝባቸው ተቆርቋሪነት እንዲያሳዩ አድርገዋል። ሙስጠፋ ሁሴን የወሰደው እርምጃ ለስልቱ ስኬት ማረጋገጫ ሲሆን፣ የእሱን ገድል ደግመን ደጋግመን በሚዲያ በመዘከር ሌሎች ፖሊሶችም የእሱን ፈለግ ተከትለው ለሕዝባችን አጋርነት እንዲያሳዩ ተጠቀምንበት። በሂደትም የኦሮሚያ ፖሊስ በብዙ ቦታዎች በተናጠልም ሆነ በቡድን ሕዝቡን ለማጥቃት የሚሰጠውን ትዕዛዝ ባለመቀበል፤ ካልተቻለም የሚሰጠውን የስምሪት ትዕዛዝ አስቀድሞ ለቄሮ በማሳወቅ አስፈላጊው ጥንቃቄ እንዲደረግ አገዘ። ፖሊስ ለትግሉ ተቆርቋሪነት ማሳየቱ ቄሮ እና ሕዝቡን የበለጠ ሲያበረታታ፣ መንግሥት በጸጥታ ኃይሉ ላይ ጥርጣሬ እንዲያድርበት አደረገ።

የትኛውም መንግሥት በሥልጣን ላይ ለመቆየት የፖለቲካ፣ የኢኮኖሚ፣ የጸጥታ፣ ማህበራዊ ወዘተ ተቋማት ያስፈልገዋል። እነዚህን ተቋማት የሥልጣን ምሰሶዎች (pillars of power) እንላቸዋለን። አንድን አገዛዝ ለማሸነፍ እነዚህን የሥልጣን ምሰሶዎች ማዳከም አስፈላጊ ነው። የትጥቅ ትግል እነዚህን ምሰሶዎች በማጥፋት ሥርዓቱን ለመጣል ይሞክራል። በሰላማዊ ትግል ውስጥ ደግሞ እነዚህ ምሰሶዎች አገዛዙን ለማገልገል እንዳይችሉ ወይም እምቢ እንዲሉ ለማድረግ የተለያዩ ዘዴዎችን በመጠቀም ይሰራል።

ከሥልጣን ምሰሶዎቹ ሁሉ ለአምባገነናዊ አገዛዝ አስፈላጊውና መለስ ዜናዊ ሲለው እንደነበረው

የሥርዓቱ የመጨረሻ ምሽግ የጸጥታ መዋቅር (security apparatus) ነው። የጸጥታ መዋቅሩ መከፋፈል እና እርስ በእርስ አለመተማመን እንዲሁም የተወሰነው ክፍል ወደ ሕዝባዊ ትግል መቀላቀል፣ የአምባገነናዊ ሥርዓቱን የማፈን አቅም በመሸርሸር ውድቀቱን ያፋጥናል። ስለዚህም የኦሮሚያ ፖሊስ ለሕዝብ መወገን መጀመሩ የቄሮ ትግል ወሳኝ ደረጃ (turning point) ላይ መድረሱን አመላካተ።

አንድ ማስገንዘብ የምፈልገው ነገር የኦሮሚያን ፖሊስ ወደ ሕዝባዊ ትግሉ ለመሳብ የተተገበረው ዘዴ መከላከያ ሠራዊት ላይ አልተሞከረም። የሠራዊቱ አባላት በሕዝቡ ላይ ጥይት እንዳይተኩሱ አልፎ አልፎ ጥሪ እናደርግ ነበር። የቄሮ አስተባባሪዎች ከተወሰኑ ከፍተኛ ወታደራዊ ባለሥልጣናት ጋር ግንኙነት ቢኖረንም እንደ ፖሊስ በግልጽ ተቃውሞ እንዲያደርጉ ግን አልተሰራም።

ይህ ደግሞ ቀድሞውኑ አስበንበት የወሰንነው ጉዳይ ነው። የመጀምሪያው ምክንያታችን የመከላከያ ሠራዊት መዋቅር ሁሉንም ብሔረሰቦች ያካተተ ስለሆነ ለአንድ ብሔር ትግል በአንድነት መወገን አይችልም። የኦሮሞ ተወላጅ የሆኑ የመከላከያ ሠራዊት አባላትን ማሳመን የሚቻል ቢሆንም ለትግሉ ተጨባጭ ጥቅም ሳያስገኙ ለአደጋ ማጋለጥ ይሆናል። በአንዳንድ ቦታዎች በስሜት ተገፋፍተው የተቃወሙ ወታደሮች ያለምንም ውጤት ለእስር እና ግድያ ተዳርገዋል።

ሁለተኛው እና ዋናው ምክንያታችን የሀገሪቱ ብሔረሰቦች በጋራ ከሚጋሯቸው የፌደራል ተቋማት መካከል የመከላከያ ሠራዊት ዋነኛው በመሆኑ፤ በተቃውሞው ውስጥ የኦሮሞ ተወላጆችን ብናሳትፍ ተቋሙ በብሔር ተከፋፍሎ ሊፈርስ ይችላል የሚል ፍርሀት ስለነበረን ነው። የመከላከያ በብሔር መከፋፈል ወደለየለት የእርስ በእርስ ጦርነት አምርቶ ሀገሪቷን ሊያፈርሳት ይችላል ብለን ሠጋን። ስለዚህም የመከላከያን የመከፋፈል አደጋ ለመቀነስ፣ የሠራዊቱ መኮንኖች እና አባላት በትግሉ ውስጥ ቀጥተኛ ተሳትፎ እንዲኖራቸው አልተደረገም። ሚናቸው የመንግሥትን እቅድ እና ስምሪት በድብቅ ለቄሮ አስተባባሪዎች ማስተላለፍ ላይ የተገደበ ነበር። አንዳንድ የሠራዊቱ መኮንኖች ከጸጥታው ኃይል የስምሪት መረጃ ባለፈ፣ የፖለቲካ አመራሩን እቅድ እና ስልት የሚጠቁሙ ምስጢሮች ለቄሮ በማካፈል ከፍተኛ ሚና ተጫውተዋል። ይህ መረጃ የትግል ዘመቻዎችን ለማቀድ እና ሊከሰቱ የሚችሉ ጉዳቶችን በመቀነስ ረገድ ትልቅ ጥቅም አበርክቷል።

ከዚህ የሀገር መከላከያ ጉዳይ ጋር በተያያዘ የማስታውሰው አንድ ክስተት አለ። አንድ ሰው የመከላከያ መኮንኖች ክበብ ውስጥ እንደሚሰራ እና እርምጃ ለመውሰድ እንደሚፈልግ በፌስቡክ ጻፈልኝ። ያቀደው እርምጃ እዚያ የሚመገቡትን ጄኔራሎች መርዘ መግደል እንደሆነም አከለበት። ለዚህ እርምጃ መርዝ ብቻ እንደሚያስፈልገውና በዚህ ረገድ እንድተባበረው ጠየቀኝ። መረጃው ባልተጠበቀ ሁኔታ ስለመጣና የመንግሥት የስለላ ክፍል ሊሆን ይችላል የሚል ጥርጣሬ ሰለነበረኝ አስቤበት እመልስልሀለሁ አልኩት። የተወሰነ ማጣራት ሳድረግ ሰውዬው እውነትም ያለው ቦታ እንደሚሰራና ያሰበውን እርምጃ ለመተግበርም በደንብ እንደሚመቸው አረጋገጥኩ። ነገር ግን ሊወስደው ያቀደው እርምጃ ያለውን ጥቅምና ጉዳት ሳውጠነጥን ጉዳቱ እንደሚበልጥ ገመትኩ። እሱ እንዳሰበው ጥቂት ከፍተኛ ባለሥልጣናትን መርዞ መግደል አገዛዙን ለጊዜው ያስደነግጣል፤ ሠራዊቱ

እየገደላቸው ላሉ ኦሮሞዎችም በቀል ሊሆን ይችላል። እነዚያን ባለሥልጣናት መግደል ግን አገዛዙን አያስወግድም፤ ተቋሙ በሙቶዎች የሚቆጠሩ መኮንኖች ስላሉት በተገደሉት በታ ሌሎች ተተክተው ሥራውን ይቀጥላሉ።

በዚህ አደጋ ሽፋን ግን ብዙ የኦሮሞ ወታደራዊ እና ፖለቲካዊ አመራሮችን ማባረር፣ ማሰር እና መግደል ይችላሉ። ይህ ደግሞ በመከላከያ ሠራዊት ውስጥ የኦሮሞን ድርሻ እጅግ ስለሚጎዳ ለትግሉ ኪሳራ ነው። በተጨማሪም የእነዚህ ከፍተኛ ባለሥልጣናት መገደል በበታች አመራሮች መካከል የበቀል ስሜት በመቀስቀስ ሕዝብን በጭካኔ እንዲጎዱ ስለሚያደርግ አገዛዙን ሊጠቅም ይችላል። ከዚህ በመነሳት ሰውዬው ያሰበውን እርምጃ እንዳይወስድ በማሳመን አስተውኩት። ሀገር ቤት ከገባሁ በኋላ ሊገድላቸው ያሰባቸውን የመከላከያ መኮንኖች በአካል ባገኘኋቸው ወቅት ሁሉ የእሱ እቅድ ትዝ ይለኛል።

## 7.5. ፈተና

በ2015 እና 2016 የትምህርት ዘመን በኦሮሚያ ውስጥ ሕዝባዊ አመጽ በተከታታይ ስለሚደረግናትምህርት ቤቶችም ስለሚዘጉ የመማር ማስተማሩ ሂደት በአግባቡ አልተካሄደም። ተማሪዎቹም በተቃውሞው በግንባር ቀደምነት ስለሚሳተፉና ልባቸው ትምህርት ላይ ስላልነበር፤ የ12ኛ ክፍል ሀገር አቀፍ የዩኒቨርሲቲ መግቢያ ፈተና (Entrance Exam) ለመውሰድ በቂ ዝግጅት እንዳላደረጉ ግልጽ ነው። በዚህ ምክንያት መንግሥት ፈተና የሚሰጥበትን ቀን እንዲያራዝም ጥያቄ አቀረብን፤ ይህንንም መጀመሪያ በመንግሥት ባለሥልጣናት በኩል ለማሳመን ተሞከረ። በመቀጠል የተማሪ ቤተሰቦች በአካባቢያቸው ወደሚገኙ ትምህርት ቢሮዎች በአካል ሄደው እንዲማጸኑ ተደረገ፤ መንግሥት ግን በእምቢታው ጸና። ይልቁንም ፈተናውን በተባለው ጊዜ በመስጠት ትግል ላይ የነበሩ እና ያልተዘጋጁ ተማሪዎችን ለመበቀል እንደ መልካም አጋጣሚ ለመጠቀም ፈለገ።

መንግሥት በውስጥ የሚደርሰውን ተማጽኖ ለመስማት ፈቃደኛ አለመሆኑን ስንረዳ፤ ፈተናው እንዲራዘም በግልም በሚዲያም ጠይቀን እምቢ የሚሉ ከሆነ ፈተናውን የሚያደናቅፍ እርምጃ እንደምንወስድ አስታወቅን። ይህን ስንል መንግሥት በተለመደው የአመጽ ስልት ፈተናውን ለማደናቀፍ ያሰብን መሰለው። ነገር ግን በፈተና ቀን አመጹ ቢኖር የሚያውከው የኦሮሚያን ክልል ብቻ ስለሆነና የሚጎዱት በመንግሥት ላይ ሲያምጹ የነበሩ ተማሪዎች ስለሚሆኑ፤ መንግሥት እንደ መልካም አጋጣሚ ሳይቆጥረው አልቀረም።

እኛ ግን ሌላ እቅድ ነበረን፤ ይህንንም ለመንግሥት ግልጽ አደረግን። ስልታችን ፈተናውን ከቀኑ በፊት በማኅበራዊ ሚዲያ ለጥፎ ማክሸፍ እንደሆነ በግልጽ አስጠነቀቅን፤ መንግሥት ግን ፈተናውን ማውጣት እንደማንችል በማሰብ ለጥያቄያችን መልስ ሳይሰጥ ቀረ። ከዚያም ፈተናውን አውጥቶ ለላከልን ሰው እስከ አንድ መቶ ሺህ ብር እንደምንሰጥ በፌስቡክ አስታወቅኩኝ። አንዳንድ ባለሀብቶች እኛ እንዳልነው ፈተናውን ማውጣት የሚቻል ከሆነ የገንዘቡን መጠን ወደ ሚሊዮን ብር ከፍ እንድናደርገው እና ወጪውንም እንደሚሸፍኑ ቃል ሲገቡልን ይህንኑ በፌስቡክ በኩል ለጠፍኩ።

ለፈተናው አንድ ሳምንት ገደማ ሲቀረው፣ የተለያዩ ሰዎች ፈተናውን መላክ ጀመሩ፤ የሚላኩት ግን በብዛት የውሸት ነበሩ፤ ያለፉትን ዓመታት ፈተና ቀኑን በመሠረዝ ሊያታልሉኝ ሞከሩ። ከዚህ የተነሣ የተላኩትን በሙሉ በጥርጣሬ መመልከት ጀመርኩ። መጀመሪያ ላይ እየመጡ የነበሩት ፈተናዎች ከወረቀት ላይ ስካን የተደረጉ ሲሆን፤ በኋላ ግን ከኮምፒዩተር የወጣ (soft copy) መምጣት ጀመረ። ጥርጣሬያችን እንዳለ ሆኖ ፈተናውን እጃችን እንደምናስገባ ከፍተኛ ተስፋ ስለነበረን በሚዲያ በኩል እንደምናከሽፈው መዛታችንን ገፋንበት። ጥቂት ቀናት ሲቀሩ የሚላኩልን ፈተናዎች በአብዛኛው እየተመሳሰሉ ስለመጡ እውነተኛውን ስለማግኘታችን እምነትታችን ጠንካራ ሆነ። መቶ በመቶ እርግጠኛ መሆን ስላለብን ፈተናዎቹ ለክልሎች እስኪከፋፈሉ ጠብቀን እኛ ጋር ከደረሱት ጋር ማመሳከሩን መረጥን። በዚህም መሠረት ሦስት ቀን ሲቀረው ፈተናው ከፊንፊኔ ወደ ክልሎች ሲላክ የምናምናቸው ሰዎች አውጥተው ልከውልን እጃችን ላይ ካለው ጋር አመሳክረን አረጋገጥን።

በመቀጠል የመንግሥት አካላትን አነጋግረን ፈተናው እንደደረሰን እና ወደ ሌላ ጊዜ ካላዘወሩ በማኅበራዊ ሚዲያ ለማሰራጨት እንደምንገደድ ብንነግራቸውም አላመኑንም። በፈተናው ዋዜማ፤ አንድ የትምህርት ሚኒስቴር ባለሥልጣን ስልክ አግኝቼ የደረሰኝን ፈተና ቅጂ ስልክለት በፈተና አሥተዳደር ውስጥ ያለ ሌላ ሰው አነጋግሮ የላኩለትን አሳይቶት ለማረጋገጥ ሞከረ። ካረጋገጡ በኋላም የመንግሥት ከፍተኛ ባለሥልጣናትን ማሳመን ስላልቻሉ የመጨረሻውን ማስጠንቀቂያ በፌስቡክ በኩል ለጠፍን። የመንግሥት ባለሥልጣናት ፈተናው ወጣ የሚለው ወሬ ሐሰት መሆኑን በሚዲያ እየወጡ ተናገሩ። ከዚህ በላይ ከእነሱ ጋር መድከም እንደማያስፈልግ በማመን የፈተናውን የመጀመሪያ ገጽ በማኅበራዊ ሚዲያ ላይ ለጠፍኩ። የመንግሥት ሰዎች አሁንም በመገናኛ ብዙኃን በመቅረብ «ፈተና አልወጣም፤ እየተለጠፈ ያለው የውሸት ነው» በማለት መግለጫ ሰጡ።

የመጀመሪያ ቀን ለመስጠት የታቀዱትን ሁለት ፈተናዎች (ሒሳብ እና እንግሊዝኛ) ሙሉውን ሰዎች ሰርተው የላኩልኝን ከመልሶቻቸው ጋር አያይዤ ለጠፍኩ። መንግሥት ግን ዓይኑን ጨፍኖ ጠዋት ፈተና መስጠት ጀመረ። ተማሪዎች ምሽት ላይ የፈተና ጥያቄዎችን ከፌስቡክ ገልብጠው ስለሄዱ ያንኑ በመልስ ወረቀቱ ላይ መሙላት ጀመሩ፤ ላላገኙትም አስተላለፉ። ሲፈትኗቸው የነበሩ መምህራን ያዩትን ለአለቆቻቸው ስላሳወቁ፤ በመጨረሻም ቢሆን መንግሥት ፈተናውን ለመሠረዝ ተገደደ። እኛም ግንቦት 22 ቀን 2008 ዓ.ም ፈተናውን የማክሸፍ ዘመቻ በድል መወጣታችንን አሳወቅን።

የፈተናው እርምጃ የቄሮን ትግል ወደ ሌላ ደረጃ ከፍ አደረገው። እስከዚያ ጊዜ ድረስ የምናደርገው ጫና በኦሮሚያ ክልል የተገደበ ነበር። ፈተናው መውጣቱ በመላው ሀገሪቱ ያሉ ትምህርት ቤቶችን ስላወከ የቄሮ ትግል በሁሉም ክልሎች የተማሪ ቤተሰቦች ቤት በመግባቱ፤ የእኔ እና የቄሮ ስም የወሬ ማሟሻ ሆነ። ልክ እንደ ማስተር ፕላኑ የመንግሥትን እጅ ጠምዝዘን ፈተናው እንዲሠረዝ ማስገደድ መቻላችን ለቄሮ ትግል የሚሰጠው መልካም አስተያየት እጥፍ ድርብ እንዲሆን አደረገ።

አዲስ የሚዘጋጀው ፈተና ቢያንስ በሁለት ወራት እንዲራዘም ጠየቅን። መንግሥት በአንድ ወር ለማራዘም ስላቀደ በእቅዱ እንድስማማ አንድ ከፍተኛ ባለሥልጣን ወደ አሜሪካ ልከው ተማጸኑኝ። ጉዳዩን ከዚህ የበለጠ መግፋት የትምህርት ዘመኑን በማቃጠል ቤተሰብ እና ተማሪዎችን ሊያስቀይም ይችላል ብለን ስለጠረጠርን የመንግሥትን ተማጽኖ ተቀበልን። አዲስ ፈተና ለመስጠት ያስታወቁት ቀን ከኢድ በዓል ጋር በመገጣጠሙ እንዲቀይሩት በጠየቅናቸው መሠረት ከበዓሉ ቀን ለማሳለፍ ተስማሙ።

ፈተናውን ለማውጣት በሚደረገው ትግል አንድ አሥቂኝ ገጠመኝ ተከሰተ። በወቅቱ ጓደኛዬ ገመቹ ገልገሉ ሊያገባ እየተሰናዳ ነበር። ከሠርጉ በፊት በነበሩ ወራት በኦሮሚያ ሰፊ ሕዝባዊ አመጽ ይካሄድ ስለነበር ውጪ ሀገር ያለው ሕዝብ ልቡ ወደ ሀገር ቤት አድልቷል። ገመቹም አንድ ቀን «በሰርጌ ቀን የሕዝቡ ሐሳብ እንዳይበታተን እባክህ ቄሮ ዕረፍት እንዲወስድ አድርግልኝ» ብሎ በቀልድ መልክ ለመነኝ፤ የሆነው ግን በተቃራኒው ነበር። ፈተናውን ያወጣንበት ዋዜማ እና ሰርጉ ተገጣጠመ። ሙሽሮቹ ሲገቡ አዳራሽ ውስጥ ተቀምጬ ፈተናውን በኮምፒዩተር እየለጠፍኩ ነበርና ቀና ስል ከገሜ ጋር ዓይን ለዓይን ተጋጨን። ጭንቅላቱን በአግራሞት እየነቀነቀ «ነገሩን አረጋጋልኝ ባልኩህ የባሰውኑ አጋጋልከው? ጭራሽ ኮምፒዩተር ይዘህ ሰርጌን ወደ ቢሮህ ቀየርክልኝ» ሲል ቀለደ።

## 7.6.ታላቁ ሰልፍ

የማስተር ፕላኑን ትግል በድል ማጠናቀቅ ያስገኘልንን ሞራል በመጠቀም የፖለቲካ እስረኞችን ለማስፈታት በየካቲት 2008 ዓ.ም የተጀመረው ዘመቻ፤ ግንቦት ላይ ደግሞ ፈተናውን ማክሸፍ በመቻላችን ተጋግሎው የበለጠ ቀጠለ። ነገር ግን ጊዜው እየረዘመ በሄደ ቁጥር ተቃውሞው ቀድሞ እንደነበረው በሁሉም ቦታዎች መሆኑ እየቀነሰ ሄደ። በተለይ ክረምት መምጣቱ እና የአዝመራ ወቅት መድረሱ አርሶ አደሩ በተቃውሞ መሳተፉን ቀንሶ በማሳው ላይ እንዲያተኩር አስገደደ። እንደ ሐረርጌ ባሉ አንዳንድ ዞኖች ግን አመጹ ተባብሶ በመቀጠል ከፍተኛ መሥዋዕትነትን አስከተለ።

ሕዝቡ እልህ ውስጥ በመግባት ከሰላማዊ ትግል ስልቶች እየወጣ የመንግሥትን ጦር በጉልበት ወደ መጋፈጥ ተሸጋገረ። ለምሳሌ በጋራ ሙለታ፣ ዶጉ ዘን፣ በግራዋ ወረዳ ለገ ሀረዋ የተባለ ቦታ ፋጡማ አሕመድ አባድር የምትባል ሴት የመንግሥት ወታደር በዘነዘና በመምታት ክላሽ እስከ መቀማት ደረሰች። በአወዳይ እና በሌሎችም ቦታዎች ግጭቶች ተከስተው የብዙ ሰዎች ሕይወት ለአደጋ ተጋለጠ። ይህ ሁኔታ የስልት ለውጥ እንድናደርግ አስገደደን፤ ሕዝቡም ከተበታተነ ይልቅ የተቀናጀ ተቃውሞ ማድረግ እንደሚያስፈልግ ወተወተን። የቄሮ አስተባባሪዎች በጉዳዩ ላይ ተወያይተን በተበታተነ መልኩ እየተደረገ ያለው አመጽ ከጥቅሙ ይልቅ ጉዳቱ እያመዘነ ስለሆነ ሀገር አቀፍ የተቀናጀ ተቃውሞ እንዲዘጋጅ ተወሰነ።

ከዚህ ውስኔ በመነሳትም በመላው ኦሮሚያ በአንድ ቀን ሰላማዊ ሰልፍ ለመጥራት ዝግጅት ተጀመረ። ይህ አጠቃላይ ሰልፍ አስፈላጊ የሆነባቸው አራት ምክንያቶች ነበሩ።

1. ተቃውሞው በተበታተነ እና በተቆራረጠ መልኩ መቀጠሉ፣ በንቃት እየተንቀሳቀሱ ያሉ አካባቢዎች ብቸኝነት ተሰምቷቸው እና ተስፋ ቆርጠው ከትግል ሊወጡ ስለሚችሉ፤
2. አንዱ ዞን ሲቃወም ሌላው ዝም ማለቱ በዞኖች መካከል ጥርጣሬ እና ቅሬታ ሊፈጥር ስለሚችል፤
3. ተቃውሞው በቀጠለባቸው ዞኖች ከሰላማዊ ትግል ስልት በመውጣት ወደ ብጥብጥ መሸጋገር ከጥቅሙ ይልቅ ጉዳት ስላለው ፈር ማስያዝ በማስፈለጉ፤
4. የመጨረሻው እና ወሳኙ ምክንያት የቄሮ እንቅስቃሴ የደረሰበትን ደረጃ እና የሕዝቡን አቅም ለመገምገም ነበር።

አንድ ሰላማዊ ትግል እያደገና እየጠነከረ ከሄደ መነሻው ላይ ከነበረበት የተቃውሞ (protest) ደረጃ ወደ የንቅናቄ (movement) ደረጃ ይሸጋገራል። ይህ የሚታወቀው በተቃውሞው ላይ የሚሳተፈው የሕዝብ ቁጥር፣ ስብጥር እና የመሬት ስፋት ከጊዜ ወደ ጊዜ እየጨመረ ከሄደና ተቃውሞውን ያለማቋረጥ ማካሄድ ከተቻለ ነው።

ከላይ እንደተገለጸው በ2008 ዓ.ም ክረምት፣ መጀመሪያ አካባቢ ተቃውሞው በተቆራረጠ መልክ ሲካሄድ በመቆየቱ፣ የቄሮ እንቅስቃሴ እያደገ ስለመምጣቱና በመላው ኦሮሚያ ሰፊና

ጠንካራ የሆነ ድጋፍ (critical mass) መፍጠሩ ላይ ጥርጣሬ ነበር። መንግሥትም "የትም አትደርሱም!" በሚል የፕሮፓጋንዳ ዘመቻ ሕዝቡን ተስፋ ለማስቆረጥ ሞከረ። በመሆኑም የንቅናቄያችንን አቅም ለመገምገም፣ የመንግሥትን ፕሮፓጋንዳ ለማክሸፍ እና ሕዝቡ በቄሮ ላይ ያለውን እምነት (public confidence) ለማጠናከር አጠቃላይ የተቃውሞ ሰልፍ በመጥራት ስኬትን ለማረጋገጥ ጠንካራ ዝግጅት ተደረገ። በዚህም መሠረት እ.አ.አ ኦገስት 6 ቀን 2016 (ሐምሌ 30/2008 ዓ.ም) በመላው ኦሮሚያ የተቃውሞ ሰልፍ ለመጥራት ወሰንን። ይሁን እንጂ ቀኑ ረዘም ላለ ጊዜ አስቀድሞ እንዳይገለጽ ከስምምነት ተደርሶ፣ ትኩረቱ በሀገር ውስጥ አደረጃጀት እና በሚዲያ በኩል ሕዝቡን ማዘጋጀት ላይ ሆነ። አስቀድሞ ያልተነገረበት ምክንያት መንግሥት በአግባቡ ተዘጋጅቶ ለማክሸፍ ጊዜ እንዳያገኝ ነበር።

ዝግጅቱ ከተጠናቀቀ በኋላ ሰልፉ አንድ ሳምንት ሲቀረው ቀኑ በይፋ ታወጀ፤ ሰፊ የሚዲያ ዘመቻ መካሄዱም ቀጠለ። ለማኅበራዊ ሚድያ ዘመቻ #GrandOromoProtests የሚለው ሃሽታግ ተመረጠ። ይህ ታላቅ ሰልፍ ለወደፊት የኦሮሞ ትግል እንዴት ወሳኝ እንደሆነ ደጋግመን ገለጽን። ለድጋፍ ሰልፉ እየተደረጉ ያሉ ዝግጅቶችን የሚያሳዩ ፎቶዎች እና ቪዲዮዎችን ፌስቡክ ላይ በመለጠፍ ሌሎችም በታዎች ዝግጅታቸውን እንዲያፋጥኑ አበረታታን። ለታላቁ ተቃውሞ ጥሪ የተላለፈበት እና የሰልፉ ቀን በጣም ስለተቀራረበ ሕዝቡ ለመስማት እና ለመዘጋጀት በቂ ጊዜ ስለማይኖረው አይሳካም የሚል ጥርጣሬ ነበረን። በሕዝቡ ውስጥ ያሉት አስተባባሪዎች ግን ከጥሪው አስቀድመው ውስጥ ውስጡን ሲያደራጁ እና ሲቀሰቅሱ ስለነበር ለስኬታማነቱ ጽኑ የሆነ በራስ መተማመን አዳበሩ።

ለሰልፉ መሳካት እኛ ካደረግነው ዝግጅት በተጨማሪ የመንግሥት እርምጃ ትልቅ ሚና ነበረው። የወቅቱ የኦሮሚያ ክልላዊ መንግሥት ፕሬዝዳንት ሙክታር ከድር እና ጠቅላይ ሚኒስትር ኃይለማርያም ደሳለኝ በመገናኛ ብዙኃን ተከታትለው በመቅረብ «ምንም ዓይነት ሰላማዊ ሰልፍ አልተጠራም… ሰላማዊ ሰልፍ በሚወጣ ሰው ላይ የማያዳግም እርምጃ እንወስዳለን» በማለት ሕዝቡን በማስፈራራት ሰልፉን ለማስቀረት የሰጡት መግለጫ የሰልፉን ጥሪ በኢንተርኔት ላላየው የገጠሩ ሕዝብ ከጆሮው እንዲደርስ አደረገ። የበታች ካድሬዎችም የፕሬዝዳንቱን እና የጠቅላይ ሚኒስትሩን መመሪያ በመከተል በገበያ ቀናት የድምፅ ማጉያ ይዘው «እሑድ ምንም ዓይነት ሰልፍ የለም» በማለት ኢንተርኔት፣ ሬዲዮ እና ቴሌቪዥን ለሌላቸው ገበሬዎች አደረሱልን። ሕዝቡም «ሰዎቹ የሚያወሩት ስለምን ሰልፍ ነው?» በማለት ሲጠይቅ ቄሮዎቹ ጉዳዩን በጆሯቸው ሹክ በማለት እንዳይቀሩ ይነግሯቸዋል።

ከቄሮ አስተባባሪዎች የግንኙነት ማዕከል አንዱ ስለነበርኩ መረጃዎችን በመቀበል እና በማስተላለፍ ተጠምጄ፤ እንቅልፍ የምተኛው ቢበዛ በቀን ሁለት ሰዓት ብቻ ነው። ወቅቱ በሰሜን አሜሪካ ያሉ ኦሮሞዎች የእግር ኳስ ጨዋታ (Oromo Soccer Federation of North America OSFNA) ስለነበር፤ ውድድሩን ለመሳተፍ ከተለያዩ በታዎች የመጡ ሰዎች OMN ቢሮ በመምጣት ያግዙኛል። ያለውን ዝግጅት ለመከታተል እና ለማበረታታት ብዬ የሀገር ውስጥ አስተባባሪዎችን በማነጋገር፣ በማኅበራዊ ሚዲያ እንቅስቃሴዎች ላይ በመሳተፍ፣ እንዲሁም በመገናኛ ብዙኃን ላይ ቀርቤ በትንታኔ መልክ ሕዝቡን በማነሳሳት ሥራ ተወጥሬ ለእንቅልፍ የሚተርፈኝ ሰዓት በጣም ትንሽ ነበር። ያለኝን አጭር ሰዓት እንኳን በየመሀሉ እያቆራረጥኩ ሸለብ እላለሁ እንጂ አከታትዬ አልተኛም።

በዚህ መሀል አርፋሴ በምጥ ተይዛ ወደ ሆስፒታል እንደምትሄድ መልዕክት ላከችልኝ፤ ሄጄ ለጥቂት ጊዜ ተቀመጥኩና አስቸኳይ ጉዳይ ሲመጣ ወደ ቢሮ ተመለስኩ። ከአንዱ ሥራ ወደ ሌላ ስሽጋገር ልጄ ኦሮሞ እኔ በሌለሁበት ለሰልፉ ጥቂት ቀናት ሲቀሩት ተወለደ። አርፋሴ አጠገቧ እንድገኝ ብትፈልግም ሁኔታዬን ተረድታ የልጃችንን ፎቶ ላከችልኝ፤ እኔም ሮጬ ሄጄ ልጄን አቅፌ ሳምኩት። አንድ ሰዓት ለማይሞላ ጊዜ አብሬያቸው ቆይቼ ወደ ቢሮ ተመልሼ ሥራዬን ቀጠልኩ። የኦሮሞን የእግር አሻራ ፌስቡክ ላይ ለጥፌ ደስታዬን ለሕዝብ አጋራሁ።

በዚህ ሁኔታ ታላቁ ሰልፍ የሚካሄድበት ቀን እየተቃረበ ሲመጣ መንግሥትን በዲፕሎማቶች በኩል በማነጋገር ሰልፉ እንደማይቀርና ያለምንም ሁከት ሙሉ በሙሉ በሰላማዊ መንገድ እንደሚካሄድ አስረዳሁ። መንግሥትም የኃይል እርምጃ እንዳይወስድ ብናስጠነቅቅም የመንግሥት አካላት ምላሽ ግን የተከፋፈለ ነበር። በመከላከያ በኩል ሰልፈኞቹ ሁከት እስካልፈጠሩ ድረስ ምንም ዓይነት እርምጃ እንደማይወስዱ ቃል ገቡ። በደኅንነት መሥሪያ ቤቱ በኩል የመጣው ምላሽ ግን ማስፈራሪያን ያዘለ ነበር። የፖለቲካው ክንፍ (የጠቅላይ ሚኒስትር ጽ/ቤት እና ፓርቲው) እርስ በእርስ የሚጋጭ አቋም አንጸባረቁ። መጀመሪያ ሊያስፈራሩን ሞከሩ፤ በመጨረሻ ግን የኃይል እርምጃ እንደማይወስዱ ጠቆሙ።

በተቃውሞው ዋዜማ (ኦገስት 5) OMN ላይ ቀርቤ የመጨረሻውን የጥሪ መልዕክት አስተላለፍኩ። የዚህን ሰልፍ አስፈላጊነት አጽንዖት ሰጥቼ በመናገር ሕዝባችን ወጣት፣ ሽማግሌ፣ ወንድ እና ሴት ሳይል በሰልፉ ላይ በመሳተፍ የቄሮ ጥያቄ የሰፊው ሕዝብ ጥያቄ መሆኑን እንዲያረጋግጥ ጥሪ አቀረብኩ። በሰልፉ ላይ የሰላማዊ ትግልን ሥነ ምግባር መከተል አስፈላጊ መሆኑንም አበክሬ ተናገርኩ። ይህ ሰልፍ የኦሮሞ ሕዝብ ፍትኃዊ ጥያቄዎቹን በሰላማዊ መንገድ ብቻ ለማስመለስ እንደሚታገል ለዓለም የማስተዋወቅ ዕድል መሆኑን በመጠቆም፤ የጦር መሣሪያም ሆነ የትኛውንም ዓይነት ስለታማ ነገር፤ ሌላው ይቅርና ዱላ እንኳን ይዘው እንዳይወጡ ምክረ ሐሳብ አቀረብኩ። በሚያሰሟቸው መፈክሮች ውስጥ ሌሎች ብሔሮችን ከሚያስቀይሙ ቃላቶች እንዲቆጠቡ፣ የእምነት ቦታዎችን፣ የንግድ ድርጅቶችን እና የሌሎች ብሔሮችን ንብረት እንዲጠብቁ አሳሰብኩ። «እውነት አለን፣ በአንድነት እንታገላለን፣ በስትራቴጂ እንመራለን፣ እናሸንፋለን!» በማለት በስሜት የተሞላ ንግግሬን አጠናቀኩኝ። መልዕክቱ በቴሌቪዥን እንደተላለፈ፣ አንድ የሰላሌ አዛውንት ልጃቸውን በማስደወል «እንዲሁ ባዶ እጃችሁን አንጠልጥላችሁ ውጡ ነው የምትለን?» ብለው ቁጣ እና አግራሞት በተሞላበት ድምፅ ጠየቁኝ። «አቦ እኔ ያለ ሽመል አንድም ቀን ከቤት ወጥቼ አላውቅም፤ ገበያም ሆነ ስብሰባ የምሄደው ሽመሌን ይዤ ነው። ሽመሌን ቤት ትቼ ወጣሁ ማለት ወንድነቴን ትቼ የወጣሁ ያህል ይሰማኛል። ውሻ ቢያባርረኝ ወይም እባብ እግሬ ላይ ቢጠመጠም በምን እከላከላለሁ?'' አሉ። እኔም ያለ ዱላ መውጣት ለምን እንዳስፈለገ ጊዜ ወስጄ አስረዳኋቸው። ሽማግሌው ይሆናል ወይም አይሆንም አላሉም። ከሰልፉ በኋላ ልጃቸውን ስጠይቀው ሽማግሌው ጠዋት ምንም ሽመል ይዘው እንዳልወጡ፤ ከተማ ሲደርሱ ግን እንጨት ከአጥር ላይ መዘው ይዘው ሰልፉን እንደተቀላቀሉ ነገረኝ።

የሰላማዊ ሰልፍ ወይም የገበያ እቀባ ዘመቻ ስናውጅ አንድ አመል የሆነብኝ ነገር ነበር። ዘመቻው ከታወጀበት ቀን ጀምሮ ያለ በቂ እንቅልፍ እሠራለሁ። ልተኛ ብል እንኳን ለረጅም ጊዜ እንቅልፍ ውስጥ መቆየት አልችልም፤ ቶሎ እነቃለሁ። በዘመቻዎቹ ዋዜማ ሰውነቴ

ቢደክምም ጭራሽ እንቅልፍ የሚባል በዓይኔ አይዞርም። ሌሊቱን ቁጭ ብዬ አድሬ ጠዋት ላይ ሰልፍ ሲወጣ ወይም እቀባው መጀምሩን የሚያሳይ ፎቶና ቪዲዮ እንደደረሰን ሳላስበው ጭልጥ ያለ እንቅልፍ ይወስደኛል። ዘመቻ ስናስብ ስኬቱ በጣም ስለሚያሳስበኝ ስለመሳካቱ የማረጋገጫ ፎቶ እንደተላከልኝ መሬት ላይ እዘረራለሁ።

በታላቁ ሰልፍ ዋዜማም ከአስተባባሪዎቹ ጋር መረጃ ስንለዋወጥ አድረን ሀገር ቤት ማልዶ ሊነጋጋ ሲል ሕዝቡ ከብዙ አቅጣጫ ወደ ሰልፉ ቦታ እየሄደ እንደሆነ ከሚደርሱኝ ዘገባዎች አረጋገጥኩ። እንደተለመደው ሌሊቱን ሙሉ እምቢ ያለኝ እንቅልፍ መጥቶ በተቀመጥኩበት ወንበር ላይ አጋደመኝ። ትንሽ ሸለብ እንዳደረገኝ ቢሮ ተሰብስበው የነበሩ ሰዎች በደስታ ሲጮሁ ቀሰቀሱኝ። ይህን ሰልፍ ስንጠራ ግብግባችን ከመንግሥት ጋር ብቻ ሳይሆን ሰልፉ እንደማይሳካ ሲያሟርቱብን ከነበሩ የኦሮሞ ግለሰቦች እና ቡድኖችም ጋር ነበር። ቢሮ የተሰበሰቡት ሰዎች በከፍተኛ ጭንቀት እና ጉጉት መንጋቱን ሲጠባበቁ ቆይተው፤ መላው ኦሮሚያ በሰልፈኞች መጥለቅለቁን ሲያዩ በደስታ ራሳቸውን መቆጣጠር አቅቷቸው ነበር የሚጮሁት። ፌስቡክ ገብቼ የሚመጡ መረጃዎችን እየሰበሰብኩ መለጠፍ ጀመርኩ። ፌስቡኬን በሰባት ኮምፒውተሮች ከፍቼ ከሌሎች ስድስት ሰዎች ጋር ሆነን ለመለጠፍ ብንሞክርም፣ እየመጣ ያለው የመረጃ ፍጥነት እና የሚለጠፈው ሊመጣጠን አልቻለም። ኮምፒውተሮቹ እየጋሉ አጥፍተን መልሰን መክፈት ነበረብን።

ከጠዋቱ ሦስት ሰዓት ሲሆን ቢያንስ ከሁለት መቶ ባላነሱ ከተሞች ላይ ሰልፎች መደረጋቸውን በፎቶ እና በቪዲዮ ማስረጃዎች ማረጋገጥ ቻልን። ከፊንፊኔ በስተቀር በብዙ ቦታዎች ሰልፉ በሰላም ተካሄደ። ታላቁ ሰልፍ በታቀደበት ወቅት በፊንፊኔ መካሄድ አለበት ወይስ የለበትም የሚል ክርክር ነበር። አገዛዙ የቁሮን ስም ለማጠልሸት እና አጀንዳ ለማስቀየር የብሔር ግጭት ሊፈጥር ይችላል የሚል ሥጋት ነበረን። የፊንፊኔ አስተባባሪዎች ግን «ኦሮሚያ በሙሉ ወጥቶ እኛ ፊንፊኔዎች አለመውጣታችን ዋና ከተማችንን ያስረከብን ይመስላል» በማለት ለመውጣት ወሰኑ። በዕለቱም በሺዎች ወደ መስቀል አደባባይ ተመሙ። እዚያ ሲደርሱ የፌደራል ፖሊሶች በሰላማዊ ሰልፈኞች ላይ ክፉኛ ድብደባ በመፈጸማቸው ሰልፉ ቢበተንም ወደ ዞኖች መሄድ የተከለከሉ የዓለም አቀፍ ዜና አውታሮች ለሰልፉ ሰፊ ሽፋን መስጠት ችለዋል።

በሌሎች ከተሞች ጠዋት ላይ በአብዛኛው ሰላማዊ ነበር። ሕዝቡ እንደታቀደው ምንም ዓይነት የጦር መሣሪያ ሳይዝ ወጣ። የመንግሥት ፖሊስ እና ወታደሮችም ከተወሰኑ ቦታዎች በስተቀር ኃይል አልተጠቀሙም።

ነገር ግን ሕዝቡ ሰልፉን አጠናቆ ወደ ቤቱ መመለስ ሲጀምር ወታደሮች ተኩስ ከፍተው ተበታትነው ሲሄዱ የነበሩ ብዙ ንጹሀንን ገደሉ። በደረሰን መረጃ መሠረት መንግሥት መጀመሪያ ሰልፉ አይሳካም ብሎ ስላሰበ የኃይል እርምጃ ከመውሰድ ተቆጥቦ ነበር። በኋላ ግን በወጣው ሕዝብ ብዛት እና በመላው ኦሮሚያ መሆኑ ስላስደነገጠው ከፍተኛ የኃይል እርምጃ በመውሰድ መቀጣጫ ለማድረግ ወሰነ። ይህን ውሳኔ በዋናነት ያሳለፈው የደኅንነት መሥሪያ ቤቱ እንደሆነም ለማወቅ ቻልን። በብዙ ቦታዎች ሰዎች የተገደሉት ሕዝቡ አጠገብ በነበሩ ወታደሮች ሳይሆን በየፎቆቹ ውስጥ በተደበቁ አልሞ ተኳሾች ነው።

በዕለቱ ማታ ባጠናቀርነው ዘገባ መሠረት በከተማ እና በገጠር ከ350 በላይ ቦታዎች ሰልፎች እንደተደረጉ አረጋገጥን። በዚያ ዕለት ቢያንስ ሁለት መቶ ሰዎች ተሰውተዋል፤ ምንም

እንኳን ይህ መሥዋዕትነት በጣም ብዙ ቢሆንም ሰልፉን ስንጠራ ካቀድነው የተጎጂዎች ግምት (casualty estimate) ያነሰ ነበር። ሰልፉን በመላው ኦሮሚያ ማካሄድ ከተቻለ፣ ከአገዛዙ የጭካኔ ባሕርይ አንጻር፣ ከአምስት መቶ እስከ አንድ ሺህ ሰዎች መሥዋዕት ሊሆኑ እንደሚችሉ ገምተን ነበር።

ታላቁ ሰልፍ ብዙ ዋጋ ቢያስከፍለንም መሳካቱ ለቀጣዩ የትግል ምዕራፍ ከፍተኛ ጠቀሜታ ነበረው። ትግሉ ከተቃውሞ ወደ ንቅናቄ ደረጃ መሸጋገሩን አሳይቷል። በሌላ አነጋገር ትግሉ በተቆራረጠ እና በተበታተነ መልኩ ጥቂት የኅብረተሰብ ክፍሎች የሚያካሄዱት ተቃውሞ ሳይሆን ሰፊውን የኅብረተሰብ ኃይል ከጎኑ ማሰለፉን ገሃድ አወጣ። የቄሮ ትግል መንግሥት እንደሚለው እና ሌሎች ሰዎች እንደሚጠረጥሩት ጥቂት ወጣቶች በስሜት የሚነዱት ሳይሆን በሳል ስትራቴጂ አውጥተው በሚንቀሳቀሱ አስተባባሪዎች የሚመራ መሆኑን አረጋገጠ። መላውን ኦሮሚያ ማንቀሳቀስ የሚችል መዋቅር እንዳለውም በተጨባጭ አሳየ። በአጠቃላይ ኦገስት 6 ቀን 2016 (ሐምሌ 30/2008 ዓ.ም) የተካሄደው ታላቁ ሰልፍ የቄሮ ትግል በርቶ የሚጠፋ አመጽ ሳይሆን ዘላቂነት ያለውና የተቀናጀ ትግል በመሆኑ፣ የኢትዮጵያን ፖለቲካ ሊለውጥ የሚችል የማይናቅ ጠንካራ ኃይል መሆኑን አስመሰከረ።

## 7.7. ማርሽ መቀየር

በታላቁ ሰልፍ መሰካት ቄሮ አስተማማኝ አቅም እንደገነባና በሰላማዊ የትግል ስልት የበለጠ ድል መቀናጀት እንደምንችል ስላረጋገጠን፣ ተጨማሪ እርምጃዎችን በመውሰድ በመንግሥት ላይ የምናደርገውን ጫና ለመጨመር ወሰንን። ለዚህ ደግሞ ጥያቄያችንን ከፍ ማድረግ እና ጠጠር ያሉ የሰላማዊ ትግል እርምጃዎችን መጠቀም ያስፈልጋል። ከጥያቄ አንጻር አስቀድመን ስናነሳቸው የነበሩትን፣ ለምሳሌ ኦሮሚያ በፊንፊኔ ላይ ያላት ልዩ ጥቅም እና አፋን ኦሮሞ የፌደራል የሥራ ቋንቋ ይሁን የሚሉት የበለጠ ጎልተው እንዲወጡ አደረግን። በተጨማሪም የዴሞክራሲያዊ ሽግግር ብሎም የሥልጣን ጥያቄን ብቅ ማድረግ ጀመርን። ከትግል ስልት አንጻር እስከዚያ ጊዜ ድረስ ስንጠቀም የነበረው ከሦስቱ ዋና ዋና የሰላማዊ ትግል ዓይነቶች ውስጥ አንዱን ብቻ ነበር። አቅማችን እየጠነከረ ሲመጣ የተቀሩትን በሂደት ሥራ ላይ ለማዋል ወሰንን።

ዕውቁ ምሁር ጂን ሻርፕ 198 የሰላማዊ ትግል ዘዴዎችን በመለየት፣ በሚሰጡት ፋይዳ እና በሚጠይቁት መሥዋዕትነት ላይ ተመሥርቶ በሦስት ዋና ዋና ምድቦች ከፍሎ ያስቀምጣቸዋል31። ። እነዚህ ምድቦችም፦

1. መቃወም እና ማግባባት (Protest & Persuasion)፥ የአንድን አገዛዝ ፖሊሲና አሠራር ኢ-ፍትኃዊነት በሰልፍ፣ ፊርማ ማሰባሰብ በመሳሰሉ ዘዴዎች ተቃውሟችንን ለመግለጽና እንዲቀየሩ ለማሳመን የምንወስዳቸው እርምጃዎች ናቸው። በዚህ ምድብ የሚካተቱ ዘዴዎች ጥቅም ኢ-ፍትኃዊ የሆነውን ጉዳይ በማጋለጥና ከሕዝብ ጋር በማስተዋወቅ የንቅናቄውን ቅቡልነት ማሳደግ ነው።

2. አለመተባበር/እምቢተኝነት (Non-Cooperation) ፥ የአገዛዙን ሕጎች እና ትዕዛዞች መጣስ፣ እንዲሁም ዜጎች የሚጠበቅባቸውን ኃላፊነቶች አለመወጣት ናቸው። ለምሳሌ ግብር አለመክፈል፣ የሥራ ማቆም አድማ እዚህ ምድብ ሥር ይካተታሉ። የእምቢተኝነት ዘዴዎች ጥቅም የአገዛዙን የማሥተዳደር አቅም ማዳከም ነው። 3. ማንኛውም መንግሥት ሥራውን ማስፈጸም የሚችለው፣ በተወሰነ ደረጃም ቢሆን ዜጎች ወደውም ሆነ ፈርተው ሲተባበሩት ስለሆነ፣ ያ ትብብር ሲቀንስ የማሥተዳደር አቅሙም ይመናመናል።

3. ማደናቀፍ (Intervention)፥ ለአገዛዙ ጠቃሚ የሆኑ ሥራዎች እንዳይከናወኑ ማወክ ነው። ለምሳሌ መንገድ መዝጋት፣ አገዛዙ የሚጠቀምባቸውን የተመረጡ ንብረቶች ማውደምን ያካትታል። የማደናቀፍ ዘዴዎች ጥቅም በአገዛዙ የዕለት ተዕለት ሥራ ውስጥ በቀጥታ ጣልቃ በመግባት በማሰናከል ማዳከም ነው።

የጂን ሻርፕን ምክር በመከተል እስከ ታላቁ ሰልፍ ቀን ድረስ በአብዛኛው የመቃወም እና

31 Sharp, Gene The Politics of Nonviolent Action. Porter Sargent Publisher, 1973

የማሰመን ዘዴዎችን ስንጠቀም ቆየን። በጥቂት በታዎች ሕዝቡ አልፎ አልፎ የእምቢተኝነት እና የጣልቃ ገብነት ዘዴዎችን ሲጠቀም ያስከፈለው ዋጋ እና ለትግሉ ያስገኘው ጥቅም ተመጣጣኝ ስላልነበር እንዲቆም ተደረገ። የታላቁ ሰልፍ ስኬት የቁሮ ትግል በንቃት እና በአደረጃጀት አስተማማኝ መሆኑን ስላረጋገጠ፤ የእምቢተኝነት እና በሂደትም የጣልቃገብነት ዘዴዎችን ወደ መጠቀም ተሻገርን። በሌላ አገላለጽ መንግሥትን ከመቃወም ወደ አስገድዶ ማስፈጸም ከፍ አልን። በሌላ አነጋገር የገበያ እቀባ፣ የሥራ ማቆም አድማ፣ ግብር አለመክፈል፣ መንገድ መዝጋት የመሳሰሉት ዋነኛ የትግል ዘዴዎች ሆኑ ማለት ነው።

እስከ ታላቁ ሰልፍ ቀን ድረስ የኦሕዴድ መዋቅር በውስጡ ትግሉን የሚደግፉ ሰዎች ቢኖሩትም በቄሮ ጥንካሬ እና በትግሉ ስኬት ላይ ሙሉ እምነት ስላልነበራቸው ተሳትፏቸው ውስን እና ምሥጢራዊ ነበር። በአንድ በኩል፣ ሰልፉ የቄሮ ትግል የኦሮሞን ሕዝብ በመላው ኦሮሚያ በአንድነት አደራጅቶ እያንቀሳቀሰ በመሆኑ እንደማይቀለበስ ሲያሳይ፤ በሌላ በኩል ደግሞ መንግሥት ሕዝቡን አፍኖ ለመግዛት የሚያስችለው አቅም ተመናምኖ ወደ ውድቀት እያመራ መሆኑንም ፍንትው አድርጎ አሳየ።

ይህ ደግሞ የኦሕዴድ አመራር ከሕወሓት ፍርሀት ተላቆ ወደ ትግሉ እንዲቀላቀል አደፋፈረው። በዚህ ድፍረት በመነሳሳት ለሕዝብ የወገነው ቡድን ከሕወሓት የወገነውን ቡድን በመፈንቅለ-ሥልጣን አስወግዶ ሥልጣን ማደላደል ቻለ።

ታላቁ ሰልፍ በስኬት በተጠናቀቀ በአንድ ወር ጊዜ ውስጥ በተካሄደው የኦሕዴድ ሥራ አስፈጻሚ ኮሚቴ ስብሰባ ላይ፣ ያለ ሕወሓት ፈቃድ ሙክታር ከድርን ከሥልጣን በማውረድ ለማ መገርሳን የድርጅቱ ሊቀመንበር አድርገው ሾሙ።

በኦሕዴድ ውስጥ ለሕወሓት ታማኝ የሆነው ቡድን ተገርስሶ ለሕዝቡ ተቆርቋሪነት ያለው ወገን ሥልጣን መያዙ ቀደም ሲል የተነደፈ ስትራቴጂ ውጤት ነው።

ዕውቁ የፖለቲካ ሳይንስ ምሁር ሳሙዔል ሃንቲንግተን ከአምባገነናዊ አገዛዝ ወደ ዴሞክራሲ ለመሸጋገር የሚያስችሉ አራት መንገዶች እንዳሉ ያስቀምጣል[32]።

1. መለወጥ (Transformation)፡ አንድ አምባገነናዊ አገዛዝ በራሱ ተነሳሽነት ሀገሪቷን ወደ ዴሞክራሲያዊ ሥርዓት ለማሸጋገር ሲወስን የሚፈጠር ሲሆን፣ ይህ የሚሆነው አምባገነኑ በራሱ የሐሳብ ለውጥ ካመጣ ወይም አንድ አምባገነን ሞቶ ተተኪው መሪ ወደ ዴሞክራሲ ለማሻገር ሲወስን ነው።
2. መገልበጥ/መናድ (Replacement)፡ ተቃዋሚዎች በትጥቅ ትግል ወይም በሕዝባዊ አመጽ አምባገነናዊ ሥርዓቱን ገልብጠው ሥልጣን በመያዝ ሀገሪቷን ወደ ዴሞክራሲ ካሸጋገሩ።
3. ስምምነታዊ ሽግግር (Transplacement)፡ የተቃዋሚዎች የትግል አቅም ተጠናክሮ አምባገነናዊ ሥርዓቱን በማዳከም ሀገሪቷን ወደ ዴሞክራሲ ለማሻገር ማስገደድ ሲችል የሚፈጠር ነው።
4. የውጪ ጣልቃገብነት (External Intervention)፡ የሌላ ሀገር ኃይል ወይም አህጉራዊ የሀገራት ትብብር ጦሩን ልኮ የአንድን ሀገር አምባገነን ከሥልጣን በማባረር ሀገሪቷ ወደ ዴሞክራሲ እንድትሸጋገር ካስቻለ።

32 Huntington, Samuel P. The Third Wave: Democratization in the Late Twentieth Century University of Oklahoma Press, 1991

የሃንቲንግተንን የሽግግር አማራጮችን በማጥናት፣ ከሀገራችን ነባራዊ ሁኔታ ጋር በማመዛዘን የስምምነት ሽግግር (Transplacement) መሞከር እንደሚሻል ወሰንን። በሰላማዊ ትግል ሥርዓቱን በማሽመድመድ ሙሉ በሙሉ ከመውደቅ እና ወደ ዴሞክራሲ ከመሻገር አንዱን እንዲመርጥ ማስገደድ እንደሚቻል ተማምነን ወደ ሥራ ገባን።

ሆኖም በዚህ ትግል ኢሕአዴግን መጣል ቢቻልም፤ ፓርቲ እና መንግሥት አንድ በሆኑበት እንዲሁም የጦፈ ተገዳዳሪ ብሔርተኝት ባለበት ሥርዓቱን ሙሉ በሙሉ ለመናድ መሞከር የሀገር መበታተን ሊያስከትል ይችላል ብለን ፈራን። ከሀገራችን ነባራዊ ሁኔታ አንጻር የተሻለ የሚሆነው አገዛዙን ሙሉ በሙሉ ከመናድ ይልቅ ከሥርዓቱ ውስጥ ለውጥ ፈላጊ ቡድን ወደ ሥልጣን እንዲመጣ በማስቻል ለዴሞክራሲያዊ ሽግግር በር መክፈት ይሻላል የሚል ድምዳሜ ላይ ደረስን።

ለኦሮሞም ሆነ ለሀገሪቱ አነስተኛ አደጋ (minimal risk) ያለው በአገዛዙ ውስጥ ለዘብተኛ ለውጥ አራማጅ (moderate reformist) ግለሰቦች እና ቡድኖች ሥልጣን ይዘው ሀገር እንዲያሻግሩ ማስቻል ነው። ስለዚህ ከኦሕዴድ ውስጥ ሕዝባዊ ውግንና ያላቸውን ቀስ በቀስ ወደ ትግሉ ጎራ መሳብ እና ማብቃትን በእቅድ ሠራን። ይህ ለውጥ ፈላጊዎችን የማበርታት አካሄድ ሁለት ስልታዊ ጥቅሞች ይኖሩታል ከሚል እሳቤ የመነጨ ነው። አንደኛ፣ የአምባገነን ሥርዓቱን ለውጥ በሚሹ እና ያለው እንዲቀጥል በሚፈልጉት (reformist vs hardliners) መካከል በሁለት ጎራ ከፍሎ ያዳክማል። ሁለተኛው ደግሞ፣ በሥርዓቱ ጉያ ውስጥ የትግል አጋር በማፍራት ኃይላችንን አጠናክሮ ድልን ያፋጥናል በሚል ተስፋ ነበር። በተጨባጭ የሆነውም ይኸው ነው።

አስቀድሞ እንደተገለጸው ለማ መገርሳ የሀገር ውስጥ ትግል መሪ ሆኖ እንዲታይ ከፍተኛ የስብዕና ግንባታ ሥራ ሲሰራ ስለነበር፤ እሱ እና ባልደረቦቹ የኦሕዴድን የአመራር መዋቅር መቆጣጠራቸው ሥርዓቱን ወደለየለት የአደባባይ ክፍፍል እና ግልጽ ፍጥጫ መራው። በተለመደው አሠራር የፓርቲ ሊቀመንበር ሆኖ የተመረጠው ሰው ወዲያው የክልሉ ፕሬዝዳንት ይሆናል። ለማ ግን ፕሬዝዳንትነቱን ሳይረከብ ከሦስት ወር በላይ እንዲቆይ ተደረገ። የተከተልነው ስልት ገዢውን ፓርቲ ለሁለት ከፍሎ ከውስጥ ሽኩቻ ወደ ግልጽ ፍጥጫ ማድረሱ ለቄሮ ድል ማስገኘት ብቻ ሳይሆን ሞራላቸውን በእጅጉ አሳደገው። ሕዝቡ የኢሕአዴግን መከፋፈል እና የእርስ በእርስ ግጭት በአደባባይ ሲመለከት የሥርዓቱ መውደቂያ መቃረቡን በመገመት የበለጠ ተደፋፍሮ ትግሉን አቀጣጠለው።

# 7.8. **የኢሬቻ ፍጅት እና የአምስት ቀናት ቁጣ ዘመቻ**

በሕዝቡ እና በቄሮ በኩል የተከፈለው መሥዋዕትነት ቢያሳዝነንም የታላቁ ሰልፍ ስኬት ከፍተኛ የሞራል ብርታት አስገኘልን። ይህንን የድል ስሜት በመጠቀም እየተቃረበ በነበረው የኢሬቻ በዓል ላይ ከፍተኛ ተቃውሞ ለማሰማት ዝግጅት መደረግ ተጀመረ። የኢሬቻ በዓልን ስምንተኛ እና ዘጠነኛ ክፍል አሰላ ስማር ጀምሮ ስታደም ቆይቻለሁ። ኢሬቻ ፈጣሪን ለማመስገን የሚደረግ ሥነ-ሥርዓት ቢሆንም ከተለያዩ የኦሮሚያ ዞኖች የመጡ ተማሪዎች እና ወጣቶች በመገናኘት ለትግሉ ቅንጅት የሚፈጥሩበት ዕድል ነው።

በተጨማሪም ሁሉም ታዳሚዎች ከየዞኑ በኦሮሞ ባሕላዊ ልብስ አምረው ስሜት የሚቀሰቅሱ ዘፈኖችን እየዘፈኑ መገናኘታቸው ብሔርተኝነትን ለማጠናከር ይጠቅማል። ከሁሉም ዞኖች መሰባሰባቸው እርስ በእርስ ለመተዋወቅ እና የግንኙነት መዋቅር (network) ለመፍጠር መልካም አጋጣሚ ነው። የተሳታፊው ሕዝብ ብዛት ለምሥጢራዊ ሥራዎች እና በድብቅ መከናወን ላለባቸው ነገሮች እንደ ሽፋን ሆኖ ያገለግላል። በተጨማሪም የሕዝቡን ብዛት ተጠቅሞ ተቃውሞ ለማሰማት አመቺ ነው። በእነዚህ ምክንያቶች የኢሬቻ በዓል ለብዙ ዓመታት የትግል መስክ ሆኖ ቆይቷል። መንግሥትም ይህንን ስለተረዳ በየዓመቱ ኢሬቻ ሲቃረብ የተሳታፊውን ሕዝብ ቁጥር ለመቀነስ፣ እንዲሁም የትግል ዓርማዎች እና ባንዲራዎች እንዳይገቡ ለመከልከል ከፍተኛ ጥረት ያደርጋል።

የ2009 ኢሬቻ የኦገስት 6ቱ (ሐምሌ 30) ታላቅ ሰልፍ በተካሄደ በሁለት ወራት ጊዜ ውስጥ ስለሚካሄድ፤ ሁለቱም ወገኖች አስቀድመው ወደ ዝግጅት ገብተዋል። መንግሥት ኢሬቻ ወደ ተቃውሞ ሊቀየር እንደሚችል በመጠርጠር ለመቆጣጠር እና ለማክሸፍ ተዘጋጀ። ቄሮ ደግሞ በዓሉን ወደ ተቃውሞ ሰልፍ በመቀየር ዓለም ሁሉ የሚሰማው ትዕይንት ለማካሄድ ዝግጅቱን ቀጠለ። የበዓሉ ቀን በተቃረበ ቁጥር እሰጣ ገባው እየበረታ መጣ፤ በቄሮ በኩል ሰላማዊ ሰልፍ እንደሚደረግ በይፋ ታወጀ። በመንግሥት ወገን ግን በለማ መመረጥ ይፋ የሆነው ክፍፍል በኢሬቻ ጉዳይም ውስጣዊ መካረርን አስከተለ። በፌደራል ደኅንነት መሥሪያ ቤት በኩል ተቃውሞውን ለመከላከል ማንኛውም እርምጃ መወሰድ አለበት የሚል አቋም ተወሰደ። ሌላው ቡድን ሰላማዊ ተቃውሞ ቢደረግ ጉዳት እንደሌለው በመሞገት፣ የኃይል እርምጃ መውሰድ ግጭቱን የበለጠ እንደሚያባብስ እና መንግሥትን እንደሚጎዳ አቋም ያዘ።

ቄሮ ይህንን በመረዳት የመንግሥትን ክፍፍል የበለጠ ያባባሰ መግለጫ አወጣ። ይህም ተቃውሞው ፍጹም ሰላማዊ እንደሚሆን እና ምንም ዓይነት ብጥብጥ እንደማይኖር ማረጋገጫ እንደሚሰጥ በማስታወቅ፤ ከኦሮሚያ ፖሊስ በስተቀር የፌደራል ኃይል ወደ ቦታው እንዳይገባ አስጠነቀቀ። ይህ የተደረገው በሦስት ምክንያቶች ነበር። አንደኛ፣ በመንግሥት ውስጥ ለዘብተኛ አቋም የያዘውን አንጃ በማበርታት ክፍፍሉን ለማባባስ። ሁለተኛ፣ የኦሮሚያ ፖሊስ ወደ ትግሉ እየተሳበ በመሆኑ ሕዝቡን አይነካም በሚል ተስፋ። ሦስተኛ፣ የኦሮሚያ ፖሊስን በማስጠጋት እና የፌደራል ጸጥታ ኃይሎችን በመግፋት በሥርዓቱ የጸጥታ ኃይሎች ውስጥ ያለውን ክፍፍል

የበለጠ ለማስፋት ነው።

በስተመጨረሻ ለዘብተኛው ቡድን የበላይነት አግኝቶ የፌደራል ኃይል እንዳይገባ ከስምምነት ተደረሰ፤ ይህም ውሳኔ በአባ ገዳ በየነ ሰንበቶ በኩል ተገለጸልን። አባ ገዳ በየነ የገዳ ሥርዓት እንዲያንሰራራ ለማድረግ ከነበራቸው ድርሻ በተጨማሪ በቄሮ ትግል ውስጥ ትልቅ ሚና የተጫወቱ ሰው ናቸው። በ2014 የOSA ዓመታዊ ስብሰባ ላይ ተጋብዘው አሜሪካ በመጡበት ወቅት ብዙ ነገሮችን ተወያይተን ጥሩ መግባባት ላይ ደርሰናል፤ ሀገር ቤት ከገቡ በኋላም እየደወሉ በትግሉ ዙሪያ ይመክሩኝ ነበር። የቄሮን ትግል ፍትኃዊነት ያለፍራቻ በግልጽ ስለሚናገሩ በቄሮዎች ዘንድ ታላቅ ታማኝነትን አፍርተዋል። የኢሬቻ ቀንም በእኛ እና በመንግሥት ባለሥልጣናት መካከል መግባባት እንዲፈጠር ከጅምሩ አንስቶ ከፍተኛ ጥረት አድርገዋል።

መንግሥት በኢሬቻ ላይ ሊነሳ የሚችለውን ተቃውሞ በኃይል ማዳፈን አስቸጋሪ እንደሚሆን በመረዳቱ በሌላ ስልት ለማሸነፍ አቀደ። ይህም ወደ ሠላሳ ሺህ የሚቆጠሩ የኦሕዴድ አባላትን ከየዞኖቹ መልምሎ ወደ ቢሾፍቱ በማምጣት፤ በሌሊት ኢሬቻ የሚከበርበት ቦታ አስገብቶ መድረኩን በመቆጣጠር የድጋፍ ድምፅ አጉልቶ ተቃውሞውን ለመዋጥ አሰበ። ይህ የመንግሥት እቅድ ለቄሮ ቀድሞ ደርሶ ስለነበር፤ ቀደም ብለው ከሌሊቱ ዘጠኝ ሰዓት ላይ የኦሕዴድ አባላትን በመምሰል የጥበቃ በታዎችን አልፈው መድረኩን ሞሉት። መንግሥት ያዘጋጃቸው ሰዎች ወደ መድረኩ ሲደርሱ ቦታው በቄሮዎች ተጥለቅልቋል። እነርሱም የሚያደርጉትን ሲያጡ የለበሱትን መንግሥትን የሚያወድስ ሹራብ አውልቀው ከሕዝቡ ጋር ተቀላቀሉ። በነጋታው ሕዝቡ በየአቅጣጫው ተቃውሞ እያሰማ ወደ ሆራ አርሰዲ ሲከንፍ የመንግሥት እቅድ መክሸፉና የቄሮዎች እቅድ ማሸነፉ እውን መሆን ጀመረ። ይህም የመንግሥት አካላትን አስቆጣ። “ኢሬቻ ላይ የታጠቀ ኃይል አይገኝም” የሚለውን ስምምነት በማፍረስ ቀድሞውኑ ወታደሮችን በዝግ መኪናዎች ደብቀው አስገቡ። ይህን ተግባር ደርሰንበት ስናጋልጥ፤ አባ ገዳ በየነ ሰንበቶ ድርጊቱን በመቃወም ወታደሮቹ እስካልወጡ ድረስ ሐይቁ ቦታ ሄደው አልመርቅም አሉ። የተለያዩ ባለሥልጣናት በየተራ ለማሳመን ቢሞክሩም አልተሳካላቸውም። ሥነ-ሥርዓቱ ሊነጋጋ አካባቢ መካሄድ የነበረበት ቢሆንም፤ አባገዳዎች እና ባለሥልጣናት ሲከራከሩ ፀሐይ ወጣች። ቄሮዎቹ አባ ገዳዎች መጥተው እንዲባርኩላቸው ይጠብቃሉ፤ አባ ገዳዎቹ ወታደሮቹ ካልወጡ በቀር ለመሄድ ፈቃደኛ አልሆኑም። በዚህ መሀል መንግሥትን የሚያወግዙ መፈክሮች ጎልተው መሰማት ጀመሩ። ይህንን ለመቅረፍ የመንግሥት ባለሥልጣናትን እንደ አባ ገዳ አስለብሰው መድረክ ላይ በማውጣት ቄሮን አታለው ለመበተን ላኳቸው። ቄሮዎቹ ወዲያውኑ ነቅተውባቸው ባለሥልጣኖቹን ከመድረክ አባረሯቸው።

በዚህ የመንግሥት ድርጊት በመናደድም ወደ መድረክ በመውጣት የትግሉ ዓርማ ሆኖ የነበረውን እጅ የማጣመር ምልክት አሳዩ። በመሀል ገመዳ ዋሪዮ የተባለ ቄሮ ማይክራፎኑን ከመድረክ መሪው ተቀብሎ «Down Down Wayyane!!» ብሎ መፈክር አሰማ። በዚህ ጊዜ ሕዝቡ በታላቅ ድምፅ ተቃውሞውን አቀለጠው። ሕዝቡ በከፍተኛ ድምፅ እየተቃወመ ቢሆንም ምንም ዓይነት ብጥብጥ አልተፈጠረም፤ ፖሊሶች ከቄሮዎች አጠገብ ቢቆሙም ምንም ግጭት አልነበረም። ከጥቂት ጊዜ በኋላ ግን በሽፍን ተሽከርካሪዎች ውስጥ የነበሩ የታጠቁ ወታደሮች ከተደበቁበት የመድረክ ጀርባ በመውጣት ሕዝቡ ላይ አስለቃሽ ጭስ ተኮሱ። መጀመሪያ ከላይ እየዞረ የእንኳን አደረሳችሁ ወረቀት ሲበትን የነበረው ሂሊኮፕተርም አስለቃሽ ጭስ መርጨት

ጀመረ። የተኩስ ድምፅ፣ አስለቃሽ ጭስ እና ጩኸት ተቀላቅለው ከባድ ድንጋጤ እና ሁካታ ተፈጠረ። ወታደሮቹ በጭስ ታፍኖ በሚተራመሰው ሕዝብ ላይ ተኩስ ከፍተው ወደ መግደሉ ገቡ፤ እግሬ አውጪኝ ብሎ የሚሮጠው ሕዝብ ከጀርባው ወዳለው ገደል ወደቀ። ከተፈጠረው መረጋገጥ ጋር በተተኮሰባቸው ጥይት ከሰባት መቶ በላይ ሰላማዊ ዜጎች ከአሥራ አምስት ደቂቃ ባነሰ ጊዜ ውስጥ ሞቱ።

የኢሬቻውን ኹነት ከዋዜማው ጀምሬ ያለ እንቅልፍ እየተከታተልኩ ስለነበር፤ ብዙ ቄሮዎች እየተካሄደ ስላለው ሁኔታ እየተፈራረቁ በቀጥታ (live) ያሳዩኛል። አንድ ቄሮ እንዲሁ በቀጥታ እያሳየኝ እያለ ጥቃቱ ሲጀምር ስርጭቱ በድንገት ስለተቋረጠ ለአጭር ጊዜ ምን እየሆነ እንዳለ ማወቅ አልቻልኩም። መንግሥት ኢንተርኔት ስለዘጋ የተፈጠረውን ነገር ለጊዜው ማወቅ አስቸጋሪ ሆነ። የሳተላይት ኢንተርኔት ያላቸውን የውጪ ሚዲያ ጋዜጠኞች ሳነጋግር ገና መስማታቸው እንደሆነና ከጥቃቱ ሠላሳ ደቂቃ ቀደም ብሎ ቦታውን ለቀው እንዲወጡ መደረጉን ነገሩኝ። ለውጪ ሚዲያ ከሚሰሩ ጋዜጠኞች መካከል አንድ ኦሮሞ ልጅ ብቻ ከፖሊሶች አምልጦ ወደኋላ ቀርቶ ስለነበር፤ በያዘው ሳተላይት ኢንተርኔት ደውሎ የተከሰተውን ነገረኝ። ወታደሮች ከተደበቁበት ሽፍን መኪና ወጥተው ወደ ሕዝቡ ሲተኩሱ የሚያሳይ ቪዲዮ ቀርጾ ነበርና ላከልኝ። የመንግሥትን ወንጀል በተጨባጭ ማስረጃ ለሕዝብ እና ለዓለም አቀፍ ሚዲያ አጋለጥን።

ኢሬቻ ላይ የተፈጸመው ድርጊት በጣም አናደደኝ! አሳዘነኝም፤ ግን ለማልቀስም ሆነ ለማዘን ጊዜ አልነበረም። እነዚያ ሰማዕታት የከፈሉት መሥዋዕትነት ፍሬ እንዲያፈራ ሥራ ላይ ማተኮር አስፈላጊ ነበር። የሰላማዊ የትግል ስልቶች የመንግሥት ኃይል በሚወስደው እርምጃ ጉዳት ሲያደርስ ድርጊቱ መልሶ መንግሥትን እንዲጎዳ (backfire) ማድረግ እንደሚቻል ይጠቁማሉ። ድርጊቱን በማጋለጥ ከሚደርሰው የዲፕሎማሲ እና የፕሮፓጋንዳ ኪሳራ በተጨማሪ ጥቃቱ ሕዝቡ ውስጥ የሚፈጥረውን የቁጣ ስሜት ወደ ሌላ እርምጃ መቀየር ያስፈልጋል። ኹነቱ በተፈጸመ በሰዓታት ውስጥ ከሀገር ቤት የቄሮ አስተባባሪዎች እና ከውጪ አንቂዎች ጋር መወሰድ ባለበት እርምጃ ላይ ሐሳብ ተለዋወጥን።

ከውጭ ሀገር አንቂዎች መካከል አንዳንዶቹ እርምጃ መውሰድ ሕዝቡን ለባሰ ፍጅት ያጋልጣል በማለት ሲቃወሙ፣ አንዳንዶቹ ስለስኬቱ ጥርጣሬ ገባቸው። የሀገር ውስጥ አስተባባሪዎች ግን የሕዝቡን ቁጣ ወደ ቅጣት መቀየር ይኖርብናል አሉ። «በአጭር ጊዜ ውስጥ የተሳካ እርምጃ መውሰድ እንችላለን ወይ?» ስላቸው እንደሚቻል አስረግጠው አረጋገጡልኝ። ለኢሬቻ እየተዘጋጀን ሳለ መንግሥት ቃሉን አጥፎ የኃይል እርምጃ ከወሰደ መልሳችን ምን መሆን እንዳለበት ተወያይተን ያስቀመጥናቸው እቅዶች ነበሩ። እቅዶቹን ደግመን ከዳሰስናቸው በኋላ ምን ዓይነት እርምጃዎች መወሰድ እንዳለባቸው ወሰንን። የሚወሰደው እርምጃ መንግሥትን የሚያሳምም ብቻ ሳይሆን ትግሉን ወደ ላቀ ደረጃ የሚያሸጋግር መሆን እንዳለበትም ተስማማን።

የኢሬቻው እልቂት በሕዝቡ ውስጥ ትልቅ ቁጣ በማስከተሉ የጣልቃ መግባት (intervention) እርምጃ ለመውሰድ ወስነን፤ ዕልቂቱ በተፈጸመበት ዕለት "አምስት የቁጣ ቀናት (Five Days of Rage)" በሚል ስያሜ ዘመቻ ታወጀ።

ከጣልቃ ገብነት ስልት መካከል በአጭር ጊዜ ውስጥ ውጤት ማምጣት የሚችለው ተመረጠ።

አገዛዙን ለማዳከም ካስቀመጥነው ስልት ውስጥ አንዱ ኢኮኖሚውን ማዳከም ስለሆነ፤ ኢንቨስተሮች በመንግሥት ላይ ያላቸውን አመኔታ ለመሸርሸር የሚያስችሉ እርምጃዎችን መረጥን። ይህም ከመንግሥት ጋር ተጣብቀው በሕዝብ ላይ ጉዳት የሚያደርሱ ባለሀብቶችን ንብረት ማውደም ነበር። በዚህም መሠረት ሕዝቡ የመንግሥት እና ከመንግሥት ጋር ቁርኝት ያላቸውን ነጋዴዎች ንብረት ማውደም ላይ ዘመተ። ኢሬቻን ለመታደም አጊጠው የወጡ ወጣቶች ሬሳቸው ወደየቀዬኣቸው ሲመለስ በማየቱ የበገነው ሕዝብ፣ የቀብር ሥነ-ሥርዓቱን ወደ ከፍተኛ ተቃውሞ ቀየረው። ከቀብር በኋላም እንደወትሮው ወደ ሚች ቤት ከመመለስ ይልቅ ወደ ቀጥተኛ እርምጃ ገባ። ጥቃት ሊደርስባቸው የሚገባቸውን ተቋማት ቄሮ አስቀድሞ ስለለያቸው፤ የሕዝብን መሬት ያለ ካሳ የወሰዱ፣ ውኃ እና አፈር የሚበክል መርዛማ ቆሻሻ የሚለቁ እና የመሳሰሉት ዒላማ ሆኑ። እንዲሁም አገዛዙ ሕዝብን ለመጉዳት በሚጠቀምባቸው ንብረቶች ላይ ትኩረት ተደርገ። እንደ ጤና እና ትምህርት ያሉ የሕዝብ መገልገያ ተቋማት እንዳይነኩ እና ጥበቃ እንዲደረግ መመሪያ ተላለፈ። ተቋማቱ ሲወድሙ በባለቤቶቹም ሆነ በሠራተኞች ላይ አካላዊ ጉዳት እንዳይደርስ ጥንቃቄ እንደሚደረግ አስተባባሪዎቹ አሳወቁ። የንብረት ማውድም መመሪያውን በቀጥታ በፌስቡክ ገጼ ላይ ስለጥፍ ብዙ የሕግ ባለሞያዎች ድርጊቱ በሕግ ያስጠይቃል በሚል ሥጋት ተደናግጠው ይመክሩኝ ነበር። ይህን በመፍራት ለአምስት ቀን በዘለቀው የቁጣ ዘመቻ ወቅት ውጭ ሀገር የሚኖሩ ብዙ አንቂዎች ለመሳተፍ ፈቃደኛ አልነበሩም። እኔ ግን ሊመጣብኝ የሚችለውን ማንኛውንም አደጋ ለመጋፈጥ ዝግጁ ነበርኩ። ምክንያቱም መንግሥት የወሰደውን አሠቃቂ እርምጃ ውድቀቱን በሚያፋጥን ጠበቅ ያለ ቅጣት ምላሽ ካልሰጠን የሕዝቡ ሞራል ተሰብሮ ከትግል ሊያፈገፍግ ይችላል።

የአሜሪካ መንግሥት ባለሥልጣናትም ሊያስፈራሩኝ ሞከሩ፤ ንብረት ማውደም የሰላማዊ ትግል አካል ነው ወይስ አይደለም በሚለው ላይ ብዙ ተከራከርን። በሰው አካል እና በሕይወት ላይ ጉዳት እስካልደረሰ ድረስ ንብረት ማውደም ተቀባይነት ያለው የሰላማዊ ትግል ስልት እንደሆነ በጉዳዩ ላይ የተጻፉ መጻሕፍትን ዋቢ አድርጌ ስለተከራከርኩ በማስጠንቀቂያ እና በተግሳጽ አለፉኝ። የአሜሪካ ሕግ አስከባሪ አካላት እንዳነጋገሩኝ ሲሰማ በፊት በሰው የሚጨናነቀው የOMN ቢሮ ባዶውን ቀረ። ሰዎችን አስበርግጎ እንዲሸሹ ያደረጋቸው "ሚዲያው ከዛሬ ነገ ይዘጋል፤ ጀዋርም ይታሰራል" የሚለው ሹክሹክታ ነበር።

አምስቱ የቁጣ ቀናት ዘመቻ ገና ከጅምሩ ካሰብነው በላይ ተሳካ። መንግሥት በወታደር ኃይል የሕዝቡን እርምጃ ማስቆም ስላልቻለ፣ የአገዛዙን እና የአጋፋሪዎቹን ንብረት የማውደም ዘመቻ በመጀመሪያዎቹ ሦስት ቀናት ያለ ምንም ከልካይ ሲካሄድ ነበር ማለት ይቻላል። ዘመቻው በድንገት ስለታወጀ፣ አገዛዙ የቄሮን የተቀናጀ ዘመቻ አስቀድሞ ባለመገመቱ ለመመከት በቂ ዝግጅት አላደረገም ነበር። በመላው ኦሮሚያ በተመሳሳይ ጊዜ በሚሊዮን የሚቆጠሩ ሰዎች እርምጃ እየወሰዱ ስለነበር ለመንግሥት የጸጥታ ኃይል ከአቅሙ በላይ ሆነበት። የአገዛዙን ዝግጅት አለማድረግ እንደ ዕድል በመጠቀም በመላው ኦሮሚያ አከርካሪውን የሰበረ እርምጃ ተወሰደ።

መንግሥት በቂ ወታደር ከኦሮሚያ ውጪ አምጥቶ ኮማንድ ፖስት (Command post) ሲያውጅ፤ ቄሮ ያቀደውን አገባዶ ዘመቻው ማብቃቱን አውጀን አስቆምነው። በዚያ ዘመቻ የጣልቃ ገብነት የትግል ዘዴን ለመጀመሪያ ጊዜ እንደመጠቀማችን መሥዋዕትነቱ ከፍ ያለ ቢሆንም ከገመትነው በታች ነበር። የጸጥታ ኃይሉ ቅድመ-ዝግጅት ስላልነበረውና በቁጥርም አናሳ ስለነበር በብዙ ቦታዎች ሕዝቡ እርምጃ ከወሰደ በኋላ በፍጥነት በመበታተኑ በወታደሮቹ

የሚደርሰው ጉዳት ሊቀንስ ተችሏል። ይሁን እንጂ በተወሰኑ ቦታዎች ላይ አላስፈላጊ ዋጋ ተከፍሏል። ለምሳሌ እንደ ምሥራቅ አርሲ እና ምሥራቅ ሸዋ ባሉ አንዳንድ ወረዳዎች በቅንጅት ማነስ እና በስሜታዊነት ከወታደሩ ጋር በመጋፈጥ ከፍተኛ ጉዳት ደርሷል።

በውጪ ያለን አንቂዎች በቁጣ ዘመቻ ወቅት እና ከዚያ በኋላም በመገናኛ ብዙኃን በኩል የመንግሥትን ትርክት (narratives) ለማክሸፍ ያደረግነው ርብርብ ተሳክቶልናል። በተለይ ንብረት ማውደም፣ መንገድ መዝጋት እና የመንግሥትን መዋቅር ማፍረስ ከተለመደው የሰላማዊ ትግል እርምጃ ወጣ ያሉ ስለነበሩ፤ መንግሥት ቄሮን በሽብርተኝነት ለመፈረጅ ሞክሯል። በበኩላችን እየተወሰደ ያለው እርምጃ የኢሬቻን ዕልቂት ተከትሎ የመጣ ቁጣ መሆኑን በመግለጽ፤ እየወደመ ያለው ንብረት አገዛዙ እና ግብራበሮቹ ሕዝብን ለመጨቆን የሚጠቀሙበት እንጂ የኅብረተሰቡ መገልገያ እንዳልሆነ አብራራን። ለምሳሌ ጥቃት የደረሰባቸው ፋብሪካዎች ያለካሳ ከሕዝብ በተዘረፈ መሬት ላይ የተቋቋሙ እንደሆኑና አጠገቡ ያለ ክሊኒክ እንዳልተነካ በፎቶግራፍ ማስረጃ እናስደግፋለን። በተጨማሪም ጥቃት የሚደርስባቸው የግል ንብረቶች ከመንግሥት ጋር በመሆን ሕዝብን የሚጎዱት ብቻ መሆናቸውን ገልጸን፤ ሁለት ፋብሪካዎች ጎን ለጎን በማድረግ አንዱ ተቃጥሎ ሌላኛው ሳይነካ የሚታይበትን በማስረጃ እናቀርባለን።

ይህንን ሐቅ በወቅቱ ኦሮሚያ ውስጥ በኢንቨስትመንት ሥራ ላይ ተሰማረተው የነበሩ ነጮችም መሰከሩ። አንድ አውሮፓዊ ፋብሪካውን ሊያቃጥሉ የመጡ ሰዎች የራሱን መኪና እንዲያወጣ በመፍቀድ ጥበቃ አድርገው እንደሸኙትና ሕይወቱን ለአደጋ እንዳላጋለጡ እማኝነቱን ሰጠ። መቀመጫቸውን ፊንፊኔ ያደረጉ የውጭ ሀገር ጋዜጠኞችም በቄሮ እገዛ ከከተማ ሾልከው በመውጣት በኦሮሚያ ዞኖች ውስጥ እየተፈጸመ ያለውን በተጨባጭ በዓይናቸው በማየት፤ መንግሥት ሊለጥፍብን የሞከረው የሽብርተኝነት ክስ የሐሰት ወሬ መሆኑን ለዓለም ሕዝብ አጋለጡ። በአጠቃላይ በኢሬቻ ቀን ከተፈጸመው ዘግናኝ ድርጊት አንስቶ በሚዲያ ዘመቻ መንግሥትን አስከነዳን። ለአምስት ቀናት በዘለቀው የቁጣ ዘመቻ መረጃን በፍጥነት እና በተጨባጭ ማስረጃ አስደግፈን በማቅረባችን በሚዲያም ሆነ መሬት ላይ ቄሮ የበላይነቱን ወስዷል።

## 7.9 ኮማንድ ፖስት ያላዳነው ውድቀት

የአምስቱ ቀናት ዘመቻ በስኬት ከተጠናቀቀ በኋላ መንግሥት በአስቸኳይ ጊዜ አዋጅ ኮማንድ ፖስት አቋቁሞ መጠነ-ሰፊ ጥቃት ሊፈጽም እንደሆነ ስለደረስንበት አስተባባሪዎቹ ኅቡዕ (underground) እንዲገቡ ተደረገ። ይህም ብዙዎቹ ወደ ትላልቅ ከተሞች ሸሽተው እንዲደበቁ ማድረግ ነበር። መንግሥት ኦሮሚያን ኮማንድ ፖስት ሥር አስገብቶ የጅምላ እሥራት ጀመረ። እስሩ ደግሞ እንደቀድሞ ፖሊስ ጣቢያ ሳይሆን በሺዎች የሚቆጠሩ ሰዎች ወደ ወታደራዊ ማሰልጠኛ ካምፖች ሊወሰዱ መታቀዱን መረጃ ስለደረሰን፤ ይህን የመንግሥት እርምጃ ወደ መልካም ዕድል ለመቀየር የሚያስችል ሐሳብ ቀረበ። እስከዚያ ጊዜ ድረስ ከተወሰኑ አስተባባሪዎች በስተቀር ቄሮዎች ትግሉን ሲያቀናጁ የነበሩት በአካል ሳይተዋወቁ በማኅበራዊ ሚዲያ ትስስር ብቻ ነበር።

መንግሥት ቄሮዎችን ከሁሉም ዞኖች አፍሶ ወደ ወታደራዊ ማሰልጠኛ ካምፖች ሲልካቸው አጋጣሚውን ተጠቅመው እርስ በእርስ እንዲተዋወቁና ለቀጣዩ ምዕራፍ የሚጠቅም ትስስር መፍጠር የሚያስችል ስልት ለማውጣት ታሰበ። ይህንን ሐሳብ በማመንጨት ረገድ ትልቁን ሚና የተጫወተው ገላና ኢማና (በፌስቡክ ስሙ Naannoo Amboo) የሚባል ቄሮ ነበር። ኢማና የምዕራብ ሸዋ ቄሮ ዋና አስተባባሪና ከመላው ኦሮሚያ አስተባባሪዎች መካከል አንዱ ነው። መንግሥት ቄሮን በወታደራዊ ካምፕ ለማጎር ማቀዱ እንደታወቀ፣ ኢማና ይህን እርምጃ ወደ ዕድል ለመቀየር የሚያስችል ሐሳብ ከትግበራ እቅድ (action plan) ጋር ላከልኝ። ከሌሎች አስተባባሪዎች ጋር ከተወያየን በኋላ እቅዱን አዳብረን ተግባራዊ ለማድረግ ወሰንን። ገላና በምዕራብ ሸዋ አካባቢ ብቻ ሳይሆን በመላው ኦሮሚያ በመንቀሳቀስ ቄሮዎችን በማሰልጠን እና በማስተባበር ከፍተኛ ሚና የነበረው ቆራጥ ታጋይ እና በሳል ምሁር ነበር። ገላና ኢማና የኢሕአዴግ አገዛዝ እሱን ለመግደል ሲያደርግ ከነበረው ብዙ ሙከራዎች ተርፎ ለውጡ እንደ እሱ ባሉ ቄሮዎች መሪነት በመጣ ማግስት ለሥልጣን በበቁ ሰዎች ኅዳር 2013 ዓ.ም በአሰቃቂ ሁኔታ ተረሸነ።

መንግሥት ኮማንድ ፖስት እንዳወጀ በቄሮ በኩል ለጊዜው የትግል እርምጃዎችን ከመውሰድ ለመቆጠብ ተወሰነ። ለዚህ ብዙ ምክንያቶች ነበሩ። የመጀመሪያው መንግሥት በአልሞት ባይ ተጋዳይነት ትልቅ ኃይል አሰማርቶ ሕዝብን ለመጨፍጨፍ ስላቀደ ይህንን ኃይል መጋፈጥ ከጥቅሙ ኪሳራው ይበልጣል። ሁለተኛው፣ እስከዚያ ጊዜ ድረስ ቄሮ ለውስጥ ግንኙነትም ሆነ ለፕሮፓጋንዳ ሥራ ኢንተርኔት ላይ ጥገኛ ሆኗል። ከቁጣ ዘመቻው በኋላ ኢንተርኔት በመቋረጡ ሌላ ዘዴ እስክናዘጋጅ ድረስ ተቃውሞውን ማቋረጥ አስፈላጊ ሆኖ ተገኘ። ሦስተኛው፣ ከኅዳር 2008 ዓ.ም ጀምሮ ሕዝቡ ያለ በቂ ዕረፍት ለአንድ ዓመት ያህል ትግል ላይ ስለቆየ፤ በተፈጠረው አጋጣሚ ዕረፍት ወስዶ ለቀጣዩ ዙር ትግል በሙሉ ኃይል እንዲዘጋጅ ነው። አራተኛው፣ በአንድ ዓመት ጊዜ ውስጥ በቄሮ እንቅስቃሴ ውስጥ የታዩ ጠንካራ እና ደካማ ጎኖችን በመተንተን እና በመገምገም ለቀጣዩ ዙር ክፍተቶችን ለመሙላትና ጠንካራ ጎኖችን ይበልጥ ለማጠናከር በተረጋጋ መንፈስ ማሰብ እና ማቀድ አስፈላጊ ሆኖ በመገኘቱ ነው።

በዚሁ መሠረት ለአሥር ወራት በቆየው የአስቸኳይ ጊዜ አዋጅኅቡዕ ለገቡትም ሆነ ወደ ወታደራዊ

ካምፖች ለተጋዙት ቄሮዎች የአቅም ግንባታ (capacity building) ተሰጣቸው። ኢማና ባቀደው መሠረት ወደ አዋሽ፣ ጦላይ እና ሌሎች ወታደራዊ ካምፖች የተወሰዱ ቄሮዎች ከሦስት እስከ ስድስት ወራት ቆይታቸው ጊዜውን በአግባቡ በመጠቀም በጥልቀት ተወያይተው፣ ልምድ ተለዋውጠው፣ ሰፊ ትስስር ፈጥረው እና ለቀጣይ እርምጃ ተዘጋጅተው ወጡ። ያልታሰሩ አስተባባሪዎች ተወያይተው ያወጡት ቀጣይ የትግል ምዕራፍ እቅድ ስለደረሳቸው ተወያይተውበት በሐሳብ አዳበሩት። የኢንተርኔት እገዳውን ለማሸነፍም ወደ ፊንፊኔ እንዲገቡ ተደረገ። ፊንፊኔ ኢንተርኔት ስለነበር ከሁሉም ዞኖች የተውጣጡ አስተባባሪዎች ወደ መዲናዋ መጥተው በመመሸግ፣ የሚተላለፈውን መረጃ እና መመሪያ ወስደው በአጭር መልዕክት (SMS)፣ እሱም ካስቸገረ ወደ ዞን እና ወረዳዎች በአካል ሄደው ያስተላልፋሉ። በዚህ ሁኔታ የአደረጃጀት እና የአቅም ግንባታ ሥራ ተጠናክሮ ለቀጣዩ ዙር በዝግጅት ላይ እያለን፤መጀመሪያ ለስድስት ወራት ታውጆ ከዚያም ለአራት ወራት የተራዘመው የአስቸኳይ ጊዜ አዋጅ ተነሳ።

አዋጁ ይነሳ ወይስ ይራዘም በሚለው ውሳኔ ላይ ለመድረስ በከፍተኛ የመንግሥት የአሥተዳደር እና የጸጥታ ባለሥልጣናት መካከል ጠንካራ ውይይት ተደረጓል። ከታችኛው የመንግሥት መዋቅር ባገኙት መረጃ ላይ በመመሥረት የቄሮ መዋቅር ሙሉ በሙሉ እንደተመታና ከአንግዲህ የተደራጀ አመጽ ሊያሥነሳ የማይችልበት ደረጃ ላይ መድረሱን ደመደሙ። ቄሮ ከአምስቱ የቁጣ ቀናት ዘመቻ በኋላ ለማድፈጥ መወሰኑ መንግሥት እዚህ ድምዳሜ ላይ እንዲደርስ አድርጎታል። ውጪ ያለነውም እንዲሰልሉን ለተመደቡ ሰዎች ሆን ብለን የተሳሳተ መረጃ በማስተላለፍ መንግሥት ከታችኛው መዋቅር ያገኘው መረጃ ትክክል እንደሆነ አረጋገጥን። አልፎም ከቄሮ አስተባባሪዎች መሀል ሾልኮ የወጣ (leaked) ሰነድ በማስመሰል ላክንላቸው። ይህ ሰነድ ቄሮ ባደረገው የውስጥ ግምገማ ከፍተኛ ጉዳት እንደደረሰበት እና ሕዝቡን እንደ ከዚህ ቀደሙ ማንቀሳቀስ አዳጋች እንደሆነ ይጠቁማል። በተጨማሪም የለማ ቡድን ወደ ሥልጣን መምጣቱና የኦሮሞን ብሔርተኝነት ማቀንቀን መጀመሩ የሕዝቡን ልብ በመሳብ ከትግል እንዲሸፍት አድርጎታል የሚል ይዘት ነበረው።

አገዛዙ ውስጥ ያሉ ቡድኖች የኦሮሞ ብሔርተኝነትን በማቀንቀን የቄሮን ትግል መጥለፍ (hijack) ይቻላል የሚል ተስፋ አደረባቸው። ሕዝቡ መስማት የሚፈልገውን ነገሮች በመናገር፣ የሀገር ውስጥና የውጭ ተቃዋሚዎችን እና አንቂዎችን ተሰሚነት በመቀነስ፣ ከጥቅም ውጪ ማድረግ ይቻላል ብለው ደመደሙ።

በዚህ ሁኔታ ቄሮ ከዚህ በኋላ ሥጋት አይሆንም በሚል እሳቤ የአስቸኳይ ጊዜ አዋጁ ሐምሌ ወር 2009 ዓ.ም ተነሳ፤ የኢንተርኔት ግንኙነትም ተለቀቀ። ሆኖም በቄሮ በኩል በፍጥነት ወደ እንቅስቃሴ ከመግባት ይልቅ በዝግታ መሄዱ ተመራጭ ሆነ። ምክንያቱም ለስድስት ወራት ዕረፍት ላይ የቆየውን ሕዝብ ቀስ በቀስ በማሟሟቅ ወደ ትግል መንፈስ እንዲመለስ ማድረግ ስለሚያስፈልግ ነበር። መንግሥትን በአንዴ አስበርግጎ ወደ ከባድ የኃይል እርምጃ ከመመለስ ቀስ በቀስ መሄዱ የተሻለ ነው ብለን አሰብን።

በዚሁ መሠረት ቀለል ያሉ ጥያቄዎችን በማንሳት ጀመርን፤ ከእነዚህ ጥያቄዎች ውስጥ አንዱ የግብር ጉዳይ ነበር። ይህንን አጀንዳ የመረጥነው በሁለት ምክንያቶች ነው። በአንድ በኩል ከአንድ ዓመት በላይ በዘለቀው የኦሮሚያው ተቃውሞ የንግድ ሥራ ስለተቀዛቀዘ፤ ነጋዴዎች በሁከቱ ምክንያት ያጡትን ገቢ ለማካካስ ግብር ባይከፍሉ ምኞታቸው ነበር።

በሌላ በኩል መንግሥት በሁከቱ ምክንያት የጎደለበትን ገቢ ለማግኘት ግብር መጨመር ግድ

ሆነበት። ይህ የነጋዴ እና የመንግሥት የጥቅም ቅራኔ ተቃውሞ ለመቀስቀስ ጥሩ አጋጣሚ ከመሆን አልፎ ለትግሉ ሌሎች ጥቅሞችም ነበሩት። በመጀመሪያ ደረጃ እስከዚያ ጊዜ ድረስ ነጋዴዎች በቀጥታ ትግሉ ውስጥ ስላልገቡ በቀጥታ የሚነካቸውን ጉዳይ ማግኘታችን እንድናሳትፋቸው ዕድል ሰጠን። ሁለተኛው የግብር አጀንዳ የነጋዴዎችን ተቃውሞ በማነሳሳት የትብብር መንፈግ (non-cooperation) ስልትን ጠንካራ በሆነ መልኩ ተግባራዊ እንድናደርግ ሌላ ዕድል ሆኖ ታየን።

በጉዳዩ ላይ በማኅበራዊ ሚዲያ ዘመቻ እንደጀመርን፣ መንግሥት ጉዳዩን ለማርገብ ከነጋዴዎቹ ጋር ስብሰባ ጠራ፤ እኛም እነዚህን ስብሰባዎች ወደ ዕድል ቀየርናቸው። ጠንካራ ነጋዴዎችን በመጠቀም የተጨመረው ግብር እንዲቀነስ ከመጠየቅ ባለፈ ለዚያ ዓመት ሙሉ በሙሉ እንዲሠረዝ እንዲጠይቁ አበረታታናቸው። ይህ ጥያቄ መንግሥት ሊያስተናግደው የሚችለው ነገር አልነበረምና መስማማት አስቸጋሪ ሆነ፤ ፍጥጫው ቀጥሎ በስፋት ለተጠቀምነው የገበያ እቀባ (market boycott) መንገድ ጠረገልን። የንግዱ ማኅበረሰብ በትግሉ ውስጥ ብዙም ተሳትፎ ባለማድረጉ፤ የገበያ እቀባ ከዚያ ቀደም አልፎ አልፎ ከመሞከሩ ወጪ የተፈለገውን ያህል ውጤታ አላመጣም። የተወሰኑ ነጋዴዎች በድብቅ ለቄሮ የቁሳቁስ እና የገንዘብ ድጋፍ ቢያደርጉም በቀጥታ አልተሳትፉም። ይህም የሆነው ከሌሎች የኅብረተሰብ ክፍሎች ጋር ሲነጻጸሩ ነጋዴዎች በቁጥር ጥቂት በመሆናቸው፣ ማንነታቸው እና የሚሰሩበት ቦታ በቀላሉ ስለሚታወቅ ለመንግሥት የበቀል እርምጃ ተጋላጭ ያደርጋቸዋል።

በዚህ ወቅት ግን የግብር ጉዳይ ከማንም በላይ ነጋዴውን ስለሚመለከት፣ ለራሳቸው ሲሉ ንቁ ተሳትፎ ለማድረግ ይገደዳሉ። የገበያ እቀባ ዘዴ፣ አሠራር እና መከተል ያለብንን ሥነ-ምግባር ደጋግመን በሚዲያ ካስተማርን በኋላ ዘመቻውን አወጅን። ብዙም ሳይቆይ በሁሉም የኦሮሚያ ማዕዘናት ተዳረሰ። ይህንን ዘመቻ ለማክሸፍ መንግሥት ምንም ዓይነት ስልታዊ ዝግጅት ስላልነበረው ለማስፈራራት እና ሱቅ ለመዝረፍ ሞከረ። ነጋዴዎቹ ከጠበቅነው በላይ ጽናት አሳዩ። መንግሥትን በመፍራት ወይም በስግብግብነት የንግድ ሥራቸውን የከፈቱ ጥቂት ነጋዴዎችን ቄሮ በማኅበራዊ ሚዲያ በማጋለጥና በአካል ተገኝቶ በማስጠንቀቅ እንዲዘጉ አደረገ። ዓመቱን ሙሉ ከነበረው የንግድ እንቅስቃሴ ሁኔታ አንጻር መንግሥት ግብር መቀነስ ሲኖርበት ጭማሪ ማድረጉ አብዛኛውን የንግዱን ማኅበረሰብ አስቆጣ። ስለዚህ በአንዳንድ ቦታዎች ሱቆችን ለማዘጋት ሁለት ወይም ሦስት ቄሮዎች በመንገድ ማለፋቸው በቂ ነበር። ነጋዴዎች ሥራ ያቆሙበትን ምክንያት የመንግሥት አካላት ሲጠይቋቸው “ቄሮ አስፈራርቶን ነው” በማለት ከተጠያቂነት ማምለጥ ችለዋል።

በገበያ አድማው ዘመቻ ከነጋዴው የበለጠ መንግሥትን አስቸግሮ የነበረው ገበሬው ወደ ገበያ መውጣት ማቆሙ ነው። መንግሥት ሱቅ ያለውን ነጋዴ አስሮ በማስፈራራት በሁለት እና በሦስት ቀናት ማስከፈት ይችላል። በሳምንት አንድ ጊዜ ለዚያውም አልፎ አልፎ ለግብይት ከገጠር ወደ ከተማ የሚመጣውን ገበሬ ግን ካልመጣ ምን ያደርገዋል? ሚሊሻ በየቤቱ እየዞረ ወደ ገበያ ሂድ ቢለው “የምሄድበት ጉዳይ የለኝም” ይለዋል፤ ምን ብሎ ያስገድደው?

የገበያ እቀባውን በተለይ ለሽያጭ በሚውሉ ሰብሎች በሚታወቁ ዞኖች ተግባራዊ ማድረግ መንግሥት ላይ ከፍተኛ ጫና እንደሚፈጥር በመገመት በስፋት ተግባራዊ ተደረገ። ለምሳሌ የጫት ምርት ለሀገር ውስጥ እና ለውጭ ገበያ በሚያቀርቡ እንደ ሐረርጌ ያሉ ዞኖች ጫት ወደ ገበያ እንዳይሄድ ማድረግ ተችሏል። እቀባው ከሐረርጌ በሚመረተው የጫት አቅርቦት

ላይ ጥገኛ የሆኑትን የጂቡቲ እና የሱማሌላንድ ማኅበረሰቦችን በማሰቆጣት በመንግሥታቸው ላይ ከፍተኛ ጫና አሳደረ። በዚህ የተነሳ የሀገራቱ ባለሥልጣናት ብዙ ጊዜ ደውለው አቀባውን እንዳስነሳ ሊያግባቡኝ ይሞክሩ ነበር። ይህ ደግሞ የቄሮ ኃይል የኢትዮጵያን መንግሥት ብቻ ሳይሆን ጎረቤቶችንም መናጥ መጀመሩን አመላከተ።

እንደ ጂማ፣ጉጂ እና ወለጋ ባሉ ቡና አምራች ዞኖች መንገድ የመዝጋት እርምጃው የትራንስፓርት አገልግሎትን በማሰተጓጎል እና የውጭ ንግድን በመጉዳት መንግሥት የሚያገኘው የውጭ ምንዛሪ ገቢ እንዲያሽቆለቁል አድርጓል። የገበያ እቀባን ከመንገድ መዝጋት ጋር በማጣመር ውጤታማ ማድረግ ተቻለ።

የዚህ ሰልት ውጤት ከፍተኛ ከመሆኑ የተነሳ የግብር ጥያቄ ከተመለሰ በኋላም ለተለያዩ ተቃውሞዎች የገበያ እቀባ ማወጁን ቀጠልንበት። የግብርን ጉዳይ ለትግሉ መጠቀማችን መንግሥትን ለማዳከም ጥሩ ምርጫ ነበር። ከፍተኛ የግብር ገቢ ከሚያገኝበት የንግዱ ማኅበረሰብ ክፍል ጋር መጋጨቱ ለምንፈልገው የኢኮኖሚ አሻጥር (economic sabotage) እርምጃ አመቺ ሁኔታ ፈጥሯል።

ይህ የእቀባ ዘዴ ለትግሉ ያለው ፋይዳ ትልቅ ቢሆንም ሕዝባችንንም የሚጎዳ መሆኑን አሰቀድመን ተረደድተናል። ከእነዚህ ጉዳቶች መካከል የነጋዴዎች ገቢ መቀነሱ ምርት ከገበያ እንዲጠፋ በማድረግ ሕዝቡን ለችግር እንደሚያጋልጥ ግልጽ ነው። የእነዚህ ችግሮች መባባስ ሕዝቡን በማሰላቸትም ለትግሉ አሉታዊ አመለካከት እንዲኖረው ሊያደርግ ይችላል። ዕውቁ የሰላማዊ ትግል ሰትራቴጂሰት ሶል አለንሰኪ እንዳለው የተጓተተ ስልት ትግልን ወደኋላ ይጎትታል (tactic that drags on too long becomes a drag)።33 በመሆኑም የገበያ እቀባው ከሦሰት እስከ አምስት ቀናት ላልበለጠ አጭር ጊዜ እንዲሆን አድርገናል። በተጨማሪም እገዳው ከመጀመሩ ቢያንሰ ከአምስት ቀናት በፊት ማሳወቃችን፣ ነጋዴው እና ሌላው ሕዝብ ለሥራ ማቆም አድማው አስፈላጊውን ቅድመ -ዝግጅት እንዲያደርግ በቂ ሰጠው።

የገበያ እቀባው በትክክል እንዲተገበር የተጠቀምነው ተጨማሪ ስልት የትራንስፓርት እገዳ ነበር። የገበያ አቀባ የንግድ ቤቶችን መዝጋት እና በገበያ ቀናት ግብይት እንዳይካሄድ መከልከልን ያጠቃልላል። የትራንስፖርት እቀባ ደግሞ በከተሞች መካከል የንግድ እና የሕዝብ እንቅስቃሴን በመግታት የኢኮኖሚ እንቅሰቃሴ የበለጠ እንዲዳከም ያደርጋል። የትራንስፓርት እቀባው በትራንስፖርት ባለቤቶቹ ፈቃድ ብቻ ሳይሆን መንገድ በመዝጋት ሲፈጸም ነበር።

ስለዚህ የትራንስፖርት እቀባ ከገበያ እቀባ በደረጃ ከፍ ያለ ነው። የገበያ እቀባ የተቃውሞ ሰልት ሲሆን፣ መንገድ መዝጋትን ግን ጣልቃ ገብነት ነው። ሁለቱን አቀናጅተን ሥራ ላይ ማዋላችን ትልቅ ውጤት አስገኝቶልናል። አብዛኞቹ የትራንስፖርት ባለቤቶች የቄሮን ጥሪ ሰምተው በፍቃዳቸው ሥራ ሲያቆሙ፣ ጥቂቶች

ግን መንግሥትን በመፍራት እና በራሳቸው ስግብግብነት አድማውን ጥሰው ይሠሩ ነበር። ይህ ደግሞ ሥራ ያቆሙት ከሚያጡት ገቢ በተጨማሪ ለመንግሥት ተጋለጭ እንዲሆኑ ያደርጋቸዋል ። የመንገድ መዝጋት እርምጃ አድርባይ (oppotunistic) ነጋዴዎችንም ለማስገደድ ስለሚረዳ፣፣ የገበያ እቀባው ሙሉ በሙሉ ስኬታማ እንዲሆን ያደርጋል።

33 Alinsky, Saul D. Rules for Radicals: A Pragmatic Primer for Realistic Radicals. Vintage Books, 1971.

የመንገድ መዝጋት ስልት የጣልቃ ገብነት አካል በመሆኑ ከፍተኛ አደጋ (risk) አለው። ቄሮዎች በአካል መንገድ ላይ ተገኝተው ድንጋይ ለቅመው ስለሚዘጉ ለመንግሥት ወታደሮች ተጋላጭ ነበሩ። በዚህም በርካታ ቄሮዎች ለሞት፣ ለአካል ጉዳት እና ለእስራት ተዳርገዋል። የመንገድ መዝጋት ዘመቻ ለሌላ አደጋም አጋልጦን ነበር። በአንድ ወቅት ወደ ቄሮ መዋቅር ሰርገው የገቡ የመንግሥት ሰላዮች (agent provocateurs) ክልከላውን በጣሱ ተሽከርካሪዎች ላይ በምብ በመወርወር የቄሮን ስም ለማጥፋት አቅደው ነበር። ይህን ሤራ እንዳወቅን የአምስቱ ቀን እገዳ በሁለት ቀናት ውሰጥ እንዲቆም አደረግን። ሤራዉ ተሳክቶ ቢሆን ኖሮ በሕይወት ላይ የሚደርሰውን አደጋ ተጠቅመው ቄሮ ላይ ለመለጠፍ ሞክረው ያልተሳካላቸውን የሽብርተኝነት ክስ ለማጠናከር የሚችሉበት ዕድል ይፈጠራል። ለአምስት ቀናት የተጠራውን እቀባ ወደ ሁለት ቀን ለማሳጠር መወሰኑ በቄሮዎች ዘንድ ጊዜያዊ ቁጣን ቢፈጥርም ምክንያቱን ከገለጽን በኃላ እቀባው በስምምነት እንዲነሳ ተደርጓል።

በአጠቃላይ የገበያ እቀባ እርምጃዎች ጉዳት ሳያበዙ በትግሉ ላይ የሚሳተፈውን የኅብረተሰብ ክፍል በማስፋት መንግሥት ላይ ከፍተኛ ጫና አሳድሯል። የቄሮ ትግል በሀገሪቱ ኢኮኖሚ ላይ ያስከተለው ተጽዕኖ የሚካድ አልነበረም። በ2014 የቄሮ ትግል ሲጀመር የኢትዮጵያ ኢኮኖሚ በ10.3 በመቶ እያደገ የነበረ ሲሆን፣ በ2018 ለውጡ ሲመጣ ወደ በ6.8 በመቶ ቀንሷል። የኢኮኖሚው መዳከም ደግሞ መንግሥት እየተዳከመ መሄዱን ይጠቁማል።

መንግሥት ከኮማንድ ፖሰት በኋላ ቄሮ የተዳከመ መስሎት ተስፋ ቢያደርግም በተቃራኒው አዳዲስ የትግል ስልቶችን በመጨመር አድማሱን አስፍተን ሥርዓቱን የበለጠ መከፋፈል እና ማዳከም ቻልን። ከትግል ዘመቻዎች ጎን ለጎን ከመንግሥት ሰዎች ጋር ስናደርግ የነበረው ንግግር እና ድርድርም ወደ ውጤት እየተቃረበ መጣ።

# 7.10. የለውጡ ዋዜማ ድርድሮች

ገና ከጅምሩ ለመንግሥት ቀረቤታ ባላቸው ሰዎች፣ በመንግሥት ባለሥልጣናት እና በውጭ ዲፕሎማቶች አማካኝነት ለድርድር ያለንን ፈቃደኝነት ስንጠቁም ቆይተን፡ በሂደትም ምሥጢራዊ ውይይት ወደ ማድረግ ተሸጋገርን። ከእነዚህ አካላት ጋር ስናደርግ የነበረው ውይይት ምሥጢራዊ መሆኑ ለሁለቱም ወገን አስፈላጊ ነበር። ከመንግሥት ጋር አየተነጋገርን እንደሆነ ቢታወቅ ለከባድ የስም ማጥፋት ዘመቻ አጋልጦን ቅቡልነታችን ሊሸረሸር፣ ብሎም ንቅናቄው ሊከፋፈል ይችላል። በመንግሥት ወገንም ቢሆን አሸባሪ እያለ ከሚፈርጀው ወገን ጋር እየተነጋገረ መሆኑ በገሃድ ቢሰማ እንደ ውርደት ይቆጠራል። ይህ ደግሞ አክራሪ የሆኑ አመራሮች ለዘብተኞቹን በክህደት ወንጅለው ለማግለል ይረዳቸዋል። ከዚህ በመነሳት ቀድመው ያነጋገሩን ለመንግሥት ቅርበት ያላቸው ግለሰቦች እንጂ በግልጽ የተወከሉት ባለሥልጣናት አልነበሩም። ምክንያቱም የመንግሥት ባለሥልጣናት ከመጡ ጉዳዩ አድጎ ኦፊሴላዊ (official) በመሆን ውይይት የሚፈልገውን የመንግሥት አንጃ ይጎዳል፡ አልፎም ለቄሮ ትግል እውቅና በመስጠት የተጋድሎ ስሜቱን ከፍ ያደርጋል የሚል ሰጋት ነበራቸው። እኔን የሚያገኙኝ ሰዎች "የምናናግርህ መንግሥትን ወክለን አይደለም" የሚል ማስተባበያ ደጋግመው ያቀርቡ ነበር።

መጀመሪያ ላይ የመንግሥት ሰዎች እንደኛው ሁሉ ለድርድር ፈቃደኛ የሆኑት ለስልት ነበር። በድርድር ስም ቀርበውን በተለያዩ መንገዶች አታለው አቋማችንን በማለዘብ ወደ መንግሥት ጎራ የማሰኮብለል ተሰፋ ሰንቀዋል። መጀመሪያ ሰው የላኩብኝ አፐሪል 2014 ተቃውሞ ከተቀሰቅሰ ከጥቂት ጊዜ በኋላ ነው። የመጡት ሰዎችም የአዲሰ አበባን ማስተር ፕላን በጎነት ለማሳመን ቢሆንም፣ እኔ ግን ለውይይት መምጣታቸው በጎ ነገር መሆኑን ገልጬ የማስተር ፕላኑን ጉዳቶች በዝርዝር አሰረዳኋቸው። ከረጅም ክርክር እና ውይይት በኋላ፣ አንኳን ሊያሳምኑ ለራሳቸውም ጥርጣሬ ውሰጥ ገቡ። አልሆን ሲላቸው ወደ ሀገር ቤት እንድገባና ከገዢው ፓርቲ ጋር እየሰራሁ የማሰተር ፐላኑንም ሆነ ሌሎች ችግሮችን ለመፍታት በቀጥታ እንድሳተፍ ሊያሳምኑኝ ሞከሩ። በወቅቱ የመመለስ አቅድ አንደሌለኝ፣ መንግሥት የፖለቲካ ምህዳሩን ለማስፋትና ወደ ዴሞክራሲ ለመሸጋገር ተጨባጭ እርምጃ መውሰድ ከጀመረ ግን እንደምመጣ ነግሪያቸው ተለያየን።

ለሁለተኛ ጊዜ የተገናኘነው ዲሴምበር 2015 በጊንጪ የተጀመረው ሁለተኛው ዙር አመጽ ከተቀሰቀሰ በኋላ በ2016 የፈረንጆች አዲሰ ዓመት ገደማ ነበር። ከፍተኛ የፖለቲካ እና የደኅንነት አመራሮችን ካካተተው ቡድን ጋር ባደረግነው ውይይት፡ ማስሰተር ፐላኑ ካልተሰረዘ ቄሮ እሰካሁን ከተጠቀመባቸው እርምጃዎች የባሰ ለመወሰድ እንደሚገደድ አስጠነቀቅን። የመንግሥት ትዕግሥት አየተሟጠጠ መሆኑን እና አነሱም ሰልፉን ካላቆምኩ የከፋ ወታደራዊ እርምጃ እንደሚወስዱ በማሰፈራራት ሳንግባባ ተለያየን።

ወቅቱ ብዙ ሰው የሚገደልበት ቢሆንም የመጡትን ሰዎች ያናገርኳቸው ተረጋግቼ ነበር፣

ውዝግብ እና ክርክር አላበዛሁባቸውም። ብዙ ነገሮችን በተለሳለሰ አኳኋን ሳቀርብላቸው ቆይቼ፣፤ ምሳ ጋብዤ፣ ከተማዋን አሳይቼ እና አጫውቼ ሸኘኋቸው። ይህንን ያደረኩት በመንግሥት ላይ እያካሄድኩ ያለሁት ተቃውሞ ለሕዝብ ጥቅም እንጂ በግል ቂም ተነሳስቼ እንዳልሆነ ለማሳየትና እነሱም ሆኑ ሌሎች ባለሥልጣናት እንደ መንግሥትም እንደ ግለሰብም በፈለጉኝ ጊዜ አግኝተው ሊያነጋግሩኝ እንደሚችሉ ለማስታወስ ነበር። በተለይ በሚዲያ ስናገር የንዴት ስሜት ስለሚነበብብኝ፣ ግትር አቋም ያለኝ ስለሚመስላቸው፣ በአካል ሲያነጋግሩኝ አቋሜን በእርጋታ እና አለዝቤ ሳቀርብ ያሰገርማቸዋል። ይህ ስልት ከሚመጡት ሰዎች ጋር ጥሩ የግል ግንኙነት መፍጠር ስላስቻለኝ አንዳንዶቹን የሥርዓቱ የውስጥ መረጃ ምንጭ ለማድረግ አስችሎኛል።

ባለሥልጣናቱ ወደ ሀገር ተመልሰው ከሳምንት በኋላ ማስተር ፕላኑ ሊሠረዝ እንደሚችል ፍንጭ ሰጡኝ፤ ቀጥሎም የኦሕዴድ ማዕከላዊ ኮሚቴ ይህንኑ ውሳኔ በግልጽ ለሕዝብ አሳወቀ። የኦገሰት ሰድሰቱ (ሐምሌ ሠላሳ) ታላቅ ሰልፍ እና የኢሬቻን ዕልቂት በተከተለው ተቃውሞ የቄሮ ጥንካሪ በግልጽ ስለታየ፣ ከመንግሥት ጋር የምናደርገው ውይይትም ከመጀመሪያዎቹ የበለጠ ጠጠር እያለ መጣ። የመደራደር አቅማችን ማደጉን በመረዳት ጥያቄያችንን ከፍ አደረግን።

ከአምስት ቀኑ የቁጣ ዘመቻ በኋላ ባደረግነው አንድ ውይይት ለመጀመሪያ ጊዜ የሥልጣን ጥያቄ አነሳን። ይህን ጥያቄ መጀመሪያ ከአንደበቴ ሲሰሙት እንደ ቀልድ ወሰዱት፡ ከፈለግን እኔና ባልደረቦቼን ኦሮሚያም ሆነ ፌደራል መንግሥት ውስጥ ሥልጣን እንደሚሰጡን ተናገሩ። ከዚያም ኮሰተር ብይ ከነማብራሪያው በመድገም ቀልዴን እንዳልሆነ አሳየኋቸው። እየጠየቀን ያለነው የግል ሥልጣን ሳይሆን ሕወሓት የፌደራል ሥልጣኑን ለቆ ለኦሮሞ ማስረከብ እንዳለበት በግልጽ ነገርኳቸው።

ይሄኔ አንድ የሕወሐት ሰው «ሀገር መምራት ይቅርና ራሳችሁንም ለማሥተዳደር ዝግጁ አይደላችሁም›› በማለት በንቀት ሊያኮስሰን ሲሞክር፡ «የኦሮሞ ምሁራን ይቅርና የጴጥጋ አህያ ሥልጣን ብትይዝ ከእናንተ በተሻለ ሀገር መምራት ትችላለች›› አልኩት። የሰውዬው የንቀት ንግግር የፈጠረብኝ ስሜት በመመከት እሱንም መልሼ ለማናደድ የተጠቀምኩት አነጋገር ነበር። ውይይታችን ከወትሮ የጋለ ስሜት የነበረው ስለሆነ ሳንስማማ ተለያየን።

ኮማንድ ፖስት ኦሮሚያን በአሥተዳደረበት ወራት ተቃውሞ ስላልነበር፡ ቁሮ የተሸነፈ ሰለመሰላቸውና እኛን ማነጋገሩ አሰፈላጊ ሰላልመሰላቸው በዚያው ጠፉ። ነገሮች እነሱ አንዳሰቡት ስላልነበሩ፡ ከአሰቸኳይ ጊዜ አዋጁ በኋላ ተቃውሞው እየተባባሰ በመምጣቱ ተገናኝተን ብርቱ ክርክር አደረግን። አፋን አሮሞን የፌደራል የሥራ ቋንቋ ለማድረግ እና የፊንፊኔን ጥያቄ ለመመለስ ቃል ገብተው ለእኔ በክልልም ሆነ በፌደራል ደረጃ ሥልጣን ለመስጠት በድጋሜ ሐሳብ አቀረቡ። እንዲያውም ለምን ኦሮሚያን የማሥተዳደር ኃለፊነት ተረክበህ፤ አለ የምትለውን ችግር አትፈታም?›» አሉኝ። ዓላማቸው ከኦሕዴዶች ጋር ሊያላትሙን እንደሆነ ግልጽ ነበር። እኔ ግን ሕወሓት ከሥልጣን መልቀቅ አለበት በሚለው አቋም ጸንቼ አሻፈረኝ አልኩ።

በቦታው የሽምጋይነት ሚና ሊጫወት ሲሞክር የነበረ አንድ ፈረንጅ «በዚህ ግትርነትህ ቀጥለህ ሕዝብ የምታሰፈጀው እስከ መቼ ነው?» ሲለኝ፤ «ሃምሳ ሚሊየን ኦሮሞዎች አሉ፣ ከዚህ ውሰጥ አርባ ዘጠኝ ሚሊዮኑን መሥዋዕት በማድረግ የቀሩትን አንድ ሚሊዮን ነጻ ለመውጣት

ዝግጁ ነን› አልኩት። ሰውዬውም «ለመሆኑ እብድ መሆንህን የኦሮሞ ሕዝብ ያውቃል?» ብሎ ሲጠይቀኝ፡ በቀልድ መልክ «አዎ በትክክል ያውቃሉ፡ እንዲያዉም ይህን እብደቴን በጣም ይወዱታል› በማለት መለስኩለት።

በዚያ ዙር ውይይት በመንግሥት በኩል ያለው አቋም እየለዘበ መምጣቱን ፍንጭ ተመለከትኩ። ለምሳሌ ለሻይ ዕረፍት ስንወጣ እንደቀልድ ሥልጣን የሚሰጥ ከሆነም ገዢው ፓርቲ ውሰጥ ላሉ ኦሮሞዎች ካልሆነ በስተቀር ለተቃዋሚዎች መስጠት የሚታሰብ እንዳልሆነ ጠቆም አደረጉ። በወቅቱ ይህን ሐሳብ በግልጽ ባንቀበልም ለእኛ ትልቅ ድል ነበር። በሕወሓት የበላይነት የሚመራው አገዛዝ ሊቀጥል እንደማይችል እየተረዱ እንደሆነ ስለሚያሳይ ወደ ግባችን እየተጠጋን መሆኑን ተረዳን።

ሥልጣን በኦሮሞ እጅ ሊገባ እንደሚችል በራሰ መተማመን ሲፈጠር ቀጣዩ ሥራ ያን ሥልጣን ይዞ ሀገርን ወደ ዴሞክራሲ የሚያሻግር ድርጅት እና ሰው ማፈላለግ ነበር። መንግሥትን እንዳለ ከመጣል ይልቅ ከውሰጡ ለውጥ ፈላጊ ቡድን ወደ ሥልጣን የማምጣት ዓለማ አስቀድመን ብናስቀምጥም፤ ቡድኑ ለብቻው ሥልጣን ከያዘ የሚፈለገውን ለውጥ ማምጣቱ ስለመቻሉ ጥርጣሬ ገባን። ስለዚህ የገዢው ፓርቲ አባላት ከፍተኛ የአመራር ቦታዎችን ቢይዙም በተወሰነ ደረጃ ሥልጣን ለተቃዋሚዎች ማጋራት ሽግግሩን ስኬታማ ለማድረግ ይረዳል የሚል ተስፋ ነበረን። ዕድሜ ልካቸውን ለነጻነት እና ለዴሞክራሲ የታገሉ የተቃዋሚ ፓርቲ አመራሮች ወደ መንግሥት መቀላቀላቸው ገዢው ፓርቲ የገባውን ቃል እንዳያጥፍ ጫና ለማድረግ ይረዳል ብለን አሰብን። በተለይም ብዙ የኦሮሞ ልሂቃን ከአገዛዙ ውጪ በመሆናቸው ወደ መንግሥት መቀላቀላቸው የታሰበውን ሽግግር በክኅሎት እና በእውቀት በመደገፍ ያጠናክራል የሚል እምነት ነበረን።

ገዢው ፓርቲ የሚመራው ነገር ግን ተቃዋሚን የሚያሳትፍ ሽግግር ለማሳካት ገዢው ፓርቲ ውስጥ ያሉትን ሰዎች እና ቡድኖች በመለየት ለሕዝባዊ ትግሉ አስተዋጽኦ የሚያደርጉትን በሕዝብ ዘንድ ቅቡልነት እንዲያገኙ ማስቻል ያስፈልጋል።

የቄሮ ትግል ከመጀመሩ በፊት ከኦሮሞ ልሂቃን አብዛኛው ኦሕዴድ ውስጥ ስለነበሩ፡ እነርሱን ሙሉ በሙሉ በማግለል ትግሉን ማሳካት አይቻልም የሚል መከራከሪያ ሰቀርብ ነበር። በሂደትም የኦሕዴደን ነውርነት (taboo) ቀሰ በቀሰ መሸርሸር ስለተቻለ፣ በቄሮ ትግል ወቅት በግልጽ "ኦሕዴድን ነጻ ማውጣት አለብን የሚል ሐሳብ ማራመድ ቻልኩ።

ኦሕዴድን ነጻ የማውጣት ሐሳብ፣ድርጅቱ በፍላጎቱ የጨቋኙ አገዛዝ አካል የሆነሳይሆን ተገዳጅ እና ተበዳይ አድርጎ የሚስል ነበር። በዚህ መልኩ አንድ ጓደኛዬ እንደገለጸው፣ ኦሕዴድን በኦሮሞ ፓለቲካ ውስጥ "ማንጻት (ሃላል ማድረግ) ተቻለ። በሰፋት በሰራነው የገጽታ ግንባታ ሥራ እና በለማ መገርሳ የሚመራው ቡድን ኦሕዴድን ከተቆጣጠረ በኃላ በንግግሮቹ ውሰጥ የትግሉን ሐሳብ አጉልቶ አጋርነት በማሳየቱ ሕዝቡ እጁን ዘርግቶ ተቀበለው። በሌላ በኩል ለተቃዋሚ ኃይሎች ሥልጣን በማጋራት የሽግግሩን ስኬት እንዲያግዙ ስላሰብን አስቀድመው እንዲዘጋጁ ብዙ ሙከራዎች ተደርገዋል። ከእነዚሀ ድርጅቶች መካከል አብዛኞቹ በስደት፡ ሀገር ውስጥ ያሉት ደግሞ አመራሮቻቸው እሰር ቤት ነበሩ። በተለይ ውጪ የነበሩት ኃይሎች በብዙ ጎራ ተከፋፍለው ስለነበር በተቀናጀ መልኩ ተደራድረው ሥልጣን ለመጋራት የሚያሰችላቸው ቁመና ላይ አልነበሩም። ተቃዋሚዎች በተከፋፈለ መልኩ ሥልጣን ለመጋራት መቅረባቸው ገዢው ፓርቲ የበላይነት እንዲያገኝ ያሰችላል። በተጨማሪም

በውጪ የነበሩት ቡድኖች በአብዛኛው የአካባቢያዊነት መልክ ስላላቸው ወደ ሀገር ገብተው በተከፋፈለ ሁኔታ በመንግሥት ውስጥ ሥልጣን ከተጋሩ፣ ትላንት ኦነግን ያዳከመውን ዓይነት መርዝ ወደ ሰፊው ሕዝብ እንዲረጩ ማመቻቸት ይሆናል።

የተቃዋሚዎችን የመከፋፈል ችግር ለማሰወገድና ውጪ ያሉ የፖለቲካ ፓርቲዎችን ቢያንስ በአንድ ኅብረት (alliance/coalition) ሥር ለማዋሐድ የተለያዩ ሙከራዎች ቢደረጉም አልተሳካም። የፖለቲካ ድርጅቶችን ማዋሐድ ካልተቻለ፣ በውጪ ያሉ የኦሮሞ ልሂቃን የጋራ አቋም ሊይዙ ይችላሉ ብለን ተሰፋ አደረግን። በ2016 የኦሮሞ አመራር ጉባዔ (Oromo Leadership Convention) በማዘጋጀት የፓለቲካ መሪዎች፣ ምሁራን፣ የሀይማኖት አባቶች፣ የሚዲያ አንቂዎች እና የተለያዩ የማኅበረሰብ ክፍሎች ስለ ኦሮሞ ትግል የወደፊት ዕጣ ፈንታ ተወያይተው የጋራ አቋም እንዲያዳብሩ ሙከራ አደረግን።

ከመጀመሪያው አንስቶ አንዳንድ ሰዎች እና ቡድኖች በተለያዩ ምክንያቶች ለመሳተፍ ፈቃደኛ አልሆኑም። የተወሰኑ አንቂዎች ከእኔ ጋር ባላቸው ቅራኔ ከመሳተፍ ተቆጠቡ፣ በአቶ ዳውድ ኢብሳ የሚመራው የኦነግ ቡድንም ለመሳተፍ ፈቃደኛ አልነበረም። በጉባዔው መሳተፍ ያልፈለጉት ጠንካራ ተቃውሞ እና የፕሮፓጋንዳ ዘመቻ አካሄዱ። ጥያቄያቸውን እና ቅሬታቸውን በሽማግሌዎች በኩል አዳምጠን ለመመለስ ብንሞክርም አልተሳካልንም። በዚህ ምክንያት እቅዳችንን ያለእነርሱ ለማስኬድ ስንገደድ እነርሱም ሌላ ተመሳሳይ ጉባዔ አዘጋጅተው በመስመራቸው ገፉበት።

የመጀመሪያው የኦሮሞ አመራር ጉባዔ ከስድሰት መቶ በላይ ተሳታፊዎች ከሰሜን አሜሪካ እና ከአውሮፓ በተገኙበት ከኖቬዢምበር 11 አሰከ 13 ቀን 2016 በአሜሪካ አትላንታ ከተማ ተካሄደ። በጉባዓው ላይ በተደረጉ ውይይቶች የኦሮሞ ትግል የደረሰበትን ደረጃ ከገመገምን በኋላ የዲያስፖራ ማኅበረሰብ ሊሠራ የሚገባውን ሥራ በተመለከተ የተነደፈው እቅድ በሁለቸ ዶክመንቶች ተዘጋጅቶ ፀደቀ።

*ሀ/ ተሳታፊዎች የተወያዩበት እና የተስማሙበት የኦሮሞ ትግል ጥያቄዎች እና ዓላማዎችን የሚዘረዝረው "የኦሮሞ ቻርተር"፣*

*ለ/ የዲፕሎማሲ እና የሰብዓዊ እርዳታ ሥራን ለማስተባበር የወጣ የድርጊት መርሐ ግብር ረቂቅ ናቸው።*

በዚሀም መሠረት የዲፐሎማሲ እና የሰብዓዊ እርዳታን የሚያስተባብር ግብረ -ኃይል ተቋቋመ። በዋሽንግተን ዲሲ እና በሂውስተን በተከታታይ በተካሄዱ ጉባዔዎች እነዚህ ረቂቆች የበለጠ ተብላልተው ተግባራዊ ሆነዋል። የኦሮሞ አመራር ጉባዔ መጀመሪያ ላይ እንዳሰብነው የኦሮሞ ልሂቃኖች መካከል ቅንጅች
በመፍጠር ለሥልጣን ክፍፍል ማዘጋደጀት አስቸጋሪ እንደሆነ ተረዳን። እቅዳችን ተቃዋሚ ቡድኖችን/ልሂቃንን በማሰባሰብ ከተሳካልን፡ መጀመሪያ በኦሮሞ ደረጃ ቀጥሎ በኢትዮጵያ ደረጃ ለሥልጣን ማዘጋጀት ነበር። የኦሮሞው አለመሳካቱን ስናይ፣ የተቃዋሚ ቡድኖችን የማስማማቱን ጉዳይ ትተን ገዢው ፓርቲ ውሰጥ ያሉ እና ለውጥ የሚሹትን አብቅተን ወደ ሥልጣን እንዲመጡ ከማድረግ ውጪ ሌላ አማራጭ እንደሌለን ተገንዝብን በዚሁ መስመር ጉዟችንን ቀጠልን።

አንድን ለውጥ ለማሳካት ራቅ አድርጎ የመዘጋጀች አስፈላጊነት ሁሌም በአእምሮዬ ሲመላለስ ነበር። ለምሳሌ በ2006 ልክ አሜሪካ እንደሄድኩ ቱባ ቱባ የኦሮሞ የፓለቲካ መሪዎች እና ምሁራን በተሰበሰቡበት አጋጣሚ በውይይት መሀል «በ2020 ወያኔን ለመጣል የሚያስችል እቅድ አውጥተን አንሥራ› የሚል ሐሳብ ሳቀርብ ብዙዎች በአግራሞት ተመለከቱኝ። ግማሹ ቀልዴን መስሎት ሳቀ፣ አንዳንዶች «ባርነት ለአሥራ አምስት ዓመታት እንዲሰለጥንብን ትመኛለሀ?› ብለው ተቆጡኝ፡ «የላከው መንግሥት ነው» ብለውም አወገዙኝ። በወቅቱ በተባለው ጊዜ ለውጥ ለማምጣት የሚያስችል ምንም ተጨባጭ እቅድ አልነበረም። 2020 ያልኩት በየጊዜው አገዛዙ የሚያደርሰውን ግፍ እየተከተልን ከመኮነን ይልቅ የራሳችንን የረጅም ጊዜ የትግል እቅድ ብናወጣ ይሻላል በሚል ነበር።

ሐሳቤ በቦታው ተቀባይነት ቢያጣም ሥርዓቱን በ2020 ለመቀየር እቅድ ማውጣት አለብን የሚለውን ሐሳብ ግን ከውስጤ አላወጣሁትም። እናም ስለ ሰላማዊ ትግል ተምሬ እና ለኦሮሞ አንዲመች አድርጌ መቀየስ ስጀመር ትግሉ ሊጠናቀቅ የሚችልበትን ግምታዊ ጊዜ በማሰቀመጥ፣ እያንዳንዱን የትግል አርምጃ ከዚያ ጊዜ ወደኋላ ማስላት (backward planning) ነበረብኝ። ሁሌም በጭንቅላቴ የሚመላለሰውን 2020ን የስሌቱ መድረሻ ነጥብ (end point) አድርጌ አሰቀመጥኩ።

በአምባገነን ሥርዓት ላይ የሚደረገው ትግል በሁለት ደረጃዎች የሚከናወን ነው። የመደመሪያው በሥልጣን ላይ ያለውን ጨቋኝ አገዛዝ በማዳከም አሊያም በመገርሰስ ወደ ዴሞክራሲ እንዲሾጋገር በማስገደድ ነው። ሁለተኛው በትግል የመጣው ለውጥ ሳይጠለፍ እና ሳይደናቀፍ ሀገሪቷን ወደ ዴሞክራሲያዊ ሥርዓት ማሸጋገር መቻል ነው።

ሕዝባዊ አመፆች አብዛኛውን ጊዜ አምባገነኖችን ማሰወገድ ወይም ለውጥ እንዲያደርጉ ማስገደድን የሚያሳኩ ሲሆን፣ ሕዝቡ የታገለለትን ነጻነት የሚያረጋግጥ አዲስ ዴሞክራሲያዊ ሥርዓት በመገንባት ረገድ ብዙም አንደማይሳካላቸው ታሪክ ያሳያል።

በ1966 ዓ.ም በሀገራችን የተካሄደውን ጨምሮ በርካታ ሕዝባዊ አብዮቶች ያለፈውን ሥርዓት ቢያሰወግዱም የዴሞክራሲያዊ ሥርዓት ግንባታ ዓላማቸውን ከዳር ሳያደርሱ ቀርተዋል። ለዚህ ቀዳሚው ምክንያት የሕዝባዊ ንቅናቄዎች አደረጃጀት እና አካሄድ በሥልጣን ላይ ያለውን አምባገነን ለመጣል እንጂ ሥልጣን ለመያዝ ስለማያዘጋጃቸው ነው። ይህ ደግሞ አንድ አምባገነናዊ አገዛዝ በሕዝባዊ ትግል ሲወገድ የሚፈጠረውን የሥልጣን ክፍተት ሌላ የተደራጀ ቡድን ጠልፎ አዲስ አምባገነናዊ ሥርዓት አንዲገነባ ዕድል ይሰጠዋል።

ሕዝባዊ ንቅናቄዎች መጨረሻ ላይ የሚያጋጥማቸውን አደጋ አስቀድመን ከታሪክ ሰለተረዳን፡ የቄሮ ንቅናቄም ተመሳሳይ ዕድል አንዳይገጥመው አስበንበታል። ሰለሆነም 2020ን የአቅዳችን የመገባደጃ ጊዜ አድርገን ሰናስቀምጥ፣ አገዛዙን ለማናዳም ብቻ ሳይሆን ለውጡ አንዳይጠለፍ በመከላከል ዴሞክራሲያዊ ሽግግሩን ለማሳካት የሚያሰችሉ ቅድመ ዝግጅቶችንም አካትተናል።በዚሀም መሠረት መጀመሪያ ላይ አገዛዙን በማዳከም ላይ በማተኮር አስተማማኝ ደረጃ ላይ ከተደረሰ በኋላ፣ ቀጥለን የሥልጣን ክፍተት ወይም የመጠለፍ አደጋን ለመቅረፍ የሚያስፈልጉ ሥራዎችን ለመሥራት አቀድን። የቄሮ እንቅሰቃሴ ከገመትነው ጊዜ ቀድሞ ፈንድቶ ካሰብነው በላይ መጠናከሩ እና አምባገነኑ አገዛዝ ለመዳከም መፍጠኑ የሽግግር እቅዱን በተያዘለት ቅደም ተከተል ተግባራዊ ለማድረግ ጊዜ አጠረን።

የሕዝባዊ ንቅናቄ ድልን ወደ ዴሞክራሲያዊ ሥርዓት ለማሸጋገር ፤ ሥልጣን በንቅናቄው ዓላማ በሚያምኑ ሰዎች እና ቡድኖች መያዝ ወይም ንቅናቄው ባለሥልጣናቱን ሊቆጣጠርበት የሚችል አደረቋጀች ማበጀት ያስፈልገዋል። ይህ አስቀድሞ መዘጋጀትን የሚጠይቅ ሲሆን፡ ዝግጅቱም በሦስት መንገዶች ሊከናወን ይችላል። አዲስ የፖለቲካ ድርጅት በማቋቋም፣ ያሉ ድርጅቶችን አግባብቶ እና አጠናክሮ ለሥልጣን ማዘጋጀት ወይም ከሥርዓቱ ውስጥ ለውጥ የሚፈልጉ ሰዎችን/ቡድኖችን እና ተቃዋሚ ኃይሎችን በማጣመር ሥልጣን እንዲጋሩ ማግባባት ናቸው። ከላይ እንደተጠቀሰው ነባር የተቃዋሚ ቡድኖችን ማስማማት ስላልተቻለ ተቃዋሚዎችን እና በአገዛዙ ውሰጥ ያሉ ለውጥ ፈላጊ ኃይሎችን አግባብቶ ለሥልጣን መጋራት ማዘጋጀት አዳጋች ሆነ። አዲሰ ድርጅት ማቋቋም ደግሞ በእቅዳችን ውስጥ አልነበረም፡ ለማቋቋም ብናስብም በቂ ጊዜ አልነበረም።

ትግሉ እየተጋጋለ እና አገዛዙም እየተዳከመ ሲሄድ አባዱላ ገመዳ ደውሎ አዲሰ የፖለቲካ ድርጅት እንዳቋቁም አበክሮ መከረኝ። ያቀረበው ምክንያት ገዢው ፓርቲም ሆነ ተቃዋሚዎች ወደ ሥልጣን ከመጡ የቄርን ጥያቄ መመለስ አይችሉም የሚል ነበር። እንደ እሱ እምነት ከሆነ የገዢው ፓርቲ ባሕል፣ ርዕዮተ-ዓለም እና ነባራዊ ድርጅታዊ ቁመና የአዲሱን ትውልድ ጥያቄ ለመመለስ ስለማያምች፡ የአመራር ለውጥ ቢመጣ እንኳን አዲሰ የፖሊሲ እና የሰትራቴጂ ለውጥ ለማምጣት አዳጋች ይሆናል። ተቃዋሚ ፓርቲዎች ኋላ ቀር የሆነ ግትር (21924) አቋም ያላቸው እና የተከፋፈሉ በመሆናቸው፡ ሥልጣን ቢይዙ ሀገርን እና ሕዝብን ወደ ብጥብጥ ከመምራት በሰተቀር የቄሮን ምኞች ማሳካት ይሳናቸዋል የሚል ነበር። ስለዚህ «ምኞታችሁ እውን እንዲሆን ከፈለጋችሁ፣ ይህን ሥርዓት መቀየር ብቻ ሳይሆን ሥልጣን መያዝ አለባችሁ። ሥልጣን ለመያዝ ደግሞ የፖለቲካ ድርጅት የግድ ሊኖራችሁ ይገባል» አለኝ።

በበኩሌ ሥልጣን የመያዝ ምኞትም ሆነ ፍላጎት በፍጹም አልነበረኝም። ነገ ሥልጣን ለመያዝ የሚመኝ ሰው ዛሬ ውጤታማ ትግል ማካሄድ አይችልም የሚል እምነት ነበረኝ። በጊዜው ደጋግሜ ሰናገር እንደነበረው ወደፊት ሥልጣን ለመያዝ የሚፈልግ ሰው ዛሬ ሊደርሰበት የሚችለውን አደጋ በመቀነሰ ግላዊ እና ፓለቲካዊ ሕይወቱን አራዝሞ ነገ ወደ ሥልጣን ቦታ መድረሰ አለበት። ስለዚህም ትግሉ የሚጠይቀውን አደጋ እና መሥዋዕትነት መጋፈጥ አይችልም።

አቋሜ እንዳለ ሆኖ ከአባዱላ እንደመጣ ሳልነግራቸው የፓለቲካ ድርጅት መመሥረት በሚለው ሐሳብ ላይ ከተወሰኑ የውጭ ሀገር አንቂዎች እና ከሀገር ውሰጥ የቄሮ አስተባባሪዎች ጋር ተወያየንበት። ውጭ ያሉ አንዳንድ ሰዎች የፖለቲካ ድርጅት የመመሥረትን ሐሳብ ደግፈዋል። በተለይ ዶ/ር አወል አሎ ከኢሬቻ ግድያ በኃላ ይህንን ሐሳብ አጽንዖት ሰጥቶ ሲናገር እንደነበር አስታውሳለሁ። የአገር ውሰጥ አስተባባሪዎች ግን የፖለቲካ ድርጅት የመመሥረትን ሐሳብ አልደገፉም። «አሰካሁን የኦሮሞ ትግል የተዳከመው በፖለቲካ ድርጅት ቡድኖች ሆኖ ሳለ ሌላ አዲሰ ድርጅት መመሥረት ቄሮን ከፋፍሎ ወደ ትናንቱ ችግር መመለስ ነው› በማለት ሞገቱ። እንዲያውም ብዙዎቹ ቄሮዎች የፓለቲካ ፓርቲ መሥርቶ ለሥልጣን መዘጋጀት የሚለውን ሐሳብ እንደ ነውር ተመለከቱት።

በአጠቃላይ የፓለቲካ ድርድት የመመሥረት ሐሳብ ፍላጎት እና ጊዜውም ስላልነበረ አልገፋንበትም። ተቃዋሚ የፖለቲካ ድርድቶችን ማስተባበር ካልተቻለ እና ሌላ የፖለቲካ

ድርጅት መመሥረትም ካልተፈለገ፤ መፍትሔው ከ ገዢው ፓርቲ ለወጣ እና የሕዝብ ውግንና ላለው ቡድን ሥልጣን መሥጠት ይሻላል የሚለው አማራጭ ላይ አተኮርን። በመሆኑም ከኦሕዴድ፣ ብአደን እና ደሕደን ውስጥ ለውጥ ደጋፊ የሆኑ ሰዎች ሥልጣን ቢይዙ ጠቃሚ እንደሚሆን ሕዝቡን ለማሳመን በተለያዩ መንገዶች ዘመቻችንን አጠናክረን ቀጠልን።

ይህንንም ያደረግነው ያለ ምክንያት አልነበረም። አባዱላ የኦሮሚያ ፕሬዝዳንት በነበረበት ወቅት፤ የሕወሓት ጣልቃ ገብነትን በመቀነሰ ድሮ ጠባብ እየተባሉ ሲገለሉ የነበሩ ወጣቶችን ወደ መንግሥት በማስሰገባት የክልሉን አስተዳደራዊ ሥራ በማሳለጥ ልማቱን ማፈጠን ችሎ ነበር። በተመሳሳይ ሁኔታ ለማ ወደ ፕሬዝዳንትነት ሲመጣም የኦሮሞን ትግል እንደ ጠላትነት መቆጠሩ ቀርቶ በግልጽ አጋርነቱን አሳየ። ከዚህ በመነሳት እነዚያ ድርጅቶች ኦሕዴድም ሆነ ሌሎች የኢሕአዴግ አባል ድርጅቶች ከሕወሓት የበላይነት ነጻ ከወጡ እና ለውጥ ፈላጊ በሆኑ ሰዎች ከተመሩ ለሕዝባቸው ጥቅም የተሻለ ይሰራሉ የሚል ግምት ስላሳደረብን ነው።

ኦገስት 2017 ከመንግሥት ሰዎች ጋር ሌላ ዙር ውይይት አድርገን የበለጠ መቀራረብ ቻልን። ዋና ዋና የሕወሓት አመራሮች የፌደራሉን ሥልጣን ለማስረከብ መስማማታቸውን ተረዳን። አሁንም ግን የጠቅላይ ሚንስትርነት ሥልጣኑን ገዢው ፓርቲ (ኢሕአዴግ) ውሰጥ ላለ አንድ ኦሮሞ ለማሰረከብ እንጂ ለተቃዋሚ ፓርቲዎች እንደማይሰጡ አጥብቀው ሞገቱ። ሽግግሩ ስኬታማ እንዲሆን ሁሉንም ፓርቲዎች ማሳተፍ የተሻለ እንደሆነ ብንከራከርም እነርሱ ግን በአቋማቸው ጸኑ። የምንከራከረው ለይምሰል አንጂ ቀደም ብለን የለማ ቡድን ሥልጣን ቢይዝ ይሻላል የሚል አቋም ላይ ደርሰን ስለነበር ከኦሕዴድ ውስጥ ጠቅላይ ሚኒስትር የመምረጡን ሐሳብ ተቀበልን።በኦሮሞ በኩል በሦሰት ጉዳዮች ላይ ዋስትና መስጠት እንዳለብን በአሸማጋዮቹ ተነገረን። ይህም፣

ሀ. ሕወሐት ሥልጣን ላይ በቆየባቸው ዓመታት ለተፈጸሙ ጥፋቶች በበቀል እንዳይከሰሱ (immunity against persecution) ፤

ለ. በግለሰብ እና በቡድን ያፈሩት ንብረት እንዳይወረስባቸው፡ እና

ሐ.የትግራይ እና የሕዝቦቿ ደኅንነት ለውጭ እና ለውስጥ አደጋ እንዳይጋለጥ የሚሉ ነበሩ።

እነዚሀ ጉዳዮች ቀድመን የገመትናቸው ስለነበሩ ለመቀበል አስቸጋሪ አልሆነብንም። ለትላንት በደል ቂም ይዞ መበቀል የኦሮሞ ባሕል አንዳልሆነ በመግለጽ ለተፈጸሙት ወንጀሎች ተጠያቂነት አሰፈላጊ ክሆነ ወደፊት በብሔራዊ አርቅ እና በሽግግር ፍትሕ ሂደት ሊፈታ ይችላል አልናቸው። በዚህ መልኩ በዋና ዋና ጉዳዮች ላይ በመርህ ደረጃ ከተግባባን በኋላ ፓርቲያቸውን አማክረው ኦፊሴላዊ ውሳኔ ላይ ለመድረስ ቃል ገቡ። እስከዚሀ ጊዜ ድረስ ምንም ሕጋዊ እና ኦፊሴላዊ ውክልና እንደሌላቸው ደጋግመው በማስታወስ፤ የምንወያይባቸውንም ጉዳዮች ኢ-መደበኛ በሆነ መንገድ እንደ ምክረ-ሐሳብ ብቻ አንደሚያደርሱ ይናገሩ ነበር። እኛም የውይይቱን ውጤት ለቄሮ አስተባባሪዎች ከማሰተላለፍ በስተቀር ልክ እንደእነሱ የመወሰን ሥልጣን እንደሌለን ተናገርን። የውይይቱን ምሥጢራዊነት ለመጠበቅ እና ሾልኮ ቢሰማ እንኳን ለመካድ እንዲያመች፡ ለተወሰኑ የውጭ ሀገር አንቂዎች እና ሀገር ቤት ላሉ አስተባበሪዎች

ውይይት እየተካሄደ መሆኑን ፍንጭ ከመስጠት ባለፈ ትንፍሽ አላልኩም። ከመጀመሪያው አንስቶ ሲያነጋግረን የነበረ አንድ ቋሚ የሕወሓት ቡድን ቢኖርም በሂደት የተለያዩ የአገዛዙ አንጃዎች ሊደራደሩን ይቀርቡን ጀመር። ይሄ ደግሞ በአገዛዙ ውስጥ መናበብ እንደሌለ ስለጠቆመን ለትግሉ በሚጠቅም መልኩ ተጠቀምንበት።

ሕወሐት የፌደራል ሥልጣን ለመልቀቅ መስማማቱን የቄሮ ድል አድርገን ብንወስድም ምናልባት እየመጣ ያለውን ለውጥ ለመቀልበስ ያሰቡት ሤራ ሊሆን ይችላል የሚል ጥርጣሬ ፈጠረብን። የቀራቸው ካርድ ምን ሊሆን እንደሚችል ሥናስብ፤ ምናልባት ሥልጣናቸውን ለኦሮሞ ለማስረከብ አስቀድመው ቃል ከገቡ በኋላ የኦሕዴድ ባለሥልጣናትን የእርስ በእርስ ሽኩቻ ውስጥ ሊከቱ አስበው ይሆናል የሚል ግምት ያዝን።

ሥልጣን እንደ ኳሰ 'ሻሞ" ብለው ወርውረው በኦሮሞ ባለሥልጣናት መካከል ፉክክር እና መከፋፈል ፈጥረው ካዳከሙ በኋላ፡ አንድም የሚፈልጉትን ኦሮሞ ሊሾሙ፣ አሊያም ኦሮሞ አልተስማማም በማለት ከሌላ ወገን ሊያመጡ ይችላሉ ብለን አሰበን። በተለይ ሥልጣን ለኦሮሞ የመስጠቱን ጉዳይ በኢሕአዴግ ደረጃ ሳይወያዩበት ለእኛ መንገራቸው ጥርጣሬያችንን አጠናከረው። ስለዚህ ሕወሐቶች አቅደውት ሊሆን ይችላል ብለን ያሰብነውን ሸር ለማክሸፍ *የጠቅላይ ሚኒስትርነቱን ቦታ በሚይዘው ሰው ላይ አሁኑኑ መስማማታቸው አስፈላጊ መሆኑ አጽንዖት ተሰጠው።*

# 7.11.ለውጡን ማን ይምራው?

ከተወሰነ ጊዜ በኋላ ከኦሕዴድ ከፍተኛ ባለሥልጣናት መካከል አንድ ሰው ከሀገር ሲወጣ ደውሉልኝ በጉዳዩ ላይ አወያየሁት። ወሬ ከመጀመራችን «ሥልጣን ለመረከብ ተዘጋጁ» ስለው "አንተ አሁንም ትቀልዳለሀ? ሥልጣን እንዲሁ በቀላሉ በእጃችን ይገባል? ሕወሓትን አሁንም አላወካትም ማለት ነው። እንዲህ በቀላሉ አይለቁም » በማለት ንግግሬን አጣጣለ። ለውጥ እየመጣ መሆኑን እና ሕወሐት ሥልጣኑን ለኦሮሞ ለማሰረከብ መስማማቱን ዘርዘር አድርጌ ስገልጽለት ልብ ብሎ መስማት ጀመረ። «ኃይለማርያም ደሳለኝ በቅርቡ ከሥልጣን ሊወርድ ሰለሚችል፣ እናንተን (ኦሕዴድን) ወክሎ ጠቅላይ ሚኒስትር የሚሆን ሰው ካሁኑ ተስማምታችሁ አዘጋጁ »አልኩት። በአንድ እጩ ላይ አስቀድሞ የመግባባት አስፈላጊነት ላይ ተስማማን። ወደ መጨረሻ ላይ እነማን ሊሆኑ ይችላሉ የሚል ጉዳይ ተነሰቶ ሦስት ስሞችን ጠቀሰ፡ አባዱላ ገመዳ፣ ወርቅነህ ገበየሁ እና ዐቢይ አሕመድ።

ከዚያ በፊት ኦሕደዴዶች ለ ጠቅላይ ሚንስትር እንዲሆን ያለምንም ማመንታት በሙሉ ሰምምነት ይቀበላሉ ብዬ አስቤ ነበር። ከዚህ በመነሳት ሕዝቡ የለውጡ መሪ (de facto leader) አድርጎ እንዲቀበለው የተደራጀ ዘመቻ በመገናኛ ብዙኃን እያደረግን ስለነበር፣ በዝርዝሩ ውሰጥ አለመካተቱ አስገረመኝ። «ለማ መገርሰስ?» ስለው፡ «እሱ የሕዝብ ተወካዮች ምክር ቤት (ፓርላማ) አባል አይደለም። ስለዚሀ ጠቅላይ ሚኒሰትር ለመሆን መስፈርቱን አያሟላም» አለኝ። ጉዳዩ ያልጠበኩት ስለነበር ጊዜ ወስጄ ለማሰብ እና ከሌሎች ሰዎች ጋር ለመወያየት ሌላ ቀጠሮ ይዘን ተለያየን።

ስልኩን እንደዘጋሁ የሆነውን ለተወሰኑ ሰዎች (የኦሕዴድ መካከለኛ አመራሮች እና የመከላከያ መኮንኖችን ጨምሮ) አሳውቄ ሰፋ ያለ ውይይት አደረግንበት። ከኦሕዴዱ ሰው ጋር ስንነጋገር ስማቸው የተጠቀሱ ሰዎች ጠቅላይ ሚንሰትር ከሆኑ ሊኖረው የሚችለውን ጥቅም እና ጉዳት እንደሚከተለው ተንትነን አስቀመጥን።

ሀ. አባዱላ ገመዳ፣ ከፍተኛ የፓለቲካ ብስለት ያለው እና ሽግግሩን ለመምራት ከሁሉም የተሻለ ዝግጅት ቢኖረውም በአመራርነት ላይ ለረጅም ጊዜ ሰለቆየ እና ለሰፊ ፕሮፓጋንዳ ስለተጋለጠ በሕዝቡ ዘንድ እንደ ለውጥ መሪ (change agent) ተቀባይነት ሊያገኝ አይችልም።

ለ. ወርቅነህ ገበየሁ፡ ሰዎችን እና የፖለቲካ ፓርቲዎችን አስተባብሮ ለመምራት የሚያስችል ሰብዕና እንዲሁም ረዘም ያለ የአመራር ልምድ ሰላለው ሽግግሩን መምራት ያስችለዋል። ነገርግን እሱም ነባር አመራር ስለሆነ እንደ አዲስ አመራር ሕዝቡ እንዲቀበለው ማድረግ ይከብደናል።
ሐ. ዐቢይ አሕመድ (የአሁኑ ጠ/ሚኒስትር)፣ ከዚህ በፊት ብዙም የማይታወቅ እና አዲሰ ፊት መሆኑ 'የለውጥ መሪ' አድርጎ ማቅረቡ ሕዝቡን ለመሳብ ይጠቅማል። በዕድሜ

ከሌሎቹ ወጣት መሆኑ በቄሮዎች ዘንድ ተቀባይነት እንዲኖረው ያደርጋል፣ ነገር ግን በቅርብ ብቅ ያለ ሰለሆነ ችሎታው፣ ባሕርይው እና አመለካከቱ አይታወቅም። ችሎታው እና አመለካከቱ በተጨባጭ ሥራ ላልተፈተነ ሰው ውስብሰቡን የፖለቲካ ሽግግር ኃላፊነት መስጠት ከፍተኛ አደጋ (risk) ሊኖረው ይችላል።

መ. ለማ መገርሳ፣ አመራርነት ውስጥ በመቆየት ጥሩ ልምድ አካብቷል, ትዕግሥት እና ብስለትም እንዲሁ ታድሏል። በንግግሩ እና ተክለ ስብዕናው የሀገር መሪነት ግርማ ሞገስ ይታይበታል። ወደ ፕሬዝዳንትነት የመጣው በቅርቡ ሰለሆነ በፕሮፓጋንዳ አልተጠቃም።

ወደ ሥልጣን ከመጣ በኋላም ለቄሮ ትግል አለኝታነቱን በግልጽ በማሳየቱ በሕዝቡ ዘንድ ተቀባይነት እንዲያገኝ አስችሎታል። የፖለቲካ አቋሙ ለዘብተኛ (moderate) ስለሆነ ሌሎች ብሔሮችን ለመሳብ ይረዳል።

ድክመቶቹ የማደራጀት ችሎታ እና በቆራጥነት መወሰን አለመቻል ናቸው። ሆኖም እነዚህን ክፍተቶች መዝጋት በሚችሉ ሰዎች በመክበብ ሽግግሩን እንዲያሳካ ማድረግ ይቻላል። ስለዚህ ለማ የሽግግር ጊዜ ጠቅላይ ሚኒሰትር ቢሆን ይሻላል የሚል ነበር።

ግምገማችንንም ከሀገርቤት ለመጣው ሰው ስነግረው፣«እናንተ ያላችሁት እውነት ቢሆን እንኳን ለማ የፓርላማ አባል ሰላልሆነ እኛ ብናጨውም ጠቅላይ ሚኒሰትር ማድረግ አይቻልም› አለኝ። ይህ ችግር ሊሆን እንደማይችል አስረዳሁት። «ደብረጽዮን የትግራይ ክልል ምክር ቤት አባል ሳይሆን ምክትል ፕሬዚዳንት ሆኖ ከተሾመ በኋላ የፕሬዝዳንትነቱን ሥልጣን እንደተረከበው ሁሉ፣ እኛም ለማን ለጊዜው ምክትል ጠቅላይ ሚኒሰትር አድርገን ሾመን፤ ከፈለግን ሙሉ ጠቅላይ ሚኒሰትር ለማድረግ የማሟያ ምርጫ (by-election) በአጭር ጊዜ ውስጥ ማካሄድ እንችላለን። ወይም የሽግግር አመራር ለሁለት ዓመት ብቻ ስለሆነ በምክትል ጠቅላይ ሚኒሰትር ደረጃ ቢመራም ችግር የለውም። ዋናው ነገር እናንተ ተግባቡ እንጂ ለማን ይቅርና፣ ማንኛውም እናንተ የተስማማችሁበትን እጩ ጠቅላይ ሚኒስትር ከማድረግ የሚያስቆማችሁ አይኖርም አልኩት፡ ለማደፋፈር አስቤ።

ንግግሬ ባይዋጥለትም ሐሳቤን ግን በግልጽ አልተቃወመም። በለማ ጉዳይ መከራከሩን አቁሞ ዐቢይ አሕመድ ጥሩ ምርጫ ሊሆን እንደሚችል ሊያሳምነኝ ሞከረ። ይህ ሰው ለውጥ የሚፈልግ ጎበዝ ወጣት መሆኑን፣ የጀርባ ታሪኩ ከሠራዊት እና ከስለላ ዘርፍ ሰለሆነ የሕወሓትን ሴራ ለመበጣጠስ እሱ እንደሚሻል ነገረን። በተጨማሪም ከልጅነቱ ጀምሮ እንደሚያውቀው እና በችሎታው ላይ እምነት እንዳለው አከለበት። በበኩሌ እስከእዚያ ጊዜ ድረስ ስለ ዐቢይ አሕመድ ያለኝ መረጃ ውስን ስለነበር የሰውዬውን ምስክርነት መቀበልም አለመቀበልም አልተቻለኝም ነገር ግን ውስብስብ በሆነ ሀገር ውሰጥ ከዚህ ቀደም በፖለቲካ አመራር ልምድ የሌለውን ሰው መሾም ትልቅ አደጋ ሊኖረው ይችላል በማለት ጥርጣሬዬን ደግሜ ለማስረዳት ሞከርኩ። በመጨረሻም ሀገር ቤት ሲመለስ ከእኔ የሰማውን ሐሳብ ለአመራሮች አቅርቦ መልሳቸውን እንደሚነግረኝ ቃል ገብቶ፡ «‹እሰከዚያው ዐቢይ ወደ አሜሪካ ሲመጣ ተነጋገሩና ለራስህ መገምገም ትችላለህ› ብሎኝ የወቅቱን ውይይታችንን ቋጨን።

ከሳምንታት በኋላ ዐቢይ አሕመድ ወደ አሜሪካ ሲመጣ በአካል ባንገናኝም ለሁለት ሳምንታት

በተደጋጋሚ ተደዋውለን በብዙ ጉዳዮች ላይ ተወያየን። የፖለቲካ አመለካከቱን ለመረዳት የተለያዩ አጀንዳዎችን እያነሳሁ አወራሁት፤ ስለቀጣዩ ጠቅላይ ሚኒስትር ጉዳይ ሳነሳለት እርሱ መሆን እንዳለበት ያለ ምንም ጥርጥር ነገረኝ።

በኢትዮጵያ የፖለቲካ ባሕል ውስጥ አንድ ሰው የሥልጣን ፍላጎቱን እንደዚህ በግልጽ መናገር ስለሌለ አስገረመኝ፤ ግልጽነቱን ወደድኩት። ነገር ግን የፖለቲካ አመራር ልምድ ማጣቱ ከእንዲህ ዓይነቱ ከፍተኛ የሥልጣን ምኞት (ambition) ጋር ተደምሮ ምን ሊያመጣ ይችላል ብዬ ማሰብ ጀመርኩ።

ወደ ዴሞክራሲ የሚደረግን ሽግግር ለማሳካት የአመራር ሚና ትልቅ ድርሻ ስላለው፣ ለረጅም ጊዜ በጉዳዩ ላይ ሳነብ እና ካስተማሩኝ ፕሮፌሰሮች ጋር ደጋግሜ ስወያይበት ነበር። ለሽግግር ጊዜ የሚሆን መሪ ሊያሟላቸው ከሚገባቸው መስፈርቶች ውስጥ በዴሞክራሲያዊ ሥርዓት አስፈላጊነት ወጥ አቋም መኖር፣ በቡድን የመሥራት ፍላጎት እና ችሎታ፣ ብዝኃነትን የማስተናገድ ፍላጎት/ልምድ እና ሀገራዊ ምልከታ የመሳሰሉት ይገኙበታል።

ከዐቢይ ጋር ባደረኩት ውይይት እና ከሌሎች ምንጮች ባሰባሰብኩት መረጃ ላይ ተመስርቼ ከላይ ከተዘረዘሩት መስፈርቶች አንጻር በዝርዝር ገመገምኩት። የግምገማውን ሪፖርትም አዘጋጅቼ አስቀድሞ ባዋራኝ ሰው በኩል ለተወሰኑ የኦሕዴድ አመራሮች እንዲደርስ ላኩኝ። የሪፖርቱ ጭብጥ የዐቢይን ጠንካራ እና ደካማ ጎን በመዘርዘር፣ አሁን ባለበት ደረጃ ዐቢይን የሽግግር ጊዜ ጠቅላይ ሚኒስትር ማድረግ ትክክል አለመሆኑን ያስቀምጣል።

ጥንካሬዎቹ የሥራ ተነሳሽነት እና የመፈጸም አቅም ያለው መሆኑ፣ ለውጥ ለማምጣት ያለው ትልቅ ፍላጎት (ambition) እና ተናግሮ የማሳመን ችሎታ ናቸው። ድክመቶቹ በቂ የመደበኛ ትምህርት እጦት፣ የፖለቲካ አመራር ልምድ ማነስ ናቸው። እነዚህ ሁለት ጉድለቶች፣ የኢትዮጵያንም ሆነ የዓለምን ታሪካዊ እና ወቅታዊ ውስብስብ የፖለቲካ ሁኔታ ላይ ጠለቅ ያለ ግንዛቤ እንዳይቀስም አግደውታል።

በተጨማሪም የሽግግር ወቅት ፖለቲካን ለመገንዘብ እና ለመምራት የሚያስችል ከንባብ ወይም ከልምድ የሚገኝ እውቀት ያንሰዋል። ከዚህ ባሻገር በኦሮሞ ብሔርተኝነት ላይ የግንዛቤ ጉድለት እና ወጣ ያለ የአመለካከት ልዩነት ስላለው፣ ከኦሮሞ ቄሮዎች እና የፖለቲካ ድርጅቶች ጋር ተቃርኖ ውስጥ በመግባት ሽግግሩን ለማሳካት የሚያስፈገውን ዘላቂ ድጋፍ ለማግኘት ያዳግተዋል።

ሥልጣን ይዞ ለውጥ ለማምጣት ያለው የጋለ ፍላጎት ከትምህርት ዝግጅት እና ካለው ልምድ ጋር ስለማይመጣጠን፣ እንዲሁም መካከለኛ እርከን ላይ ያለ ወታደራዊ መኮንን (junior officer) ስለሆነ የፖለቲካ ችግሮችን ከፖለቲካዊ ብልኃት ይልቅ በጉልበት መፍታት ሊመርጥ ይችላል። ይህ ወይ አዲስ አምባገነናዊ ሥርዓት ይወልዳል፣ አለበለዚያም ሀገሪቱን ወደ እርስ በእርስ ጦርነት ይመራታል።

ዐቢይ አህመድ ወደ ሀገር ቤት ሲመለስ ከኤርፖርት ደውሎ ጠቅላይ ሚኒስትሩ ማን ይሁን የሚለውን ሐሳብ ከምን እንዳደረስኩት ጠየቀኝ። «አሁን ለማ መገርሳን ጠቅላይ ሚኒስትር ብታደርጉትና አንተ የእሱ ጽ/ቤት ኃላፊ (Chief of Staff) ብትሆን ይሻላል። ላንተም ለሀገርም ጥሩ የሚሆነው ለሁለት ዓመት እሱን እያገዝክና ልምድ እያካበትክ ምርጫ

ሲደረግ ጠቅላይ ሚኒስትር ብትሆን ነው» አልኩት። «ለምን ናቅከኝ?» አለኝ። «አይ አንተን አልናቅኩህም። ትልቅ አቅም አለህ፤ ልምድ ግን ይጎድልሃል። እንደ እኔ እና አንተ የጋለ አቅም ያላቸው ነገር ግን ልምድ የሚጎድላቸው ሰዎች የሽግግር ፖለቲካን ለመምራት ይቸገራሉ። ሽግግር ትዕግሥት እና የተረጋጋ አመራር ይጠይቃል። ትዕግሥት እና እርጋታ ደግሞ ከዕድሜ እና ከልምድ ጋር የሚመጣ ነው» ብዬ ላሳምነው ሞከርኩ። እሱ ግን በእኔ ሐሳብ ደስተኛ እንዳልሆነ ግልጽ ነበር። ደግሜ እንዳስብበት ነግሮኝ ወደፊትም ውይይታችንን እንደምንቀጥል ተሰማምተን ስልኩን ዘጋን።

ከዚህ ጊዜ በኋላ በፊት የሚያናግሩኝ የኦሕዴድ ሰዎች ጠፉ። ድሮ በምንገናኝበት መንገዶች ሁሉ ብሞክርም አልተሳካም፤ ለሪፖርቴም ምንም ምላሽ አልመጣም። ከጥቂት ሳምንታት በኋላ አንድ ባለሥልጣን ደውሎልኝ ያቀረብኩት ሐሳብ ተቀባይነት እንዳላገኘና ምርጫቸው ዐቢይ እንደሆነ ነገረኝ። እኔም እንድደግፈው ሲመክረኝ የእኔ አቋም ያው መሆኑን ነገርኩት። ነገር ግን በወቅቱ በአደባባይ ወጥቼ ከመናገር ተቆጡብኩ።

ኃይለማርያም ሥልጣን እንደሚለቅ እና አዲስ ጠቅላይ ሚኒስትር እንደሚሾም በይፋ መወራት ሲጀምር ሽግግሩን መምራት ያለበት ለማ መገርሳ እንደሆነ በፌስቡክ እና በOMN በኩል በግልጽ መናገር ጀመርኩ። በወቅቱ ዐቢይ አሕመድ የኦሕዴድ ሊቀመንበር ሆኖ ለጠቅላይ ሚኒስትር እጩነት እንዲቀርብ ብዙ የኦሕዴድ ሰዎችን የማሳመን ሥራ እየሠራ እንደነበር በማወቁ ጠቅላይ ሚኒስትር የመሆን ዕድሉ በጣም ሰፊ እንደሆነ አምኜ ነበር። ተቃውሞዬን ለሕዝብ ያቀረብኩት ያንን ውሳኔ ለማስቀየር ሳይሆን ነገ ሊመጣ ከሚችል ችግር አስቀድሜ ለማስጠንቀቅ እና አቋሜን በታሪክ ማኅደር ለማስፈር ነበር።

የካቲት 2010 ዓ.ም የኦሕዴድ ማዕከላዊ ኮሚቴ ዐቢይ አሕመድን ሊቀመንበር አድርጎ ከሾመ በኋላ ለማ መገርሳ ያለውን ዕድል ለዐቢይ ማሰረከቡ የራሱ ውሳኔ እንደሆነ በግልጽ ተናገረ። ከዚህ በኋላ ብዙ ሰዎች በዐቢይ አሕመድ ላይ የማነሳውን ተቃውሞ እንዳቆም መከሩኝ። ከሰሜን አሜሪካ የተውጣጡ የሀገር ሽማግሌዎች ሚኒሶታ ባለው ቢሮዬ መጥተው፣ «ምንም ቢሆን ኦሮሞ ነው፤ ከወያኔ የከፋ አይደለም። እርስ በእርስ ተጠላልፈን ይህንን ዕድል እንዳናባክን። ተው።" በማለት ተማጸኑኝ። ከሀገር ውስጥም አርቲስቶች፣ ባለሀብቶች እና የሀገር ሽማግሌዎች ተቃውሞዬን እንዳቆም ሌት ተቀን እየደወሉ ወተወቱኝ።

ውስጥ ውስጡን ደግሞ ሀሜት እና የስም ማጥፋት ዘመቻው ተዛመተ። «ጀዋር ለራሱ ጠቅላይ ሚኒስትር መሆን ስለፈለገ በቅናት ዐቢይ አሕመድን ተቃወመ» ብለው የሚያስቡም አልጠፉም። እንዲያውም ከወያኔ ጋር ተባብሬ እሱ ላይ እንደምዘምት ሀሜት ተናፈሰ። እውነታው አንዳንድ የሕወሓት ሰዎች መጀመሪያ ላይ ከለማ መገርሳ ይልቅ ዐቢይ አሕመድ ይሻላል የሚል አቋም ነበራቸው። ምናልባትም መንበሩን ይቆናጠጣል ብለው ስላልገመቱ ይሆናል። የእኔ ተቃውሞ ግን ከግል ጉዳይ ጋር ምንም ግንኙነት አልነበረውም። አንዳንድ የሕወሓት ባለሥልጣናት ዐቢይ አሕመድ ላይ ያነሳሁትን ተቃውሞ ለስልት ያደረኩት በማስመሰል በጥርጣሬ እያዩት እንደነበር ወደ አገር ከገባሁ በኋላ ነግረውኛል። ጥርጣሬያቸውን ያጠናከረው ደግሞ ተቃውሞ እየመራሁ በነበረበት ወቅት የዐቢይ አሕመድን ስም የሚያጠለሹ መረጃዎች እየላኩልኝ ቢቆዩም በሚዲያ አለማስተላለፈ ነበር።

ከለማ መገርሳም ሆነ ከዐቢይ አሕመድ ጋር የግል ጓደኝነትም ሆነ ፁብ አልነበረኝም። የእኔ

ትችት እና አስተያየት ከእሱ ጋር ተነጋግሬ እንዲሁም ከሌሎች ምንጮች ባሰበሰብኩት መረጃ ላይ በመመርኮዝ ባደረኩት ግምገማ ላይ የተመሠረተ ነበር። አሜሪካ መጥቶ ከተመለሰ በኋላም ጥርጣሬዬን ያባባሱ ሁለት ነገሮችን ፈጸመ። አንደኛው፣ ዐቢይ አሕመድ አሜሪካ በመጣ ጊዜ ራሱን ጨምሮ አባዱላ እና ሌሎች ባለሥልጣናት ከበቀለ ገርባ ጋር ለተከሰሱ የፖለቲካ እስረኞች የመከላከያ ምስክር ሆነው ፍርድ ቤት እንደሚቀርቡ ቃል ገብቶልኝ ነበር። ይህንኑ ለማቀላጠፍ የእስረኞቹ ጠበቃ ከነበረው አብዱልጀባር ሁሴን ጋር አገናኝቼ አውርተው ተግባቡ፤ የቀጠሮው ቀን ሲደርስ ግን ቀሩ።

ሌላኛው ደግሞ፣ የካቲት 2009 ዓ.ም ሁለተኛው ኮማንድ ፖስት ሲታወጅ አብዛኛው የኦሕዴድ የፓርላማ አባላት በድፍረት የተቃውሞ ድምፅ ሲሰጡ ዐቢይ አሕመድ በምክር ቤቱ ስብሰባ ላይ ሳይገኝ ቀረ። ድምፅ ከመስጠት የቀረበት ምክንያት ሕወሓትን በማስቆጣት ጠቅላይ ሚኒስትር የመሆን ዕድሉን እንዳያጣ በማሰብ እንደሆነ ገባኝ። ያሳዘነኝ ለራሱ ብቻ በመቅረት አልተወሰነም፤ እሱ እና ከእሱ ጋር የነበሩ ሰዎች የፓርላማ አባላቱ አዋጁን እንዲደግፉ ለማሳመን መሞከራቸው ነው። ይህ ድርጊት ምናልባት ጠቅላይ ሚኒስትር ሲሆንም ልክ እንደበፊቱ በኮማንድ ፖስት ሀገር ለማሥተዳደር አስቦ ይሆናል ብዬ አሰብኩ። ገና በማለዳው በአስቸኳይ ጊዜ አዋጅ ማሥተዳደር የመረጠ መሪ አዲስ አምባገነን የመሆን ፍላጎት እንዳለው ጠቋሚ ስለሆነ የዐቢይ አሕመድ አመራር ላይ ቀድሞ ያለኝ ጥርጣሬ እንዲጠናከር አደረገ።

በአጠቃላይ የዐቢይ አሕመድን መሾም የተቃወምኩት ሽግግሩን ለመምራት የሚመች ልምድ እና ባሕርይ የለውም ብዬ ሰለደመደምኩ፤ የሃምሳ ዓመታት የኦሮሞ ሕዝብ መሥዋዕትነት እና ኢትዮጵያን ወደ ዴሞክራሲ ለማሻገር የተገኘው ዕድል ይባክናል ብዬ ስለሠጋሁ ነበር። ለእርሱ እንደነገርኩት፣ ሐሳቤ ለማን እና ገዱን ሽግግሩን እንዲመሩ በመሾም ዐቢይ አሕመድ እና የተቀሩት ወጣቶች ለእነርሱ አጋር ሆነው ከሽግግሩ ማግስት በሚደረግ ምርጫ ወደፊት ቢመጡ ይሻላል የሚል ነው።

ሆኖም አብዛኛው ሕዝብ የእኔን አቋም ስላልደገፈ የዐቢይ አሕመድ ወደ ሥልጣን መምጣት የፓርቲው ፍላጎት ብቻ ሳይሆን የሕዝቡም እንደሆነ ተረዳሁ። ሕዝቡ ብቻም ሳይሆን፣ ዛሬ «ጠ/ሚኒስትር ዐቢይን አንተ ነህ ያመጣሁብን» እያሉ የሚረግሙኝ፤ በአገር ውስጥ እና በውጪ የነበሩ የተቃዋሚ ፓርቲ መሪዎችም ተቃውሞዬን እንዳቆም ግፊት አድርገውብኛል። በመጨረሻም «ፈጣሪ የእኔን ሥጋት ስሕተት አድርጎ፣ የእናንተን ተስፋ እውነት ያድርገው!» ብዬ ፌስቡክ ላይ ለጥፌ ተቃውሞዬን ገታሁ።

በአንድ በኩል የዐቢይ አካሄድ ገና ከጠዋቱ የነበረኝን ሥጋት እውን እያደረገ ሲሄድ፣ በሌላ በኩል ደግሞ በተቃውሞ መቀጠል ከሕዝቡ እያጋጨኝ ስለሆነ: ከዚህ በላይ በፖለቲካው መቀጠል ለኔም ሆነ ለትግሉ ጉዳት እንጂ ጥቅም እንደሌለው በመገመት፣ ከቀጥተኛ የፖለቲካ ተሳትፎ እራሴን ማግለል እንደሚሻል ደመደምኩ። 32ኛ ዓመት ልደቴን ያከበርኩ ዕለት ይህንኑ በፌሰቡክ ለጠፍኩ። ድሮውንም ቢሆን ትግሉን ካጠናቀኩኝ በኋላ፣ በፖለቲካው የመቀጠል ሳይሆን ወደ ትምህርት የመመለስ ዓላማ ነበረኝ።

ነገር ግን ከፖለቲካ እንደምገለል ሳሳውቅ የመንግሥት ሰዎችን ጨምሮ የተለያዩ የማኅበርሰብ ክፍሎች የኔ በተሳትፎ መቀጠል ለሽግግሩ መቀጠል አስፈላጊ መሆኑን በመግለጽ፣ ውሳኔዬን እንድቀይር ተመጸኑኝ። በተለይ በወቅቱ ለውጡ የመቀልበስ (counter revolution)

አደጋ ሊያጋጥመው እንደሚችል ሥጋታቸውን በመግለጽ፣ እንደ ማስረጃም በዛ ሰሞን በግብጽ ጦሩ ያደረገውን መፈንቅለ መንግሥት፣ እንዲሁም እኔው እራሴ ስለ ለውጥ ቅልበሳ የጻፍኩትን34 በመጥቀስ፣ ተሳትፎዬን እንድቀጥል ወተወቱኝ። እኔም ተስማማሁ።

ኢሕአደግ ከአሥራ ሰባት ቀናት ስብሰባ በኋላ ዐቢይ አሕመድን ሊቀመንበር አድርጎ ሾመ ቀጥሎም ጠቅላይ ሚኒስትር አድርገው ሰየሙት። እኔም «ወንድሜ፣ እንኳን ደስ አለህ። ሀገርን ወደ ዴሞክራሲ የሚያሻግር ሰው ያድርግህ» በማለት መረቅኩት። እሱም በጽሑፍ መልዕክት አመስግኖኝ «ያለፈው አልፏል። ከዚህ በኋላ የትግሉን ዓላማዎች ከግብ ለማድረስ በጋራ እንሠራለን» አለኝ።

ጠ/ሚኒስትር ዐቢይ አሕመድ ሥልጣን ይዞ ከሁለት ወራት በኋላ ሰኔ 16 ቀን 2010 ዓ.ም ለውጡን የሚደግፍ ሰልፍ መስቀል አደባባይ ተጠራ፤ በሰልፉም ላይ በምብ ተወረወረ። መጀመሪያ ላይ ቦምቡን የወረወረው ለውጡን ለመቀልበስ ያሰበ የሕወሓት አንጃ ይሆናል የሚል ጥርጣሬ ነበረኝ። ቦምቡ ተወርውሮ በጥቂት ደቂቃዎች ውስጥ ግን አንድ ቄሮ ቦምቡን የወረወረው ሰው አጠገቡ ቆሞ እንደነበርና አፋን ኦሮሞ እንደሚናገር በፌስቡክ ጠቆመኝ።

ይህን መረጃ ለፕሮፌሰር ሕዝቅኤል ገቢሳ ነግሬው ከተወያየን በኋላ፣ ልክ እኛ መጀመሪያ እንደጠረጠርነው ዐቢይም በምቡን የወረወረው ሕወሓት መስሎት በስሕተት እርምጃ እንዳይወስድ መረጃው እንዲደርሰው ተስማማን። በዚሁ መሠረት በወቅቱ አጠገቡ ለነበረ ሰው ደውዬ መረጃውን ሰጥቼው በአስቸኳይ ለጠ/ሚኒስትር ዐቢይ እንዲደርሰው ነገርኩት።

ዐቢይ ግን በቴሌቪዥን ቀርቦ ለጥቃቱ ሕወሓትን ተጠያቂ የሚያደርግ መግለጫ ሰጠ። መግለጫው ውስጥ "የቀን ጅቦች" የሚለውን ቃል መጠቀሙ ከሕወሓትም አልፎ የትግራይን ሕዝብ በጅምላ እንደፈረጀ ተደርጎ ስለተተረጎመ በጠ/ሚኒስትሩ እና በሕወሓት መካከል የነበረውን መቃቃር አባባሰው።

ዐቢይ ሥልጣን ከተቆናጠጠ ከአራት ወራት በኋላ ሐምሌ 2010 ዓ.ም ወደ አሜሪካ እንደሚመጣ በወቅቱ የውጭ ጉዳይ ሚኒስትር በነበረው በዶ/ር ወርቅነህ ገበየሁ በኩል ሰማሁ። ጥርጣሬዬን እና ተቃውሞዬን ወደ ጎን ትቼ ሕዝቡ ለእርሱ አቀባበል እንዲዘጋጅ ለመርዳት ወሰንኩ።

የጠቅላይ ሚኒስትሩ ልዑካን ሊመጣ ሁለት ቀናት ሲቀረው ከሀገር ቤት የመጡ አምስት ባለሀብቶችን ያቀፈ የሽማግሌዎች ቡድን ሊያናግሩኝ እንደሚፈልጉ ነገሩኝ። ሽማግሌዎቹ ወይዘሮ መኪያ ማሚዩ፣ ከቢር ሑሴን፣ ሐጂ ባቲ ዋቲዬ፣ ሐጂ ሂኮ ቱራ እና አለማየሁ ከተማ 14

ምናልባት ዐቢይ ሲመረጥ ስለተቃወምኩት ተቀይሟል ብለው በማሰብ ሊያስታርቁን ፈልገው የመጡ መሰለኝ። ያረፉበት ሆቴል ሄጄ ሳነጋግራቸው ለደኅንነቴ ስለሚሰጉ ወደ ሀገር ቤት እንዳልገባ ሊያሳምኑኝ በራሳቸው ተነሳሽነት እንደመጡ ነገሩኝ። አጥብቄ ስጠይቃቸው ግን መንግሥት ወደ ሀገር እንዳልገባ ሊያሳምነኝ እንደላካቸው ተረዳሁ። እነዐቢይ በሥልጣን

34 በግብጽ የተከሰተው ጸረ ለውጥ እርምጃ በኢትዮጵያ እንዳይደገም የሚል ረዘም ያለ ጽሑፍ Karaan kun Morsitti nu geessaa laata? በሚል ርዕስ በአላን ኦሮሞ አዘጋጅቼ ኤፕሪል 27, 2018 https://www.facebook.com/search/posts/?q=masri%20jawar%20 mohammed%20counter%20revolution

ጉዳይ በእኔ ላይ ሥጋት እንዳላቸው ቀድሞውንም አውቅ ነበር። ሥልጣን እንደማልፈልግ በተለያዩ ሰዎች ለማሳመን ብሞክርም ስላልተሳካ፤ በ32ኛ ዓመት የልደት ቀኔ ከፖለቲካ ጡረታ መውጣት እንዳሰብኩ በፌስቡክ እስከመለጠፍ ብሄድም ሊያሳምናቸው አልቻለም። ስለዚህ ሽማግሌዎቹ ብዙ እንዲናገሩ አልፈቀድኩላቸውም። መመለሴ ሊሻር የማይችል የመጨረሻ ውሳኔ እንደሆነ አስረግጬ ነገርኳቸው።

ከቁርስ በኋላ ሌሎቹን እዚያው ትቼ አለማየሁ ከተማን ይዤ ወደ ቢሮዬ ሄድን። አለማየሁን ለይቼ የወሰድኩት ለነዐቢይ ስለሚቀርብ የእኔ መመለስ ጉዳይ በሽምግልና ከሚሆን ቀጥታ እንዲነግረው ነበር።

ዞር ዞር እያለ የOMN ስቱዲዮ ሲጎበኝ ወለሉ ላይ አንድ ፍራሽ አይቶ ምን እንደሆነ ሲጠይቅ ጋዜጠኞቹ ላለፉት አራት ዓመታት ማደሪያዬ እንደነበር ሲነግሩት ቁጭ ብሎ ስቅስቅ ብሎ አለቀሰ። መኝታዋ ለወትሮ የተጎዳን ሰው ለመሸከም የምታገለግል ቃሬዛ ነበረች፤ አሮጌ እቃዎች ከሚሸጡበት ሱቅ የወሰድኳት የምትተጣጠፍ ስለሆነችና ቢሮ ውስጥ ለመተኛት ስለምትመች ነው። ይህ ቦታ ከባለ አምስት ኮከብ ሆቴል አልጋ የበለጠ ምቹ ነው ብዬው መኝታዋ ላይ ተጋድሜ እየቀለድኩ አበረታታሁት። ቡና አፍልተን እየጠጣን ሳለ መመለሴ ለምን እንዳስፈለገ ካስረዳሁት በኋላ፣ ለጠ/ሚኒስትር ዐቢይ እና ለለማ ገልፆ እንደሚያሳምናቸው ተስማማን።

በተጨማሪም ከሕወሓት ጋር እየተፈጠረ የነበረውን ቅራኔ በአስቸኳይ የመፍታት አስፈላጊነት ላይ ተወያይተን፤ ወዲያው ለዶ/ር ደብረጽዮን ገብረሚካኤል ደውሉ አገናኘኝ። ከደብረጽዮን ጋር ሰላምታ ከተለዋወጥን በኋላ በተቃውሞ ወቅት ኮምፒዩተሩን በመጥለፍ (hack) እና የግል ምስጢሩን በማጋለጣችን ይቅርታ ጠየቅኩት። እሱም «የልብህን ካደረስክ በኋላ ይቅርታ ትጠይቀኛለህ አይደል?» ብሎ ቀለደብኝ።

ያለፈውን ትተን ስለ ነገው ለመወያየት ተስማምተን፣ የብሔራዊ እርቅ አስፈላጊነት እና ይህንን ሽግግር በጋራ መምራት ላይ አጽንዖት ሰጥቼ አወራሁት። ይህንን ችግር ለመቅረፍ ወደ መቀሌ ሄጄ ከአመራሩ እና ከሕዝቡ ጋር መነጋገር እንደምፈልግ ነገርኩት። እሱም ለዚህ ዓላማ እንድሄድ ፈቃደኛ መሆናቸውን አስረዳኝ። በዚህም መሠረት ሀገር ቤት እንደደርስኩ የምሄድበትን ቀን ለመወሰን ተስማማን።

ጠ/ሚኒስትር ዐቢይ እና የቡድኑ አባላት ዋሽንግተን ዲሲ እና ሎስ አንጀለስ ሕዝቡን አነጋግረው ወደ ሚኒሶታ ሲመጡ፣ ከኮሚኒቲ መሪዎች ጋር አየር ማረፊያ ሄደን ተቀበልናቸው። ሆቴል እንደደረሰን ከለማ ጋር አንድ ክፍል ገብተን እየተወያየን ሳለ ዐቢይ እና ወርቅነህ ተቀላቀሉን። አስፈላጊ እና አስቸኳይ ናቸው ብዬ ያሰብኳቸውን ጉዳዮች ለውይይት አቀረብኩ።

የመጀመሪያው በትጥቅ ትግል ውስጥ የነበሩ ድርጅቶች ወደ ሀገር ተመልሰው የለውጡ አካል በሚሆኑበት ጠቀሜታ ላይ ነበር።

እንደ ኦሮሞ ነጻነት ግንባር (ኦነግ)፣ የኦጋዴን ብሔራዊ ነጻነት ግንባር (ኦብነግ) እና አርበኞች ግንቦት ሰባት ካሉ ድርጅቶች ጋር እርቅ ወርዶ ወደ ሰላማዊ ትግሉ እንዲገቡ ሁኔታዎችን ማመቻቸት ለሽግግሩ ስኬት አስፈላጊ እንደሆነ በአጽንዖት ተናገርኩ።

ስለዚህ እነዚህን ድርጅቶች በፍጥነት አነጋግረው እና አስማምተው ወደ ሀገር እንዲያስገቡ ሐሳብ ሳቀርብ እነሱም ሐሳቤን እንደሚጋሩ ገለጹ።

ሁለተኛው የተወያየንበት ጉዳይ ከሕወሓት ጋር የተፈጠረውን ቅራኔ በአስቸኳይ የመፍታት እና ወደ መቀሌ የሸሹትን አመራሮች አስተማማኝ ዋስትና ሰጥቶ የመመለስ አስፈላጊነት ላይ ነበር። ኢኮኖሚውን እና የጸጥታ መዋቅሩን ለረጅም ጊዜ የተቆጣጠረ ኃይል ከሥልጣን ሲባረር በብልኃት ካልተያዘ ሀገሪቱን ወደ ከባድ ጦርነት ሊያስገባት እንደሚችል ገለጽኩ። ዐቢይ ግን ሕወሓት ጃጅቶ የተሸነፈ በመሆኑ ሥጋቴ መሠረተ ቢስ እንደሆነና ጉዳዩ በኢሕአዴግ ውስጥ እንደሚፈታ ተናግሮ ከዚያ ያለፈ እንዳልናገር በሩን ዘጋ።

በመጨረሻ ስለ ምርጫ ሳነሳ፣ «ከሁለት ዓመት በኋላ ስለሚመጣ ምርጫ ለምን ትጨነቃለህ?» ብሎ በግርምት ተመለከተኝ። ወደ ዴሞክራሲ የሚደረግ ሽግግር እንዲሳካ ከተፈለገ የመጀመርያው ምርጫ ወሳኝ እንደሆነና ለዚህም አስቀድሞ መዘጋጀት አስፈላጊ መሆኑን ተናገርኩ። ጠ/ሚኒስትር ዐቢይ ለዚህ አትጨነቅ፤ ዶክተሮችን በመቶዎች አሰልፈን የትኛውንም ፓርቲ በቀላሉ ማሸነፍ እንችላለን» አለኝ። እኔ ግን «እንዲህ ቀላል አይሆንም። የተጋጋለ ብሔርተኝነት በሰፈነበት የሽግግር ፖለቲካ ውስጥ፣ አይደለም ሰው አህዮችን ዓርማ እና ባንዲራ አልብሶ በማቅረብ የናንተን ዶክተሮች ማሸነፍ ይቻላል» ብዬ አፌዝኩበት። ጉዳዩን ከመጤፍ እንዳልቆጠረው ስላየሁ አለፍኩት።

ከዚህ ውይይት ዐቢይ በጉዳዮች ላይ ጠለቅ ያለ ውይይት ለማካሄድ ዝግጁ እንዳልሆነ በደምብ ተረዳሁ። በሦስቱ (ጠ/ሚኒስትር ዐቢይ፣ ለማ እና ወርቅነህ) መካከል ያለው ግንኙነት ከውጪ እንደሚታየው ፍቅር በፍቅር እንዳልሆነም ስለታዘብኩ፤ አብረው ሩቅ መጓዝ እንደማይችሉና ይህም ለሽግግሩ ውስጣዊ እንቅፋት እንደሚፈጥር በመረዳቴ ጭንቀቴ ጨመረ።

ከውይይታችን በኋላ ሕዝቡ ተሰብስቦ ወደሚጠብቀን ስታዲየም ሄድን። ስንደርስ ስታዲየሙ ሙሉ ነበር። ከሚውለበለቡ ባንዲራዎች አንጻር አብዛኛው ታዳሚ ኦሮሞ ቢሆንም፣ የተለያዩ ብሔረሰቦች እንዳሉም ይታያል። መድረክ ላይ የነበርን ሰዎች በተቻለ መጠን አንድነትን በማሳየት የሕዝቡን ደስታ ለማጠናከር ጥረት አደረግን። እውነቱን ለመናገር በጊዜው የተደበላለቀ ስሜት ውስጥ ነበርኩ። በአንድ በኩል ኦሮሞ ከሃምሳ ዓመታት ትግል በኋላ ልጆቹ ወደ ሥልጣን ስለመጡ ከጭቆና ተገላገልኩ ብሎ በደስታ ስሜት ግልብጥ ብሎ ወጥቶ ስታዲየሙን በእልልታ ሲያደበላልቀው ማየቴ አስደሰተኝ። በሌላ በኩል መጀመሪያ ከነበረኝ ጥርጣሬ በተጨማሪ ጠዋት ባደረግነው ውይይት በዐቢይ ላይ ባየሁት ባሕርይ እና አስተሳሰብ ለውጡ ሊደናቀፍ እንደሚችል የበለጠ ስለተረዳሁ፤ ወደፊት ይህ ሕዝብ ለሞራል ስብራት ሊዳረግ እንደሚችል ሳስብ አዘንኩ። ሀዘኔን በውስጤ አምቄ በማግስቱ ልዑካኑን ከሸኘን በኋላ ለውጡን ለማሳካት እና በተቻለኝ ሁሉ ለመሞከር ወደ ሀገር ቤት ለመመለስ ተዘጋጀሁ።

# ትውስታ በምስል #3



OMN ስቱዲዮ ሥራ በማስጀመር ዝግጅት ላይ ከኤሊያስ ኢብሳ፣ ሙሐመድ አብዶሽ እና ግርማ ታደሰ ጋር። ፈረንጇ የቴክኒካል ሥራ እንድትረዳን የቀጠርናት ነበረች።



ከOMN ኤዲተር ፉዓድ ሲራጅ ጋር ፕሮግራሞችን እያቀናበርን።




የOMN በተከፈተበት እለት ከአመራሮቹ ጋር ዶ/ር ሰንታየሁ፣ ዶ/ር በዳኔ፣ ዶ/ር ሀምዛ አብዱረዛቅ፣ ራሚ መሀመድ፣ አቢ ኢቲቻ፣ ግርማ ታደሰ፣ ሌይላ አባዋሪ እና አብዱል



በOMN ሲተላለፍ በነበረው የራባ ዶሪ ፕሮግራም ላይ ከዶ/ር ሄኖክ ገቢሳ፣ ዶ/ር ብረሃኑ ሌንጂሶ እና የፕሮግራሙ መሪ ዶ/ር ግርማ ጉተማ ጋር ፖለቲካን ስንተነትን



የOMN የመዓዘን ድንጋይ ከሆኑት ኤሊያስ ኢብሳ እና ሙሐመድ አብዶሽ ጋር። ሁሌ አብረን ስንሰራ ያየን አንድ ሰው "The Three Amigos" የሚል መጠሪያ ሰጠን።



የ OMN ዋና ዳሬክተር በመሆን ሚዲያውን ፈር ካስያዘው ድር ብረሃኑ ዲርባባ ጋር ከድል በኋል ፊንፊኔ ላይ ተገናኘን።



በትግሉ ወቅት ለረጅም ጊዜ ኮምፒዩተር ላይ አቀርቅሬ ስለምቆይ የነርቭ ዕክል ገጥሞኝ
የቀኝ ጎኔ ፓራላይዝድ ሆኖ ሆስፒታል ገብቼም ሥራ ማቆም አልቻልኩም ነበር።



ለአራት ዓመታት ያህል በOMN ቢሮ ስተኛባት የነበረችው "አልጋዬ"
ፕሮፌሰር ሕዝቅኤል ለሥራ መጥቶ ከጎኔ ወንበሮችን ገጣጥሞ ተኛ።



ትንሽ ጊዜ ሲገኝ ከልጄ ኦሮሞ ጋር ስሄድ
ከኮምፒተሯ ጋር ሲሻማኝ።



ጃዊ (ሐሰን ዩሱፍ) በትግሉ ወቅት በበጎ ፈቃደኝነት
ቦዲ ጋርድ፣ ሹፌር እና ረዳቴ በመሆን አንድም ቀን
ያልተለየኝ።




የቄሮ ትግል ፍቃዱ ሹመታ የተባለ ልጅ መፈክር ሲያሰማ የተነሳው ፎቶ የማስተር ፕላኑ ተቃውሞ ዋነኛ ምስል ሆኖ ነበር።





በምዕራብ ሸዋ ባቢቻ ላይ ቄሮዎች እስከ አፍንጫው ታጥቆ ሰልፍ ሊበትን የመጣውን የአጋዚ ጦር ባዶ እጃቸውን ሲጋፈጡ።



በሀረርጌ አንዲት ሴት ተቃውሞዋን አስፈራርተው ለማስቆም የሞከሩ ወታደሮችን ያለፍራቻ ስትጋፈጥ።



የገበያ እቀባ ሲታወጅ ሱቆች ሙሉ በሙሉ ይዘጉ ነበር።



ቄሮዎች መንገድ በመዝጋት ላይ ሳሉ ተነስተው የሚልኩትን ፎቶ፣ ፌስቡክ ላይ ከመለጠፌ በፊት፣ ማንነታቸው ታውቆ ለአደጋ እንዳይጋለጡ ፊታቸውን እሸፍን ነበር።




ለታላቁ ሰልፍ ዝግጅት ወቅት አንድ ቄሮ የሰልፉን እለት (August 6) በክንዱ ላይ ጽፎት።



ገመዳ ዋሪዮ የተባለ ወጣት በኢሬቻው የተቃውሞ እለት "Down Down Woyane!" በማለት መፈክር ሲያሰማ።



በወቅቱ እናቴ ልትጠይቀን መጥታ ነበርና ጸጉር መላጨት እምነቴ አይፈቅድም በማለት የተቃውሞ ምልክቱን ፎቶ እንስቼ እንድለጥፍ ጠየቀችኝ።



በትግሉ ወቅት በቀለ ገርባ እና ሌሎች የፖለቲካ እስረኞች ጸጉራችንን በመላጨት ለተሰዉ ታጋዮች ሀዘን እንድናሳይ ባዘዙን መሠረት እኔም ተላጨሁ።





በትግሉ ወቅት ከወጣቶቹ ጋር ተቀላቅለው ሲቃወሙ የነበሩ እናት ወደ ሀገር ተመልሼ አገኘኋቸው።

Jawar Mohammed
February 15, 2018

BREAKING: Ethiopia's prime minister submits resignation, the state affiliated Fana reports.

FBC (Fana Broadcasting Corporate S.C.)
6 mins

#Breaking

ሰበር ዜና

ጠቅላይ ሚኒስትር ኃይለማርያም ደሳለኝ የስራ መልቀቂያ አስገቡ



ጠ/ሚ ኃይለማርያም ደሳለኝ ሥልጣናቸውን መልቀቃቸውን በፌቡስክ ያበሰርኩበት።



በሚኒሶታው የአቀባበል ዝግጅት ላይ ንግግር እንዳደርግ ጠ/ሚ ዐቢይ ሲጋብዘኝ እጄን በማጣመር ድሉ የቄሮ ትግል ውጤት መሆኑን ስገልጽ።



"የለውጡ አመራሮች" ወደ ሚኒሶታ የመጡ እለት ከኤርፖርት ተቀብዬ ወደ ሆቴል ስንሄድ።



ከዶ/ር ወርቅነህ፣ ዝናሽ (የዐቢይ ባለቤት)፣ ጠ/ሚ ዐቢይ እና ፕሬዝዳንት ለማ ጋር በሚኔሶታው መድረክ ላይ።

# ክፍል ስምንት - ለውጡን የማዳን ሙከራ

## 8.1. *ጉዞ ወደ ሀገር ቤት*

ለትምህርት ወደ ውጭ ከሄድኩበት ጊዜ አንስቶ አንድ ቀን ወደ ሀገር ቤት ተመልሼ ሕዝቤን የማገልገል ተሰፋ ነበረኝ። ውጭ ሀገር ስለመኖር አስቤ አላውቅም። በሚዲያ መንግሥትን በመንቀፍ በግልጽ መጻፍ እና መናገር አስከጀመርኩበት ጊዜ ድረስ ትምህርታዊ ጥናት ለማድረግ በየዓመቱ ወደ ሀገር ቤት እመላለስ ነበር። በኋላ ላይ ከሀገር ስወጣ የተቀበልኩት የኢትዮጵያ ፓስፖርት ጊዜው ስላለፈ ለማሳደስ ለኤምባሲው ማመልከቻ ሳስገባ በአካል እንድሄድ ተጠየኩ። ሌሎች ሰዎች አስፈለጊውን ቅጽ ሞልተው በፖሰታ በመላክ ፓሰፓርታቸውን ማሳደስ እንደሚችሉ ስለማውቅ፣ እኔም ልክ እንደሌሎቹ አስፈላጊውን ነገር በፖስታ ከላኩ በኋላ ወደ ኤምባሲው በአካል ካልመጣህ ማለታቸው ጥርጥሬ ውሰጥ ከተተኝ። ጠበቃዬን ሳማክረው ኤምባሲ የኢትዮጵያ ሉዓላዊ (sovereign) መሬት ሰለሆነ መንግሥት ችግር ሊፈጥርብኝ እንደሚችል ነገረኝ። ከዚያም መሄዱን ትቼ የአሜሪካ ፓሰፖርት ማውጣቱ ላይ አተኮርኩ። በቀጣዮቹ ዓመታት በመንግሥት ላይ ያደረኩት የተቃውሞ አንቅሰቃሴ ስለጨመረ ወደ ሀገር የመግባት ዕድሌም በዚያው ልክ አየራቀ ሄደ።

በመንግስት ውስጥ ያሉ፣ ከመንግስት ውጭ ያሉ እና የቄሮ ትግል ተሰክቶ ለውጥ ሲመጣ ወደ ሀገር ቤት የመግባት ፍላጎቴ ዳግም ተቀሰቀሰ። ወደ ሀገር ለመግባት የወሰንኩት በሦስት ዋና ዋና ምክንያቶች ነበር። የመጀመሪያው በመራራ ትግል አና በታላቅ መሥዋዕትነት ለውጥ ያመጡትን ቄሮዎች አና ሕዝቡን ለማመስገን ሲሆን፣ በሁለተኛ ደረጃ እንደ እኔ ያሉ ሰዎች ወደ ሀገር መግባታቸዉ ለለውጡ ትዕምርታዊ ጠቀሜታ (symbolical benefit) ሰላለው ነው። በስደት ለረጅም ጊዜ የቆዩ ተቃዋሚዎች እና አንቂዎች ወደ ሀገር መመለሳቸው የስደት ምዕራፍ መዘጋቱን ያመለክታል። ይሀ ደግሞ እንደ ሕዝብም ሆነ እንደ ሀገር ለሚደረግ እርቅ የሞራል ሰንቅ ይሆናል። ሦስተኛው ከለውጡ መንግስት ጋር ተግባብቼ ለመስራት ለሽግግሩ ሰኬት የበኩሌን አስተዋጽኦ ለማበርከት ነው። ከዚሀ በመነሳት ወደ ሀገር ለመግባት መወሰኔን በሰኔ ወር 2010 ዓ.ም መጨረሻ አካባቢ ለሕዝብ ይፋ አደረግኩ።

ወደ ሀገር ቤት የመግባት ሐሳቤ አንደታወቀ ከተለያዩ የኅብረተሰብ ክፍሎች ተቃውሞ ገጠመኝ። ለመመለስ መወሰኔን ባሳወቅኩበት ወቅት ሽግግሩ ወዴት እንደሚያመራ ገና ግልጽ ሰላልነበር፤ የብዙ ሰዎች ተቃውሞ ለደኅንነቴ በመሥጋት ነበር። በትግሉ ወቅት ስንፋለማቸው የነበሩ አብዛኞቹ የህወሓት አመራሮች ጸድተው አልወጡም ነበር። አዲሶቹ አመራሮች በብዙ ችግሮች የተከበቡ ስለነበር የስልጣን ምደባ ላይ እና ስልጣናቸውን ለማጽናት ስለሚተጉ የደህንነት ጉዳይ አሳሳቢ ነበር ።

ህወሓትን ከስልጣን ለማውረድ ባደረግነው ትግል ለበቀል ያነሳሳቸው ይሆናል የሚለ ጥረጣሬም ነበር። በዚሀ ሥጋት የተነሳ ሐሳቤን እንድቀይር ሀገር ቤት ያሉ ሰዎች በስልክ አና በፌስቡክ ዘመቻ ከፈቱ። አንዳንዶቹ ወደ አናቴ እና ወደሚያውቁኝ ሰዎች ሄደው ሐሳቤን አንዲያሰቀይሩኝ ተማጸኑ። በውጪም የሀገር ሽማግሌዎች ከተለያዩ ግዛቶች ሚኒሶታ ድረስ በመምጣት አንዳልገባ ሊያሳምኑኝ ሞከሩ። አኔ ግን ወደ ሀገር መግባት የሚያስከትለውን ጉዳት እና ጥቅም አመዛዝኜ ውጪ ከመቆየት መግባቱ አንደሚሻል ወስኜ በአቋሜ ጸናሁ።

ከላይ አንደገለጽኩት፣ የመንግሥት ባለሥልጣናት አንዳልመለስ ከአገር ውሰጥ ሽማግሌዎችን የላኩት ለደኅንነቴ በመስጋት አንደሆነ ቢገልጹም፣ አውነታው ግን ሥልጣን አንዳልቀማቸው ሰግተው አንደሆነ ግልጽ ነበር። ወደ ሚኒሶታ ሲመጡ ሥልጣን አንደማልፈልግ በመንገር ጥርጣረያቸውን ለማስወገድ ሞክራያለሁ። ጠ/ሚኒስትር ዐቢይ «ሰትመለስ ምን ለማድረግ አሰበኸል? ምን እናድርግልህ?›› ብሎ ሲጠይቁኝ ገብቼ ሚዲያ ማቋቋም ለዛ የሚያስፈልገው በጀት እገዛ ከዚያም አልፎ የመንግስት ሃላፊነት ተሰጥቶኝ ማገዝ አንደምፈልግ ነገርኩት። «ቤት እና መኪና ይሰጠው» እንዲሁም ለግሌ ጥበቃ እንዲመደብልኝ ለለማ እና ለወርቅነህ ትእዛዝ አስተላለፈ።

ወደ ሀገር ቤት ለመመልስ እንደወሰንኩ ባልደረቦቹ ሙሐመድ አብዶሽ አና ኤሊያስ ኢብሳ OMNን በፊንፊኔ ለማቋቋም ቀደም ብለው ወደ ሀገር ቤት በመሄድ፤ በጥቂት ሳምንታት ውሰጥ ፈቃድ አውጥተው ሰራተኞች ቀጥረው እና ሰቱዲዮ ገንብተው ስርጭት አሰጀመሩ። ወደ ሀገር ቤት የምገባበት ቀን ኦገስት 3 ቀን 2018 (ሐምሌ 29/2010 ዓ.ም) እንዲሆን ወስነው አሳወቁኝ። ወዳጆቼ የሆኑት ተመስገን በሪሶ አና ሚሊዮን ቤለማም ከአሜሪካ ሄደው እነ ሙሐመድ አብዶሽን ተቀላቀሏቸው። ከሀገር ቤትም ሰው በመጨመር የአቀባበል ኮሚቴ አቋቁመው ሁኔታዎችን ወደ ማመቻቸት ገቡ። ከሚኒሶታ ሥነሳ፣ ሽማግሌዎች ወደ OMN ቢሮ መጥተው በእንባ ታጅበው መረቁኝ። እነዚያ ሽማግሌዎች አንደ አባት የምቆጥራቸው እና አሜሪካ ከሄድኩ ጀምሮ ሲያበረታቱኝ የነበሩ አንጋፋ ታጋዮች ሲሆኑ፣ በቁሮ ትግል ሰኬት ደስተኛ ቢሆኑም ትቼያቸው በመሄዴ ግን አዘኑ፡ እኔም አንጀቴ ተላወሰ። በሚኒሶታ ኤርፖርት አርፋሴን አና ልጄ ኦሮሞን በእንባ ተሰናብቼ ጉዞዬን ጀመርኩ።

በማግስቱ ዋሽንግተን ዲሲ አድረን ፕሮፌሰር ሕዝቅኤል ገቢሳን ጨምሮ ከሃምሳ ሰዎች ጋር በኢትዮጵያ አየር መንገድ ወደ ፊንፊኔ አቀናን። ፊንፊኔ ሰንደርስ የሀይማኖት አባቶች እና የሀገር ሽማግሌዎች እናቴን አጅበው በሌ ኤርፖርት መጥተው ተቀበሉኝ። በወቅቱ የገቢዎች ሚኒሰትር የነበሩት ወ/ሮ አዳነች አቤቤ፣ የፌደራል ፖሊስ ኮሚሽነር ዘይኑ ጀማል አና ሌሎች

ባለሥልጣናት አቀባበሉ ላይ ነበሩ። ከአውሮፕላን ማረፊያ ወደ ኢሊሊ ሆቴል ስንሄድ የመንገዱ ዳር እና ዳር የትግል ዓርማ አንግበው በተሰለፉ በሺህ የሚቆጠሩ ቄሮዎች ተሞልቷል። ፊታቸው ላይ ያለውን ደስታ ስመለከት ከአጠገባቸው የተሰዉትን ወጣቶች አስታውስኼ ውስጤ ተረበሸ። ኢሊሊ ሆቴል ትንሽ አረፍ ካልን በኋላ ወደ ሚሊኒየም አዳራሽ ሄድን፤ እዚያ ስንደርስ አዳራሹን ሞልቶ ሲጠብቀን ከነበረው ሕዝብ በተጨማሪ ለማ መገርሳ፣ አዳነች አቤቤ፣ ታከለ ኡማ፣ጠይባ ሀሰን እና ሌሎችም የመንግሥት ባለሥልጣናት ነበሩ። አባገዳዎች እና የሀይማኖት አባቶችም ተገኝተዋል። እናቴ እና የጠ/ሚኒሰትር ዐቢይ አሕመድ አባትም እዚያው ነበሩ።

ለማ መገርሳ ባደረገው የእንኳን ደህና መጣህ ንግግር ውስጥ ለመጣው ለውጥ የቄሮን ትግል በማመስገን የእኔን ድርሻ አወደሰ። ሕዝቡም በከፍተኛ ሰሜት ተቀበለው። ቀጥሎ እኔ እንድናገር ተጋበዝኩ። ላለፉት አራት ዓመታት ከኦህዴድ ሰዎች እና ከቄሮዎች ጋር ስሰራ ብቆይም፤ በአካል መካከላቸው ስገኝ የመጀመሪያዬ ነበር። ንግግሬ ያተኮረው የኦሮሞ ብሔርተኝነት ታሪክ ከተቃውሞ ፖለቲካ (resistance politics) ወደ አሥተዳደር ፖለቲካ (governance politics) መሸጋገር አለበት በሚለው ሐሳብ ላይ ነበር።

ይህ የታሪክ ሽግግር ለረጅም ጊዜ ሲያሳስበኝ የቆየ ጉዳይ ነው። የብሔር ትግል የፖለቲካ ሥልጣን ሲቆናጠጥ ትርክት (narrative) መቀየር ግድ ይላል። ትግል በሚካሄድበት ወቅት በምንታገልለት ሕዝብ እና በሀገረ-መንግሥቱ መካከል ያለው ግንኙነት የጠላትነት ስለሚሆን፤ ትግሉ አገዛዙን ቀይሮ መንግሥታዊ ሥልጣን ሲይዝ ግን ግንኙነቱን የተጎዳውን በመካስ የትምክህተኞችን ትርክት በመናድ ከጠላትነት ወደ ወዳጅነት መቀየር ያስፈልጋል።

ሥልጣን ከያዙ በኋላ በተቃውሞ ትርክት መቀጠል ውስጣዊ ተቃርኖን በመፍጠር በመሥዋዕትነት የመጣውን ለውጥ ለአደጋ ያጋልጣል። ስለዚህ በአንድነት አና በስልት አምባገነኑን ሥርዓት ያዳከመውን የኦሮሞ ወጣት በገዢነት ወደ ዴሞክራሲ እና የልማት ኃይል ለማሸጋገር፤ አመለካከቱ ከተቃውሞ ፖለቲካ ወደ አሥተዳደር ፖለቲካ መቀየር አለበት።

ይህን ጉዳይ የሚያብራራ ሰፊ ንግግር አደረኩ። የኦሮሞ ወጣት ሰከን ብሎ ስልጣኑን እንዲያስጠብቅ ለለውጡ አመራር ጊዜ እንዲሰጥ ተማጸንኩ። በአማርኛ ባደርኩት ንግግር ደግሞ የኢትዮጵያ ሕዝቦች አሁን የተገኘውን ዕድል በብልኃት በመጠቀም ሀገራቸውን ወደ ዴሞክራሲ እንዲያሸጋግሩ ጥሪ አቀረብኩ።

ንግግሬን አንደጨረሰኩ የቄሮ እንቅሰቃሴ ከተጀመረበት ጊዜ አንስቶ ስጠቀምበት የነበረውን ኮምፒዩተር አባ ገዳ በየነ ሰንበቶ ለለማ መገርሳ እንዲያበረክቱልኝ ጠየኳቸው። በቄሮ ትግል ውሰጥ ማኅበራዊ ሚዲያ ከፍተኛ ሚና ስለነበረው፤ የዚህ ትግል መሣሪያ ምልክት የነበረውን ኮምፒዩተር ለመንግሥት መስጠት፡ከእሁን በኋላ በወጣቱ አና በመንግሥት መካከል መተባባር እና ማገዝ እንዳለበት አሳሰብኩ። እንደ ግለሰብም ወደ ሀገር የገባሁበት ዓላማ መንግሥትን ለመተባበር አንጂ ለመታገል አለመሆኑን በመጠቆም እነዐቢይ ያላቸውን ጥርጣሬ ለማቃለል በማሰብ ነበር።

ለማ መገርሳ መንግሥትን ወክሎ ኮምፒዩተሩን አንዲቀበል የመረጥኩት የኦሕዴድን ድርጅት እና ቄሮን በማቀራረብ ረገድ ለተጫወተው ሚና ለማመስገን እና እውቅና ለመሰጠት ሰለፈለኩኝ ነው። ኮምፒዩተሩን ከእኔ ተቀብለው ለለማ እንዲሰጡ አባ ገዳ በየነ ሰንበቶን በሁለት ምክንያቶች ነበር የመረጥኩት። የመጀመሪያው ገዳ አንደተቋም (institution)

ትልቅ ክብር ስለሚገባው ሲሆን፤ ሁለተኛው አባ ገዳ በየነ ሰንበቶ ለቄሮ ትግል ስኬት በግላቸው ላበረከቱት አስተዋጽኦ የሚገባቸውን እውቅና ለመስጠት ነው። አባ ገዳ በየነ ኮምፒዩተሩን ከእኔ ተቀብለው ለለማ ሲሰጡት አዳራሹ በታላቅ ስሜት በጭብጨባ እና በፉጨት ማጀቡ፣ ቄሮ እና ሕዝቡ የመሪዎቹን አንድነት ለማየት ምን ያህል ጉጉት እንደነበራቸው ያመለከተ ነው።

በማግስቱ ወደ አምቦ አመራን። በትግሉ ወቅት የአምቦ ቄሮ እና ማኅበረሰብ ማንኛውንም ዘመቻ ስናውጅ በቀዳሚነት ወደ ተግባር በመለወጥ ለሌላው አካባቢ ሞራል ይሆኑ ስለነበር፤ አንድ ቀን በዚሁ በጣም ተደስቼ ድል የተጎናጸፍን ዕለት አምቦ ውስጥ በባዶ እግሬ በመዳዝ እንደማመሰግናቸው ቃል ገባሁ። ወደ ሀገር ቤት እንደምገባ ሳሳውቅ የአምቦ ቄሮዎች በባዶ እግር ጎዳናቸው ላይ ለመራመድ የገባሁትን ቃል አስታወሱኝ። ስለዚህ ወደ ሀገር በገባሁ ማግስት አምቦ መሄድ ግዴታ ሆነ። ኅዳር 2 ቀን 2008 ዓ.ም ሁለተኛው ዙር አመጽ ወደ ተቀሰቀሰባት ጊንጪ ጎራ ብለን ሰማዕት ለሆኑ ቄሮዎች የመሠረት ድንጋይ አስቀምጠን፡ ሕዝቡንም አነጋግረን አለፍን።

አምቦ ስንደርስ ሀጫሉ ሁንዴሳ ከእኔ ቀድሞ ደርሶ ስለነበር፤ መንገድ ላይ ተቀብሎኝ ጓደኛው የነበረው አለማየሁ ገርባ በተሰዋበት የአምቦ ሁለተኛ ደረጃ ትምህርት ቤት ፊትለፊት ችግኝ እንድተክል ጋበዘኝ። አለማየሁ ገርባ በ2006 በተካሄደው የተማሪዎች ተቃውሞ የተገደለ ሲሆን፣ በኋላ ለመጣው የቄሮ ትግል ትልቅ አርአያ ነበር። ከመኪናው ወርጄ ጫማዬን አውልቄ፣ ከሀጫሉ ጋር እጅ ለእጅ ተያይዘን በተዘጋጀው ጉድጓድ ውስጥ የመታሰቢያ ችግኝ ተክለን ወደ አምቦ ስታዲየም ስናመራ ከአምቦ እና አካባቢው የተውጣጡ በሺዎች የሚቆጠሩ ሰዎች ሜዳውን ሞልተው ተቀበሉን። ዝግጅቱ በአምቦ ዩኒቨርሲቲ ፕሬዝዳንት ዶ/ር ታደሠ ቀነዓ እና በአምቦ ቄሮዎች የተዘጋጀ ነበር። በወቅቱ የኦሮሚያ ፖሊስ ኃላፊ የነበሩት ኮሚሽነር ደቻሳ ቢቲማ እና ምክትሉ ኮማንደር በቀለ መገርሳ ከፊንፊኔ አጅበውን መጡ። የኦሮሚያ ፖሊስ ከቄሮ ትግል ጎን እንዲሰለፍ ትልቅ ሚና በመጫወታቸው፤ ከእነዚህ አዛዦች ጋር ወደ አምቦ መሄዳችን ትልቅ ክብር ነበር።

የአምቦ ፕሮግራም ከተጠናቀቀ በኋላ ወደ ቀጣዩ ከተማ ጉደር ስናመራ ከፌደራል ባለሥልጣናት ለኮሚሽነር ደቻሳ ተደውሎ ለሕይወቴ የሚያሰጋ መረጃ እንዳለና የጉደሩ አቀባበል ላይ እንዳንሳተፍ ተነገረው። በፕሮፌሰር ሕዝቅኤል ገቢሳ የሚመራ አንድ የልዑካን ቡድን እንዲሄድ አድርገን፤ እኛ ዞረን ወደ ፊንፊኔ ተመለስን።

በሚቀጥለው ቀን ወደ ሻሸመኔ አቀናን። አዚያ ስንደርስ ከአካባቢው ዞኖች የተጓዘ በሚሊዮን የሚቆጠር ሕዝብ ተሰብስቦ ጠበቀን። የተዘጋጀው ስታዲየም ያን ሁሉ ሕዝብ ማስተናገድ አልቻለም፤ ይባስ ብሎ የተከፈተው አንድ የመግቢያ እና መውጫ በር ብቻ ነበር። ይህም ሕዝቡ እርስ በእርስ እንዲገፋፋ እና እንዲረጋገጥ ሰላደረገው፤በተወሰኑ ደጋፊዎችና ተቃዋሚዎች መካከል በተነሳ ግጭት የሰዎች ሕይወትማለፍ ጀመረ። ስታዲየም ገብተን በተዘጋጀልን ቦታ ከተቀመጥን በኋላ፤ ምርቃት ተከናውኖ ቆሜ መናገር ስጀምር ሕዝቡ እየተጋፋ ወደ ፊት መምጣት በመጀመሩ ማይክራፎኑ ድምጼን እያሰማ እንዳልሆነ አሰተዋልኩ። የባሰ መረጋገጥ ተፈጥሮ ብዙ ጉዳት እንዳይደርስ ንግግሩን አሳጥሬ ዝግጅቱን በፍጥነት አጠናቀን ወጣን።

በአውሮፕላን ወደ ፊንፊኔ ለመመለስ ሐዋሳ ሰንደርሰ፣ እኛ ከወጣን በኋላ "በጀዋር ላይ ቦምብ ተወረወረ" የሚል ወሬ በመናፈሱ ሻሸመኔ ላይ የብዙ ሰዎች ህይወት እንዳለፈ ለመረዳት ቻልን።

ቀድሞውኑ የሚጠሉኝ ሚዲያዎች ክስተቱን በማራገብ የእኔን ስም የሚያጠፋ ዘመቻ ለረጅም ጊዜ አካሄዱ። ከአደጋው በኋላ በየዞኑ ተጉዘን ሕዝቡን ለማናገር የገባነውን ቃል ለጊዜው እንዲዘገይ አደረግን።

ውሎ አድሮ በሻሸመኔ የተፈጸመው ድርጊት የኦሮሞን ሕዝብ እየዞርኩ እንዳላናግር ጽንፈኛ የሸረበው ሴራ መሆኑን ተረዳሁ። በወቅቱ ጽንፈኛው ከጀርባ ሆኖ በሮችን በመዝጋት እንዲሁም በግፊያው የተነሳ የድምፅ ማጉያው እንዳይሰራ ተደርጓል።

እኔ ከሄድኩ በኋላ የተፈጸመውን ግድያ ለማጣራት በወቅቱ የተቀረጹ ቪዲዮዎችን ስንመለከት፤ የተሰቀለው ሰው የእኔን መምጣት የሚቃወም ጽንፈኛ ቢሆንም የእኔ ደጋፊ እንደገደለው አውቀን ለጸጥታ አካሎች ስናሳውቅ በተደረገው ክትትል ከአጭር ጊዜ በኋላ መኪና ገጭቶ እንደገደለው ሰማን። ይህ ድርጊት በሻሸመኔ የተፈጸመው ሁከት የጽንፈኛው ሤራ ስለመሆኑ የነበረንን ጥርጣሬ ይበልጥ አጠናከረው።

በዚሁ ምክንያት ወደተለያዩ ከተሞች በመጓዝ ሕዝቡን ማነጋገሩን ትቼ ከመንግሥት ባለሥልጣናት ጋር በመነጋገር ፍርሀታቸውን በማርገብ በተቻለ መጠን በሀገር ማረጋጋት እገዛ ላይ ለማተኮር ወሰንኩ። በዚሀም መሠረት በወቅቱ የሀገሪቱ ፕሬዝዳንት በነበሩት ዶ/ር ሙላቱ ተሾመ ተጋብዘን ቤተመንግሥት ሄድን።

ከፕሬዝዳንት ሙለቱ ጋር ባደረግነው ውይይት ትልቅ እውቀት አና ልምድ ያላቸው ሰው መሆናቸውን ተረዳሁ። ሀገሪቱን በማረጋጋት ወደ ዴሞክራሲ ማሸጋገር ያለውን ጠቀሜታ አበክረው ተናገሩ። ከንግግራቸው መሀል የማልረሳው፣ከዚህ በፊት «እዚህ ሀገር ያለው ችግር ሕግ ሲረቀቅም ሆነ አንድ ፓሊሲ ሲወጣ፤ ሥልጣን ላይ ያለውን ሰው ፍላጎት አና አመለካከት ብቻ ያማከለ ነው።

ያ ሰው ሁሉን ዐዋቂ፣ መቼም ከሥልጣን የማይወርድ እና ለዘላለም የሚኖር ተደርጎ ይታሰባል። ነገርግን ሰውዬው ድንገት ከሥልጣን ሲወርድ ወይም ሲሞት የወጡ ሕጎች እና ፖሊሲዎች ዋጋ ያጣሉ። ስለዚሀ እናንተ ይሀንን ለውጥ የመምራት ግዴታ ያለባችሁ ሰዎች በግለሰቦች ፍላጎት እና ምኞት ላይ ከተመሠረተ ፖሊሲ አና ሰትራቴጂ ይልቅ፣ ሀገርን ያማከለ አና ከዘመን ዘመን የሚሻገር ተቋም መንንባት ላይ አተኩሩ›› አሉን። በዚህ ንግግራቸው መለስ ዜናዊ ትዝ አለኝ።

በቀጣይ የወቅቱ የተወካዮች ምክር ቤት አፈ-ጉባዔ ከነበረችው ወይዘሮ ሙፈሪያት ካሚል ጋር ተገናኝተን፤ በደቡብ ክልል ብሔሮች የራሳቸውን ክልል ለመመሥረት እያካሄዱ ባሉት ትግልና ባስከተለው ውጥረት ላይ ተወያየን። የብሔሮችን እራስን የማሥተዳደር መብት እንደምደግፍና በተለይ ለሲዳማ ታጋዮች ቀረቤታ ስላለኝ እንዳግዝ ጠየኳት።

ሕዝቡ ያነሳቸው ጥያቄዎች በሕገ-መንግሥቱ የተረጋገጡ ስለሆኑ ለማፈን ከመሞከር በሕጋዊ አና በሰለማዊ መንገድ መፍታት የተሻለ እንደሆነ ነገርኳት። በእኔ በኩል "ኤጀቶ" (የሲዳማ ወጣቶች ንቅናቄ) ትግላቸውን በትዕግሥት አና በሰላማዊ መንገድ ብቻ እንዲያደርጉ ለመምከር ቃል ገባሁላት።

በቀጣይ ወደ ጠቅላይ ሚኒስትሩ ቤተ-መንግሥት ተጠርቼ ከጠ/ሚኒስትር ዐቢይ አሕመድ፤ ለማ መገርሳ እና ዶ/ር ወርቅነህ ጋር ተገናኝተን ምሳ በላን። እዚያም በሚኒሶታ የተነጋገርናቸውን ጉዳዮች ደግሜ አነሳሁላቸው። በተለይ ከኦነግ ጋር ተነጋግሮ ወደ ሀገር ሰለመመለስ አበክሬ ተናገርኩ። ጠ/ሚኒስትር ዐቢይ ከዚህ ቀደም ወደ አሰመራ ሲሄድ ከኦነግ አመራር ጋር ተገናኝቶ እንዳወራና በወቅቱ ዶ/ር ወርቅነሀ እና ለማ ሄደው ጉዳዩን እንደሚጨርሱ ነገሩኝ። ወደ ትግራይ የመሄድ እቅድ እንዳለኝ አና ከዶ/ር ደብረጽዮን ጋር መነጋገሬንም አሳወኳቸው። ወደ መቀሌ መሄድ አማራን ሊያስከፋ ሰለሚችል መጀመሪያ ወደ ባሕር ዳር ብሄድ የተሻለ አንደሆነ ተወያይተን እኔም ተሰማምቼ ወደዚያው አመራሁ።

በወቅቱ የአማራ ክልል ፕሬዝዳንት ገዱ አንዳርጋቸው ባደረጉልን ግብዣ ወደ ባሕርዳር አቀናን። ስለ አቶ ገዱ ረዘም ላለ ጊዜ መረጃ ሳሰባስብ ሰለቆየሁ፤ በግል የማውቀው ያሀል ይሰማኝ ነበር። አንደኔ ሐሳብ ቢሆንማ፣ ሀገሪቱን ከለማ ጋር ለማሻገር ምክትል ጠቅላይ ሚኒሰትር ሆኖ ይመረጥ ነበር። ይሀን ሰው በአካል አግኝቼ ሰለ ሽግግሩ ስኬት ለማወያየት ትልቅ ምኞት ነበረኝ።

ባሕር ዳር ስንደርስ በወቅቱ የክልሉ የኮሚኒኬሽን ጉዳዮች ኃለፊ የነበሩት አቶ ንጉሱ ጥላሁን አቀባበል አደረጉልን። ንጉሱ፣ በኦሮሚያ ክልል አርሲ የተወለደና አፋን ኦሮሞም የሚናገር ሰለሆነ በኦሮሞ አና በአማራ ብሔሮች መካከል ያለውን ግንኙነት ለማሻሻል በቆራጥነት ሲሰራ ቆይቷል። በቁሮ ትግል ወቅት ሁለቱን ብሔሮች በማጋጨት ትግሉን ለማዳከም የሚደረገውን ጥረት በማክሸፍ ትልቅ ሚና ተጫውቷል። አውሮፐላን ማረፊያ ስንደርስ አቀባበል አድርገውልን ጃኖ አለበሱን። ጃኖ የእኛ ነው? ወይስ የእናንተ ነው? ብለን በቀልድ ተከራክረን፤ 'የጋራ ነው' በሚለው ተሰማምተን ወደተያዘልን ሆቴል አመራን። ምሽት በእራት ግብዣ ላይ ከገዱ ጋር ረጅም ጊዜ ወስደን ተወያየን። ሽግግሩን እያጋጠሙ ያሉ ተግዳሮቶች እና መወጣት የሚቻልበትን ሁኔታ፣ በትግሉ ወቅት ተመስርቶ የነበረውን የኦሮሞ አና የአማራ (ኦሮ-ማራ) ስልታዊ ትብብር (tactical alliance) ወደ ዘላቂ አጋርነት በማሳደግ ሽግግሩን ስኬታማ ማድረግ እንደሚያስፈልግ ተሰማማን።

በአማራ ክልል ሥር የሚተዳደሩት የወሎ ኦሮሞዎችን አንዲሁም በኦሮሚያ የሚኖሩ የአማራ ብሔር ተወላጆችን ደኅንነት እና መብት ማረጋገጥ በሚቻልበት ሁኔታ ላይ መከርን። በወቅቱ እየሻከረ የመጣውን የትግራይ እና የአማራ ክልል ግንኙነት እንዴት ማሻሻል አንደሚቻል ስንወያይ የእኔ ሐሳብ ሕወሓት በቅርቡ ከሥልጣን በመገፋቱ የድንጋጤ እና የፍርሀት ሰሜት ውስጥ ሰለነበረ፤ በዚህ ጊዜ አወዛጋቢ ጉዳዮችን በማንሳት የባሰ ከማስበርገግ ይልቅ አቋምን አለዝቦ ማረጋጋት ያስፈልጋል የሚል ነው። በሁለቱ ክልሎች መካከል ያሉ አጨቃጫቂ የድንበር እና የማንነት ጉዳዮችን በችኮላ ለመፍታት ከመሞከር ይልቅ ቀስ በቀሰ በምክክር መቅረፍ የተሻለ አንደሆነ አጥብቄ ተናገርኩ። ከነበረን ውይይት እና ከሩቅ ባሰባሰብኩት መረጃ እንደተረዳሁት፤ ገዱ ተራማጅ (progressive) የአማራ ብሔርተኛ እና በፌደራሊዝም ሥርዓት ላይ ጥሩ አቋም ያለው መሆኑን ማረጋገጥ ቻልኩ።

በማግስቱ ንጉሱ ጥላሁን የአማራ ወጣቶችን ሰብሰቦ ጋብዘኝ ሰፊ ውይይት አደረግን። ወጣቶቹ በአማራ እና በኦሮሞ የፖለቲካ ኃይሎች መካከል አወዛጋቢ የሆኑ ጉዳዮችን አንስተው ጠየቁኝ። ከአነዚሀም አንዱ የአኖሌ ታሪክ ጉዳይ ይገኝበታል። “አኖሌ ጭፍጨፋ በእውነት የተከሰተ ሳይሆን የአማራን ስም ለማጥፋት የተፈበረከ የሐሰት ታሪክ ነው” የሚል መከራከሪያ አቀረቡ።

እኔም ስለ አኖሌ በተጻፉ ጉዳዮች ላይ ከመጨቃጨቅ ይልቅ እውነቱን ማወቅ ከፈለጉ አርሲ ሄደው በቦታው ያለውን ሕዝብ መጠየቅ እንደሚሻል መከርኳቸው። በኦሮሚያ ስለሚኖሩ የአማራ ተወላጆች መብት እና ደኅንነት ጉዳይ አንስተው ሲጠይቁኝ፣ በኦሮሚያ የሚኖር አማራ እንደ ማንኛውም የኦሮሞ ተወላጅ ሙሉ የዜግነት መብት እንዳለው በማረጋገጥ በሕግ የተቀመጠው መብት እንዲከበር ሁሉም መታገል እንዳለበት ገለጽኩላቸው። በኦሮሚያ ያሉ የአማራ ተወላጆች ልዩ መብት (special privilege) እንዳላቸውም ነገርኳቸው። ይህም በኦሮሚያ ከሦስት መቶ በላይ ትምህርት ቤቶች በአማርኛ እንዲያሰተምሩ መደረጉን አወሳሁ። በኦሮሚያ የሚኖሩ የአማራ ተወላጆች በተደራጀ መልኩ ለመብታቸው መታገል ከፈለጉ በኦሮሚያ ክልል ምክር ቤት (ጨፌ) ውሰጥ የተወሰነ ውክልና እንዲኖራቸው ማድረግ እንደሚቻልም አብራራሁ።

ወጣቶቹ ያነሱት ሌላው ጥያቄ "ኦሕዴድ ልክ እንደ ሕወሓት የአንድ ብሔር የበላይነት የሚንጸባረቅበት አምባገነናዊ አገዛዝ ይመሠርት ይሆን?" የሚል ነበር። ማንኛውም ሥልጣን የጨበጠ ኃይል የሀገሪቷ ዜጎች ገና ከጅምሩ ተባብረው ወጥረው በመያዝ ካላስገደዱት በስተቀር አዲስ አምባገነንነትን ከማንበር አይመለሰም፤ ስለዚህ ሁላችንም በመተባበር ሥልጣን የያዘው ቡድን ወደ ዴሞክራሲ ከሚያሸጋግረው ሃዲድ እንዳይዛነፍ መያዝ አለብን ስል መልስ ሰጠሁ።

ከዚያም ኮሎኔል ደመቀ ዘውዱ እና ባልደረቦቹ ከሚመሩት የ"ወልቃይት ኮሚቴ"ጋር ተገናኘን። ታስረው በነበሩበት ወቅት ድምፅ ስለሆንኳቸው አመሰገኑኝ፤ የኦሮሞ ትግል ለወልቃይት ኮሚቴ እገዛ ሲያደርግ ነበር። በወልቃይት ጥያቄ ላይ ከማንም ባንወግንም ጥያቄያቸውን በሕገ-መንግሥቱ መሠረት በሰላማዊ መንገድ የማቅረብ መብታቸው እንዲከበር ደግፈናል።

በአንድ ወቅት የኮሚቴው አባላት ጥያቄያቸውን ለፌዴረሽን ምክር ቤት ለማቅረብ ወደ ፊንፊኔ እየሄዱ እያለ የፌደራል ደኅንነት ሰዎች ሊያስሯቸው ሲሞክሩ የኦሮሚያ ፖሊስ አድኗቸው ነበር፤ ይህም ያለንን የትግል ትብብር አጠናከረ። በቄሮ ተቃውሞ ወቅት የዚህ ኮሚቴ አመራር በአማራ እና በኦሮሞ መካከል ትብብር እንዲፈጠር ከማንም ቡድን በላይ ሚና ተጫውቷል። በአማራ ክልል ሲደረጉ በነበሩ ሰልፎች ላይ "ኦሮሞ ደም ደሜ ነው፤ የፖለቲካ አስረኞች ይፈቱ" የሚሉ መፈክሮችን አንግበው በመውጣት ለቄሮ ትግል አጋርነታቸውን አሳይተዋል።

ስለዚህ ባሕር ዳር ላይ በተገናኘንበት ወቅት ወደፊት ስለምናደርገው የእርስ በእርስ ትብብርም ሰፊ ውይይት አድርገናል። አሁንም የወልቃይትን ጥያቄ በሕገ-መንግሥቱ እና በሰላማዊ ትግል መጠየቃቸውን እንዲቀጥሉ አደራ አልኩ። ያለውን የለውጥ ሰሜት እንደ አጋጣሚ በመጠቀም ከትግራይ ባለሥልጣናት እና ምሁራን ጋር በውይይት ለመፍታት እንዲሞክሩ ምክር ለገስኳቸው። ወደ ኦሮሚያ መጥተው ከቄሮ አሰተባባሪዎች ጋር እንዲተዋወቁ እና የልምድ ልውውጥ እንዲያደርጉም ጋብዤ ተለያየን።

የክልሉ ሚዲያ የሆነውን የአማራ ክልል ማስሚዲያ ሰቱዲዮን ጎብኝተን፤ ፐሮፌሰር ሕዝቅኤል፣ ዶ/ር ደረጀ ሃዋዝ እና እኔ ቃለ-ምልልስ አድርገናል። በቃለ-ምልልሱ ከአማራ ታጋዮች አና ሕዝብ ጋር ያለንን ግንኙነት የበለጠ የማጠናከርን አስፈላጊነት፤ ሽግግሩ የብሔር ብሔረሰቦችን መብት እና ጥቅም ባስከበረ መልኩ መሄድ እንዳለበት ጠቅለል አድርገን አወራን። ከዚያም ወደ ፊንፊኔ ተመለስን። ከባሕርዳር መልስ ወደመቀሌ ለማቅናት የነበረኝ አቅድ የዐቢይ እና የሕወሓት አመራርን

ይሁንታ ስለሚጠይቅ፣ ይህ እሰኪሟላ ድረስ ተጓተተ። በስተመጨረሻም ለመሄድ ቀን አንደቆረጥኩ፣ ሕወሓት የደህንነት ሹም እና በአስከፊ የሰብዓዊ መብት ጥሰት የሚከሰሰውን ጌታቸው አሰፋን የሥራ አሰፈጻሚ አባል አድርጎ በመምረጡ የጉዞዬን እቅድ መሰረዜን በይፋ ገለጽኩ። ጌታቸው አሰፋ በሥልጣን ላይ በነበረበት ወቅት ከፈጸማቸው በደሎች በተጨማሪ፣ ከሥልጣን ወርዶ መቀሌ ከመሸገ በኋላም ለውጡን ለመቀልበስ ያሴራል በሚል በእነዐቢይ ይወገዝ ነበር። ሕወሓት ይህን እያወቀ ከማሰወገድ ይልቅ አዲስ ሹመት መስጠቱ፣ ለሕዝቸን ስሜት ደንታ እንደሌለው፣ ለእርቀ-ሰላምም ዝግጁ እንዳልሆነ ጠቋሚ ሰለነበርና እኔንም አላሰፈላጊ ፖለቲካዊ ዋጋ ሰለሚያከፍለኝ ያቀድኩትን ጉዞ በመሰረዝ ተቃውሞዬን መግለጽ ፈለኩ።

## 8.2. የሰላም ጥረት ጅማሮ

በቀጣይ በኦሮሞ እና በአጎራባች ብሔሮች መካከል የነበረውን ግጭት መፍታት ላይ አተኮርኩ። በተለይ ከሶማሌ እና ከሐረሪ ጋር የተፈጠረው ቅራኔ እና ግጭት አስቸኳይ ሥራ ይጠይቅ ነበር። ከሶማሌ ክልል ጋር በሺዎች የሚቆጠሩ ንጹሀንን ሕይወት የቀጠፈ የድንበር ግጭት ነበር። ከሐረሪ ጋር ከክልሉ መፈጠር ጀምሮ የነበረው ቅራኔ በሽግግሩ ወቅት ፈንድቶ ከተማዋን ለብጥብጥ አጋልጦ ቆይቷል። ስለዚህ ለእነዚህ ችግሮች መፍትሔ ማፈላለግ ገና ወደ ሀገር ቤት ከመመለሴ በፊት የጀመርኩት ሥራ ነው። በአሜሪካ እና በአውሮፓ ከሚገኙ የሁለቱ ማኅበረሰብ መሪዎች ጋር ተገናኝቼ ቅሬታቸውን በማዳመጥ ነገሩን እንዲያበርዱ ጥረት ሳደርግ ቆይቻለሁ።

በሐረሪ እና በአቅራቢያው ባሉ ኦሮሞዎች መካከል ተከስቶ የነበረው ውጥረት አፋጣኝ መፍትሔ የሚያስዕፈልገው ከባድ ችግር ነበር። ለሐረር ከተማ የሚያገለግል የመጠጥ ውኃ ለከተማዋ አጎራባች ከሆኑ የገጠር ቀበሌዎች ተነስቶ በአርሶ አደሮች ሰፈር አቋርጦ የሚመጣ ሲሆን፣ አርሶ አደሩን ሳይጠቅም ሰለሚያልፍ ትልቅ ቅሬታ ፈጥሯል። እንዲሁም የከተማው ቆሻሻ ተጭኖ በገበሬው የእርሻ መሬት ላይ ይጣላል። ቀደም ሲል ቆሻሻው የሚጣልበት ቦታ ሲመረጥ፤ የቆሻሻው ጥርቅም በሕብረተሰቡ ላይ የጤና እክል በማያደርሰ መልኩ ተቃጥሎ የሚገኘው የኤሌክትሪክ ኃይል ለገበሬው ጥቅም እንደሚውል ቃል ተገብቶ ነበር። በተግባር ግን ቆሻሻው አልተቃጠለም ወይም አልተቀበረም። ክፍት ሜዳ ላይ ተቆልሉ በመበስበስ በሰው፣ በእንሰሳት እና በሰብል ላይ ጉዳት ሲያስከትል ከርሟል።

ከለውጡ በፊት ሕዝቡ በውኃም ሆነ በቆሻሻ ጉዳይ በተለያየ ጊዜ ቅሬታውን ሲያቀርብ ቢቆይም ሰሚ ሊያገኝ አልቻለም። የቄሮ ትግል መንግሥትን እያዳከም ሲመጣ አርሶ አደሮች በማሳቸው ውስጥ የሚያልፈውን የውኃ መሥመር በመቁረጣቸው ከተማዋ ተጠማች።

ቆሻሻ ለመጣል የሚመጡ መኪኖችን በመከልከላቸውም ቆሻሻ በከተማዋ መንገዶች ላይ እየተጣለ የነዋሪዎችን ጤና ለአደጋ አጋለጠ። ከተማዋ በዚህ ዓይነት ችግር ውሰጥ እያለች፣ ሀገርቤት እንደተመለስኩ የሐረሪ ሽማግሌዎች እና ወጣቶች ወደ ፊንፊኔ መጥተው አነጋንሩኝ።

ቅሬታቸውን ካዳመጥኩ በኋላ የአካባቢውን አባ ገዳዎች፣ ቄሮዎች እና የሀይማኖት መሪዎች አስጠርቼ አወያየሁ። ከሁለቱም ቡድኖች ጋር ባደረገነው ውይይት የከተማዋ ችግር አንዱ ምንጭ የክልሉ አመራር በውስጣዊ ሽኩቻ የተነሳ የሕዝቡን ጥያቄ መፍታት አንደተሳነው ተረዳሁ። በአመራሩ መካከል የነበረው ሽኩቻ ሁለት መልክ ነበረው።

ቀዳሚው ክልሉን በጋራ በሚያስተዳድሩት ሁለቱ ፓርቲዎች (ኦሕዴድ እና የሐረሪ ሊግ) ባለሥልጣናት መካከል ያለው ፉክክር (rivalry) ነው። ፕሬዝዳንቱ ከሐረሪ ብሔረሰብ ሲሆን፣ ምክትሉ ኦሮሞ ነው። በየደረጃው ያለው ሥልጣንም እንዲሁ ለሁለት የተከፈለ ሰለነበር፤ በከፍተኛ ባለሥልጣናት መካከል የሚፈጠርን ሽኩቻ እሰከታች በማውረድ አሥተዳደራዊ

ሂደቶችን እና አገልግሎቶችን መስጠት ወደማይቻልበት ደረጃ አሳድጎታል። የባለሥልጣናትን ግላዊ ውዝግብ የብሔር መልክ በማላበስ በሕዝቡ መካከል ብጥብጥ ፈጠሩ። የሐረሪ ሊግ "ክልሉ በሰሜ ሰለተሰየመ የበላይነት ይገባኛል" በሚል ሰሜት ሲንቀሳቀስ፤ የኦሕዴድ ቡድን ደግሞ የሕዝብ ብዛትን ዋቢ በማደረግ የራሱን የበላይነት ይመኛል። አንዳንድ የሕወሓት መሪዎች ይህን ውዝግብ በማባባስ የሐረሪን ቡድን በማስጠጋትና ከኦሮሞ ባለሥልጣናት ጋር በማጋጨት በመሀል የክልሉን ሀብት ይበዘብዙ ነበር። በለውጡ መጀመሪያ ሰሞን ሽኩቻው ተባብሶ የሁለቱ ድርጅት ባለሥልጣናት ውዝግብ ወደ ሕዝቡ ወርዶ ከተማዋን ወደ ሁከት መራት።

ሁለተኛው የሐረሪ ብሔር ባለሥልጣናት መካከል የተፈጠረ ውዝግብ ነው። የሐረሪ ሕዝብ በቁጥር ትንሽ ቢሆንም ብዙ የፓለቲካ አንጃዎች አሉት። እነዚህ አንጃዎች የፓለቲካ ባለሥልጣናትን ብቻ ሳይሆን ባለሀብቶችንም ያሳተፉ ሰለነበሩ፤ በሽግግሩ ወቅት የነበረው ሽኩቻ የክልሉን አሥተዳደር የበለጠ አሽመደመደው። በወቅቱ የክልሉ ፕሬዝዳንት የነበረው ሙራድ አብዱልሀዲ በሕወሓት ድጋፍ ለረጅም ዓመታት በሥልጣን ላይ ሰለቆየ፤ ለውጡ ሲመጣ ወጣት የሐረሪ መሪዎች ሊፈነቅሉት ሞከሩ። ሙራድ በበኩሉ ሥልጣን ለመልቀቅ ፈቃደኛ አልነበረም። ይህ የሥልጣን ሽኩቻ ክልሉ ከአርሶ አደሮች ጋር ያለውን ግጭት እንዳይፈታ አደረገው።

የክልሉን አሥተዳደር ተብትቦ የያዘውን ውሰብሰብ ሽኩቻ ከተረዳሁ በኋላ የመንግሥት ባለሥልጣናትን በማነጋገር መፍትሔ ለማፈለልግ ወሰንኩ። ከፕሬዝዳንት ሙራድ ጋር ባደረግነው ውይይት ሥልጣን ለመልቀቅ ዝግጁ መሆኑን ሲነግረኝ ሐሳቡን ለፌደራል ባለሥልጣናት አካፈልኩ። በገባው ቃል መሠረት ብዙም ሳይቆይ ሥልጣኑን ለኦርዲን በድሪ አሰረከበ። ኦርዲን ሥልጣን እንደያዘ የአርሶ አደሮቹን ቅሬታ ለመፍታት እርምጃ መውሰድ ጀመረ። ከቄሮዎች፣ ከገዳ አባቶች እና ከአርሶ አደር ተወካዮች ጋር ተወያይተን የውኃ መሰመሩ እንዲጠገን እና ቆሻሻውም እንዲወገድ ከሰምምነት ተደረሰ።

ነገሮች ከተረጋጉ በኋላ ከተማዋን እንድጎበኝ እና ሕዝቡንም እንዳወያይ ጋበዙኝ። በሰታዲየም በተካሄደው የአቀባበል ሥነ-ሥርዓት ላይ ፕሬዝዳንት ኦርዲን በድሪን እና የምሥራቅ ሐረርጌ ዞን አሥተዳዳሪዎችን ወደ መድረክ በመጋበዝ እጅ ለእጅ ተያይዘን ለከተማው እና ለአካባቢው ሰላም እና ልማት በአንድነት እንደምንሠራ ቃል ገባን። ወደ ኦርዲን አየጠቆምኩ «ይሀ ሰው እኔን ይመስላል። አባቴ ለደረሰነት መጥቶ እዚሀ አካባቢ ሰለነበር ማን ያውቃል...›› ብዬ በቀልድ መልክ ኦሮሞ እና ሐረሪ በጋራ ላላቸው ቤተሰባዊ ትሰሰር እንደ ምሳሌ አቀረብኩ። ሕዝቡም ከወጣቱ መሪ ጎን በመቆም ለከተማዋ ሰላም አና ልማት አንዲሠራ ተማጸንኩ።

ከዝግጅቱ በኋላ ከሐረሪ ክልል አሥተዳደር አና ከምሥራቅ ሐረርጌ ዞን አመራሮች ጋር ተሰብስበን በሰፋት ተወያየን። በኦሮሞ በኩል ያሉ የሐረሪ ክልል አመራሮች በተለይም ከሩቅ ዞኖች የመጡት፣ በሁለቱ ሕዝቦች መካከል ሰላለው ታሪካዊ አና ማኅበራዊ ውሰብሰብነት (complexity) በቂ ግንዛቤ እንደሌላቸው ሰለተገነዝብኩ ጠለቅ ያለ ውይይት አንድናደርግ ፈለኩኝ።

በሐረሪ በኩል ያሉት ኦሮሞ ወደ ሥልጣን በመምጣቱ የተጋነነ ፍራቻ (exaggerated fear) አላቸው። ኦሮሞ የሐረሪን ክልል አፍርሶ በኦሮሚያ ሥር የመጠቅለል ፍላጎት አለው ብለው ይሠጋሉ። ይሀ የተፈጠረው ከፋፍሎ ለመግዛት እንዲያመች በመሆኑ ሁለቱን የማቃቃር

ሥራ በሰፊው ሲሰራ ቆይቷል።

ሰለዚህ ያንን ጥርጣሬ ለማቅለል መሞከር ነበረብኝ። ከሁለቱም ወገን አመራሮች ጋር ያደረግነውን ዝግ ውይይት ተከትሎ በክልሉ ምክር ቤት አዳራሽ በሁለቱም በኩል ካሉ ማኅበረሰቦች ጋር ግልጽ ውይይት አደረግን።

በውይይቱ ወቅት ወጣቶች አወዛጋቢ ጉዳዮችን በከረረ መልኩ በማንሳት፤ አንዱ ሌላኛው ላይ ጣቱን ይቀስራል። የሀገር ሽማግሌዎች ግን የሁለቱን ማኅበረሰቦች ታሪክ በማውሳት የእርቅ ሐሳብ ሲያቀርቡ ነበር።

ከኦሮሞ ወገን ሲነሱ የነበሩ ጥያቄዎች "በቁጥር እኛ በልጠን ሳለ ለምን በኢኮኖሚ እና በፖለቲካ አድሎ ይደረግብናል?" የሚሉ እና ሌሎችም ናቸው። እንደ አንድ ተጽኖ ፈጣሪ ኦሮሞ፣ ኦሮሞዎችን መገሰጽ እና ሐረሪዎችን ደግሞ ማበርታት ሰላም ለማምጣት አሰፈላጊ ነበር።

ከዚሀ በመነሳት ለተነሱ ጥያቄዎች መልስ ስሰጥ ሦስት ነጥቦችን አጽንዖት ሰጥቼ ተናገርኩ። የመጀመርያው ነጥብ አንድ ተሳታፊ እንደተናገረው የሐረሪ እና የኦሮሞ ሕዝቦች ሁለት የተለያዩ ዘሮች አለመሆናቸውን ነው። ዘር ይቅርና ሁለት የተለያዩ ብሔሮች ለመሆን እንኳን መስፈርት አያሟሉም። የሐረሪ ሕዝብ እና በአካባቢው የሚኖሩ የኦሮሞ ጎሳዎች ለምዕተ-ዓመታት በተደበላለቀ ማኅበራዊ እና ኢኮኖሚያዊ ግንኙነት አብረው በመኖራቸው ለብዙ ትውልዶች ተጋብተው ተቀላቅለዋል። ሐረሪ ሆኖ የኦሮሞ አጎት፣ አክስት ወይም አያት የሌለው የለም። ሰለዚህ አሁን ላይ በከተማዋ የሚኖረው ሁለት የተለያየ ዘር ሳይሆን ድብልቅ ዘር ነው። የሐረሪ ሕዝብ በጋብቻ የመዋሐድ ጠንካራ ባሕል ያለው ነው። ከሐረሪ ተጋብቶ ከተማ የገባ ሰው ቋንቋውን ተምሮ ወዲያው ሐረሪ እንደሚሆን ይታወቃል። ልዩነት ካለ የሚናገሩት ቋንቋ ነው። እንደዚያም ሆኖ የአካባቢው ማኅበረሰብ ሁለቱንም ቋንቋዎች ይናገራል። ሰለዚሀ በሁለቱ መካከል ያለው ግንኙነት የዘመድ አዝማድ ነው።

ሁለተኛው አጽንዖት የሰጠሁት ጉዳይ፣ የሐረር ከተማ የአንድ ወገን ብቻ ሳትሆን እንደ ሶማሌ፣ ኦሮሞ፣ ሐረሪ፣ አፋር ያሉ የምሥራቅ ኢትዮጵያ ሕዝቦች የጋራ ታሪክ ቅርስ መሆኗን ነው።

ሰለዚሀ ይህችን የጋራ ቅርስ መጠበቅ ለሐረሪ ሕዝብ ብቻ የሚተው ሳይሆን የሌሎች ብሔሮች ጭምር መሆኑን መረዳት ያሰፈልጋል። ከተማዋን የሚጎዳ ሁከት እና ብጥብጥ በአካባቢው የሚገኙ ብሔሮችን ሁሉ ታሪካዊ ቅርስ የሚጎዳ ነው።

ሦስተኛው ጉዳይ፣ የሐረር ከተማ ሕዝብ ራሰን በራሰ ማሥተዳደር በመለሰ ዜናዊ ዘመን የተጀመረ ሳይሆን፤ የሐረሪ ሕዝቦች አና በአካባቢው ያሉ የኦሮሞ ጎሳዎች በሰላም አብረው እንዲኖሩ ያሰቻለ ሰምምነት ከብዙ ትውልዶች ጀምሮ ስላለ ነው። የሐረሪ ሕዝብ የሚኖርበት መሬት ሙሉ በሙሉ በኦሮሞ ጎሳዎች ተከበ ሳለ፤ ዳር ድንበሩ ለክፍለ-ዘመናት ተጠብቆ ያለ ግጭት መኖር የቻለው ሁለቱ ብሔሮች በሕግ የተደነገገ ግንኙነት ስላላቸው ነው። ሰምምነቱ የሐረሪ ሕዝብ አሰፋፈር በኦሮሞ ቢከበብም ባሕሉ፣ ቋንቋው አና ራሰን በራስ የማሥተዳደር መብቱ እንዲከበርለት፤ እንዲሁም ከከተማው ውጪ የእርሻ መሬት እንዲያገኝ ያስቻለ ነው። ራባ ዶሪ የሚባለው የአካባቢው ኦሮሞ ጎሳዎች ጦር በከተማዋ ላይ የሚቃጣውን ማንኛውንም ጥቃት የመከላከል ኃላፊነት ነበረበት። ለምሳሌ በ1874 በራኡፍ ፓሻ የሚመራው የግብጽ ጦር

ሐረርን በወረረ ጊዜ የራባ ዶሪ ጦር ለአሥር ዓመታት ተዋግቶ በ1885 ከተማዋን ነጻ ያወጣው በዚህ ሰምምነት መሠረት ነው። በጨለንቆ ጦርነትም የሐረሪው አሚር አብዱላሂ እና የአፍረን ቀሎው በከር ዋሬ የምኒሊክን ወረራ ተባብረው እንደተከላከሉ ታሪክ ያወሳል።

ስለዚህም ሁለቱ ሕዝቦች በሁለት የተለያዩ ነገር ግን ተደጋጋፊ በሆኑ አሥተዳደሮች ሥር መኖራቸው፣ ለብዙ ክፍለ-ዘመናት ከትውልድ ወደ ትውልድ ሲተላለፍ የቆየ እንጂ በቅርቡ መንግሥት የሰጣቸው አይደለም። አካባቢውን በኃይል ለመግዛት የሚፈልጉ ኃይሎች የሁለቱን ሕዝቦች ግንኙነት ለማደፍረስ ቢሞክሩም ያልተሳካላቸውም በዚሀ ዕድሜ ጠገብ ትስስር መነሻነት ነው። ሰለሆነም የዛሬዎቹ የሁለቱ ሕዝቦች መሪዎች ከትላንት አባቶች ብስለት መማር ከቻሉ፤ አንዱ የሌላውን መብት በማክበርና ወደፊት በጋራ ጥቅም ላይ በመተባበር ጠንካራ ልማት እና ሰላምን በአባባቢው ማረጋገጥ አንደሚችሉ ተናገርኩ። ኦርዲን በድሪ እና ከእሱ ጋር ወደ ሥልጣን የመጡ አመራሮች ሕዝቡ ሲያሰማ የነበረውን ችግሮች ለመፍታት በመንቀሳቀሳቸው እየሻከረ የነበረውን የሁለቱን ሕዝቦች ግንኙነት ብዙም ሳይቆይ ማሻሻል ቻሉ። እሰከዛሬም ከተማዋ አንጻራዊ ሰላም ሰፍኖባታል።

## 8.3. የሶማሌ እና የኦሮሞ እርቅ

የሕወሓት አገዛዝ የቄሮን ትግል ለማዳከም ከተጠቀመባቸው ስልቶች አንዱ ኦሮሞን ከአጎራባች ብሔሮች ጋር በማጋጨት የሐሳብ እና የጉልበት መበታተን ለመፍጠር መሞከሩ ነው። በዚሁ ስሌት ኦሮሞ እና ሶማሌን በድንበር ጉዳይ በማጋጨት ከፍተኛ ጉዳት ደርሷል። ከሞያሌ እስከ ቦርዶዴ በተካሄደው ከባድ ጦርነት በሺዎች የሚቆጠሩ ዜጎች ከሁለቱም ወገኖች ተገድለው በሚሊዮኖች የሚቆጠሩ ተፈናቅለዋል።

ሤራውን ያቀነባበሩ ጄኔራሎች በሁለቱ ሕዝቦች ላይ ከፍተኛ ሰብዓዊ እና ኢኮኖሚያዊ ጉዳት ቢያደርሱም ትግሉን ማስቆም ሰላልቻሉ ለውጥ መጣ። በትግሉ ወቅት ከሶማሌ ምሁራን እና አንቂዎች ጋር ግጭቱ እንዳይባባስ በቅንጅት እንሠራ ነበር፤ ከእነሱ ውስጥ አንዱ የአሁኑ የክልሉ ፕሬዝዳንት ሙስጠፋ መሐመድ ነው። ለውጡ እንደመጣ የወቅቱ ፕሬዝዳንት አብዲ ሙሐመድ (አብዲ ኢሌ) ከሥልጣን መወገዱ አይቀሪ በመሆኑ እሱን የሚተካ እጬ ማፈላለግ አሰፈላጊ ሰለነበር፤ ወደ በድብቅ ናይሮቢ ተጉዤ ከሶማሌ ልሂቃን እና የሀገር ሽማግሌዎች ጋር ባደረገነው ውይይት ሙሰጠፋ ቀጣዩ የክልሉ መሪ እንዲሆን ተሰማሙ።

እኔ ወደ ሀገር ቤት ገብቼ በጥቂት ቀናት ውስጥ አብዲ ኢሌ ተይዞ ታሰረ፤ ሙሰጠፋም ከኬንያ ወደ ፊንፊኔ፣ ብዙም ሳይቆይ ወደ ጅግጅጋ በመሄድ በምክትል ደረጃ የፕሬዝዳንትነቱን ሥልጣን በመቆጣጠር አሥተዳደራዊ ተሃድሶ ጀመረ። ቀደም ብለን ባቀድነው መሠረት የሶማሌ እና የኦሮሞን ግጭት በመፍታት ላይ አተኩሬ ወደ ሥራ ገባሁ። ሲካሄድ የነበረው ጦርነት ከውጪ ሲታይ የብሔር ግጭት ቢመስልም ቀረብ ብለን ሰንመረምረው፣ በዋናነት አጎራባች በሆኑ ጎሳዎች መካከል ያለ ውዝግብ ነው። በሁለቱ ክልሎች ድንበር አካባቢ የሚኖሩ ጎሳዎች በጣም ተቀራራቢ ባሕል እና የኑሮ ዘይቤ ስላላቸው፣ እንዲሁም ሁለቱንም ቋንቋዎች አፈራርቀው ሰለሚናገሩ የቱ ሶማሌ የቱ ኦሮሞ እንደሆነ ለማውቅ ያስቸግራል። አሰፋፈራቸው የተቀላቀለ እና በተመሳሳይ የኢኮኖሚ እንቅሰቃሴ ሰለሚተዳደሩ፤ ድንበር የሚለው አሳቤ ዘመናዊ አሥተዳደር ያመጣው ጉዳይ እንጂ በምድር ላይ የሚታይ ተጨባጭ መሥመር አይደለም።

የሁለቱ ክልሎች ድንበር በ2014 በተደረገው ሪፈረንደም ቢወሰንም መሬት ላይ ያለውን ማኅበራዊ እና ኢኮኖሚያዊ እውነታ ብዙም አልለወጠውም። የድንበር ጉዳይ የግጭቱ መንስዔ ሆኖ ቢነገርም የኮንትሮባንድ ንግድ ከፍተኛ ሚና እንደነበረው ለመረዳት ቻልን። የኮንትሮባንድ ነጋዴዎች የጎሳ ግጭቶችን በመቀስቀስ የመንግሥት ጸጥታ ኃይልን ትኩረት አቅጣጫ ለማስቀየር ጠቃሚ ዘዴ ሆኖ አገኙት። የደኅንነት እና የመከላከያ አመራሮች በኮንትሮባንድ ንግዱ ውስጥ ቁልፍ ተዋናኝ መሆናቸው ይህ ዘዴ ውጤታማ እንዲሆን አስችሏል። የቄሮ ትግል ሲፋፋም የሕወሓት ጄኔራሎች ለኮንትሮባንድ ማስተላለፊያ ሲጠቀሙበት የነበረውን መሰመር የጎሳዎች ግጭት በመቀሰቀሰ ለፓለቲካም ይጠቀሙበት ጀመር። የኮንትሮባንድ መተላለፊያ መንገድ ዳር የሚኖሩ የተወሰኑ ጎሳዎችን ሲያጋጩ የነበረበትን ልማድ አድማሱን አሰፍተው ከሞያሌ እሰከ ቦርዶዴ ድረሰ ግጭት በመቀሰቀስ ሁለቱን ብሔሮች እና ክልሎች የጦርነት አውድማ አደረጉት።

ይህን ከተረዳን በኋላ ችግሩን ለመፍታት በክልል/በብሔር እና በጎሳ/በሰፈር ደረጃ መሥራት እንደሚያስፈልግ ተገነዘብን። በቅድሚያ በክልል/በብሔር ደረጃ የተፈጠረውን ቅራኔ ለማሰተንፈስ በከፍተኛ አመራሮች መካከል መግባባት መፍጠር አስፈለገ። ይህን ለማድረግ ግን የችግሩ ምንጭ የሆኑትን አመራሮች ከሥልጣን በማንሳት መጀመር ነበረበት። አዲስ የተሾሙት አመራሮች በሁለቱ ብሔሮች እርቅ ቀድሞውኑ ያምኑ ስለነበር በአጭር ጊዜ ውስጥ በሁለቱ ክልሎች አስተዳደራዊ መዋቅር መካከል መልካም ግንኙነት ተፈጠረ።

በመቀጠል ከሞያሌ እስከ በርዶዴ ጎን ለጎን የሰፈሩትን የሁለቱን ብሔር ጎሳዎች እንደየ ጉርብትናቸው ለማስታረቅ ወደ ሥራ ተገባ። የሀይማኖት አባቶች፣ አባገዳዎች፣ ሱልጣኖች፣ ኡጋዞች እና ገራዶችን ፈንፈኔ ጠርተን አነጋገርናቸው። አንድ ቀን ለማን ለማነጋገር ወደ ኦሮሚያ ፕሬዝዳንት ቢሮ ስሄድ የሆነ ባለሥልጣን ብዙ ሽማግሌዎችን አንድ አዳርሽ ውስጥ ሰብሰቦ ከፊታቸው ተቀምጦ ሲናገር አየሁ። የተሰብሳቢዎቹን ማንነት ስጠይቅ ከባቢሌ አካባቢ የመጡ የሶማሌ እና የኦሮሞ ሽማግሌዎች እንደሆኑና ለማስታረቅ እየተሞከረ መሆኑ ተነገረኝ። ሽማግሌዎቹን ምሳ እንድጋብዝ አስፈቅጄ ወደ ቤቴ ይዣቸው ሄድኩ። በቁጥር ሃምሳ ይሆናሉ። መጀመሪያ በቁምነገር ለመነጋገር ይቅርና ለፈጣሪ ሰላምታ እንኳን ፈቃደኛ አልነበሩም። ስለዚህም ሰለ ሰላም ከማውራታችን በፊት ኩርፊያውን በዘዴ መስበር ነበረብኝ።

ቤቴ ደርሰው ጥቂት ከተቀመጡ በኋላ የሰላት ሰዓት ሲደርስ አንድ ቦታ አንጥፈንላቸው አብረው እንዲሰግዱ አደረግን። ሙስሊም ሆነው አብሮ አለመስገድ አግባብ እንዳልሆነ ተረድተው እየደበራቸውም ቢሆን ተነሰተው ተዘጋጁ። ኦሮሞዎቹ ሶማሌዎች እንግዳ ስለሆኑ ከመካከላቸው አንድ ሰው እንዲያሰግድ ሐሳብ አቀረቡ። ሶማሌዎቹ ደግሞ ባለቀዬው ኦሮሞ ሰለሆነ ያሰግድ አሉ። ትንሽ ከተጨቃጨቁ በኋላ ከሁሉም በዕድሜ ታላቅ የሆነ እንዲያሰግድ ተሰማምተው፤ ሰግድን ሰንጨርስ ምሳ ቀረበ። ምግቡ በየግል ሳይሆን በቡድን እንዲበላ በሰፋፊ ትሪ ቀረበና ሰው ተደባልቆ ተመገበ። በመቀጠል ጫት ቀርቦ መቃም ሲጀመር ገና ከጅምሩ ወደ ንትርክ እንዳይገቡ በመሥጋት የግጭት ጉዳዮች እንዳይነሱ አድርገን ተራ የቀን ተቀን ማኅበራዊ ጉዳዮች እያነሳን እንዲያወሩ አበረታታን።

በቅርብ ጊዜ በመሃከላቸው በተከሰተ ጦርነት ይቆራረጡ እንጂ፤ እነዚህ አጎራባች ጎሳዎች ሁለቱንም ቋንቋ ከመናገር ባለፈ ብዙዎቹ የሥጋ ዝምድና እንደነበራቸው ከወሬያቸው ተረዳሁ። አንድ እንግዳ የሆነብኝ ነገር ከነበሩት ሰዎች መካከል በብሔር ኦሮሞ ሆኖ የሶማሌ ቋንቋ እንጂ አፋን ኦሮሞ የማይችል፣ ሶማሌ ሆኖ ደግሞ አፋን ኦሮሞው ከሶማልኛው የሚሻል መኖራቸው ነበር። ጨዋታቸው እየደራ ሲሄድ የእርሰ በእርሰ መከፋታቸውን ለተወሰነ ጊዜ ረስተው ቦታ እየቀያየሩ እየተፈላለጉ ዘመድ አዝማድ መጠያየቅ ጀመሩ። በድንበር ጦርነት ምክንያት ለረጅም ጊዜ ተቆራርጠው ተነፋፍቀው ሰለነበር ጠዋት የነበረው መኮራረፍ እና መፈራራት እንደጠፋ ሰለተረዳሁ፤ የአስር ሰላት እንደሰገድን የተሰበሰብንበትን ቁምነገር ወደ መወያየት ገባን። ሁለቱም ወገኖች ቅሬታቸውን አቀረቡ። ተናጋሪዎች በንዴት ስሜት ውስጥ ሲገቡ ጣልቃ በመግባት እያረጋጋሁ በትዕግሥት እንዲደማመጡ አደረኩ። ቅሬታው ተሰምቶ ካለቀ በኋላ በብዙ ጉዳዮች ላይ ወደ መተማመን ቀረቡ። ሁሉም ጎራ ለወደፊቱ አብሮ የመኖርን እና እርቅ የማውረድን አሰፈላጊነት አጽንዖት ሰጥተው ተናገሩ።

የግራ ቀኙን አሰተያየት በጥሞና ሰከታተል ቆይቼ ግንባር ቀደም አጀንዳ ቀራጮች (opinion

makers) እነማን እንደሆኑ ግልጽ እየሆነልኝ መጣ። ቀሰ ብዬ ሳጣራ እነዚያ አጀንዳ ቀራጮች ከኮንትሮባንድ ነጋዴዎች ጋር ግንኙነት አንዳላቸው ለማወቅ ቻልኩ።

ከሁለቱ ወገን የተውጣጣ አነስተኛ ቡድን መሥርቼ ለብቻ ሳወያይ እነዚያን አጀንዳ ቀራጮች ማሳመን ከተቻለ ሰላም ማስፈን እንደሚቻል ተረዳሁ። በቀኑ ውይይት የተደረሰውን ሰምምነት የማሰፈጸም ኃላፊነት ለአጀንዳ ቀራጮቹ ለመስጠት ወሰንን። ከእነሱ ወገን አንድ ጥይት ከተተኮሰ ተኳሹን አጋልጦ ለፖሊስ አሳልፎ መስጠት የእነሱ ግዴታ እንደሆነ፤ አለበለዚያ ግን የብጥብጡ ምንጭ ተደርገው እንደሚወሰዱ ተሰማማን።

በሁለቱ ብሔሮች መካከል የተሄደው ጦርነት ሲባባስ የነበረው በሦስት ኃይሎች ነበር። የመጀመሪያው በሁለቱም ወገን ከክልል እስከ ቀበሌ የተሰገሰጉ አሥተዳዳሪዎች እና የጸጥታ ዘርፍ ሰዎች ናቸው። ሰላም ለማምጣት እነዚህን ሰዎች ከቦታቸው ዞር ማድረግ ሰለሚያሰፈልግ ለውጡ እንደመጣ በፍጥነት ተፈጸመ። ሁለተኛው ኃይል የፌደራል ወታደራዊ መኮንኖች እና የደኅንነት ሰዎች ሲሆኑ፣ ዋና ዋናዎቹ ከሽግግሩ ጋር ከአካባቢው ርቀዋል። ሦሰተኛው የዲያስፖራ ማኅበረሰብ ሲሆን፣ ከሚኒሶታ (አሜሪካ) ጀምሬ፣ አውሮፓ፣ ኬንያ እና ዱባይ በመሄድ በጦርነቱ ውስጥ እጃቸው ያለበትን ሰዎች አና ቡድኖች በማነጋገር ግጭቱን በፕሮፓጋንዳ እና በገንዘብ ማገዛቸውን አቁመው እርቅ በማውረድ እንዲረዱን ተማጸንኩ። ብዙዎቹ ጥሪውን ተቀብለው በመተግበር ለእርቀ-ሰላሙ ሰኬት የበኩላቸውን ሚና ተጫውተዋል።

የኦሮሞ እና የሶማሌን ግጭት ለመፍታት ባደርግነው ጥረት አሰቸጋሪ የነበረው ሞያሌ እና ድሬደዋ አካባቢ ነው። የድሬደዋውን ግጭት ለመፍታት በሁለት ደረጃ ተንቀሳቀሰን። የመጀመሪያው በወቅቱ ተደጋግመው ሲከሰቱ ለነበሩ ሁከቶች መንስዔ የሆኑትን ሁኔታዎች በመፍታት እሳቱን ማጥፋት ነው። ሁለተኛው ከነዋሪዎቹ ለሚነሱ የባለቤትነት አና አሥተዳደራዊ ጥያቄዎች በሂደት መፍትሔ መፈለግ ናቸው። ኦሮሞው ከተማዋ ሕገ-መንግሥታዊ ባልሆነ አሠራር ከኦሮሚያ ተነጥላለች የሚለውን የይገባኛል ጥያቄ ወደጎን ትቶ፣ ጊዜያዊ ግጭቶችን ማሰቆም ላይ እናተኩር የሚለውን የእኛን አካሄድ እንዲቀበል ማሳመን ከባድ ነበር።

ስለዚሀ አካሄዳችን የባለቤትነት ጉዳይን የሚጻረር ሳይሆን በሕግ እና በውይይት ለመፍታት በቅድሚያ ከተማዋን እያመሳት ያለውን ሁከት አስቁመን ሰላም የማሰፈንን አሰፈላጊነት መግለጽ ነበረብን።

የሕወሓት አገዛዝ የኦሮሞን ሕዝብ ከአጎራባች ብሔሮች ጋር ለማጋጨት ከቀበራቸው ፈንጂዎች ውሰጥ አንዷ ድሬደዋ መሆኗንና ቀሰ ብለን በዘዴ ካልሄድን በሰተቀር ፈንድቶ ብዙ ነገሮችን ሊያጠፋብን እንደሚችል ለማስረዳት ሞከርኩ። ሐሳቤ ለአሁኑ ግጭቱን እንግታ፣ ሀገሪቷን እናረጋጋ፣ ከዚያም የባለቤትነት እና የአሥተዳደር ጥያቄዎችን የኦሮሞ፣ የሶማሌ አና በከተማዋ ያሉ የሌላ ብሔር ተወላጆችን ጥቅም እና መብት ባማከለ መልኩ እንፍታ የሚል ነበር።

መጀመሪያ ላይ የድሬደዋ እና የአካባቢውን ቄሮዎች፣ በርበርታ (የሶማሌ ወጣቶች) ፣ አባ ገዳዎች እና ኡጋዞችን ወደ ፊንፊኔ ጠርቼ ካወያየሁ በኋላ በቀጣይ በድሬደዋ የጋራ ውይይት ለማዘጋጀት አቀድን። ወደዚህ ጉዞ የሄድነው በወቅቱ የሶማሌ ክልል ፕሬዝዳንት ሆኖ ሥራ ከጀመረው ሙስጠፋ ሙሐመድ ጋር ነበር። ድረደዋ ኤርፖርት ሰንደርሰ ሞቅ ያለ አቀባበል ተደርጎልን ከሁለቱም ወገኖች ተወካዮች ጋር የአዳራሽ ውሰጥ ስብሰባ አካሄድን። ሕዝቡም

የሁለቱ ወገን አመራር አብሮ በመገኘቱ ያለውን ደሰታ፤ ከተማዋን እያወከ ያለውን ግጭት በአስቸኳይ እንድናሰቆም ተማጸነ። ከሁለቱ ወገን ያሉ ቅሬታዎች እና ጥያቄዎችም ቀርበው ሰፊ ውይይት አደረግን። በዚህ ጉዞ ሥራውን ማጠናቀቅ ሰላልቻልን፤ ወደ ከተማዋ ሁለት ሦስቴ መመላለስ ነበረብኝ።

የድሬደዋን ግጭች ውስብስብ ያደረገው በሁከቱ ወቅት የተገደሉ የጅቡቲ ዜጋ የሆኑ ሱማሌዎች ጉዳይ ነበር። ጉዳዩን በሽምግልና ለመጨረሰ ስንሞክር የሶማሌ ሽማግሌዎች ለሟች ቤተሰቦች ካሳ እንዲከፈል ጠየቁ። የኦሮሞ ሽማግሌዎች ደግሞ «ካሳ እንከፍላለን ነገር ግን ወንጀሉን የፈጸመው ግለሰብ መታወቅ አለበት፤ ሰለዚህ የሶማሌ ሽማግሌዎች ግድያ የፈጸመውን ግለሰብ ለይተው ይንገሩንና የወንጀለኛውን ጎሳ አስገድደን ካሳ እናሰከፍላለን አሉ።

ችግሩ ግድያው የተፈጸመው በቡድን ፀብ (mob riots) ጊዜ በመሆኑ "ኦሮሞ ገደለው" ከማለት ውጪ የትኛው ግለሰብ ወንጀሉን እንደፈጸመ መለየት አለመቻሉ ነበር። የሁለቱም ወገን ሽማግሌዎች ክርክር ባሕላዊ መሠረት ስላለው በቀላሉ ልናልፈው አልቻልንም። ከዚህ በመነሳት ማምለጫ መላ ፈጠርን።

የካሳውን ገንዘብ እኔ እንደማፈላልግ ቃል ገባሁላቸው። እንደዛም ሆኖ የኦሮሞን ሽማግሌዎች ማሳመን ቀላል አልነበረም። «እኛ ገንዘብ አጥተን ሳይሆን አካሄዱ የካሳን ሥርዓት ያልጠበቀ ሰለሆነ ነው>> አሉ።

በባሕላዊ መንገድ አልሆን ሲለን ዑለሞች (የእሰልምና ሊቃውንት) አባገዳዎቹን እንዲያሳምኑ በማድረግ ተሳካልን፤ ገንዘቡን ከባለሀብቶች አሰባሰቤ ካሳውን ከፍዬ ጉዳዩ ተፈታ።

ቀጥሎ ወደ ጅቡቲ ሄጄ በድሬደዋ ጉዳይ ላይ እጃቸው ካለበት አካላት ጋር በመመካከር የከተማዋን ሰላም እና መረጋጋት እንዲደግፉ ተማጸንኩ። በድሬደዋ እና ጅቡቲ መካከል ጠንካራ ማኅበራዊ ትስስር አለ። በሁለቱም ቦታ የሚኖሩት ሶማሌዎች ከኢሳ ጎሳ ሲሆኑ በሁለት ሀገራት ቢከፈሉም የሚተዳደሩት በአንድ ባሕላዊ መሪ (ኡጋዝ) ነው። የጅቡቲ ሙቀት ሲያይል ብዙ ዜጎቿ ወደ ድሬደዋ በመምጣት ዕረፍት ያደርጋሉ። የሀገሪቱን ፕሬዝዳንት ኢስማዔል ኦማር ጌሌን ጨምሮ ብዙ የጅቡቲ ዜጎች ትውልዳቸው ድሬደዋ ነው። ባለፉት መንግሥታት በደል የተሰደደ ብዙ ኦሮሞ በጅቡቲ ይኖራል። ሰለዚህም የድሬደዋ ሰላም የሁለቱን ከተሞች ሕዝብ በቀጥታ እንደሚመለከት እና አብሮ መሥራት እንደሚያሰፈግ ተሰማማን።

በሞያሌ አካባቢ በቦረና እና ገሪ ጎሳዎች መካከል ያለው ግጭት ደግሞ የባሰ ውሰብሰብ ነበር። ተመሳሳይ ቋንቋ የሚናገሩት እነዚሀ ሁለቱ ጎሳዎች ለዓመታት ተደጋጋሚ ደም አፋሳሽ ጦርነቶችን አካሂደዋል። የሁለቱ ጎሳዎች ግጭት መንስዔ ውስብስብ እና ረጅም ታሪክ ያለው ሲሆን፣ በቄሮ ትግል ወቅት የሶማሌ እና የኦሮሚያ ክልሎችን በብሔር ደረጃ ለማጋጨት በተሸረበው ሤራ ምክንያት ተባብሶ ከሁሉም ድንበሮች የከፋው ጉዳት እዚህ ደርሷል። የሞያሌ ከተማን ሁለት ቦታ በመክፈል ከአስፓልት ወዲሀ ለኦሮሚያ ክልል፤ የቀረው ለሶማሌ ክልል ተሰጥቷል። አካባቢው ከሶማሊያም ሆነ ከኬንያ የሚመጣ እና የሚሄድ ዋና የኮንትሮባንድ ንግድ መተላለፊያ መሆኑም ግጭት ለመቀሰቀስ አመቺ ያደርገዋል። የሁለቱን ጎሳዎች ግንኙነት የበለጠ ውሰብሰብ ያደረገው ሁለቱም በኬንያም በኢትዮጵያም ሰለሚኖሩና የሁለቱ ሀገራት ፖለቲከኞች እጃቸውን ማስገባታቸው ነበር።

የሁለቱን ወገን (ገሪ እና ቦረና) ሽማግሌዎች በአሜሪካ፣ በኬንያ አና በፊንፊኔ አነጋግረን ሰላም በማስፈን ላይ እንዲረዱን ብዙ ጥረት ተደረገ። ጥረቱን ስጀምር በገሪዎች ወገን እኔን ማመን

ከብዷቸው ነበር። ምክንያቱም በጦርነቱ ወቅት OMN ለቦረና ወግኗል የሚል ቅሬታ ይቀርብበት ስለነበረ ነው።

ይህ ጉዳይ በገሪ ማኅበረሰብ ዘንድ ምን ያህል ቅሬታ እንደፈጠረ ለመጀመሪያ ጊዜ የተረዳሁት የረጅም ጊዜ ወዳጄ እና የጎሳው አባል ከሆነው ሲራጅ ሁሴን ነው። በካሊፎርኒያ ግዛት ኦሬንጅ ካውንቲ (orange country) ከተማ ውስጥ ይኖር ነበርና አሜሪካ እንደሄድኩ መጀመሪያ ከተዋወኳቸው ኦሮሞዎች አንዱ ነው። ፓልቶክ ላይ "komba" በሚል ሰም ይጠቀም ነበር፤ እኔ ደግሞ በአያቴ ቶላ ቡሊ ሰም እታወቃለሁ።

ከሲራጅ ጋር በፓልቶክ ተዋውቀን በሎስ አንጀለስ የኦሮሞ ኮሚኒቲ ሰብሰባ ላይ እንድሳተፍ ጋበዘኝ። ውጭ ሀገር በሚደረግ የኦሮሞ ስብሰባ ላይ እንድገኝ እና እንድናገር የጋበዘኝ የመጀመሪያው ሰው እርሱ ነበር። በዚሁ ግንኙነታችን ተጠናክሮ እንደ ልጁ አቀረበኝ። ሲራጅ ጠንካራ የኦነግ ደጋፊ፣ እኔ ደግሞ የድርጅቱ ተቺ ሰለነበርኩ የፖለቲካ አመለካከታችን ብዙ ጊዜ ባይገጥምም ከፖለቲካ መስመር ይልቅ ኦሮሞነትን የሚያሰቀድም ሰው ሰለሆነ በጥሩ ወዳጅነት አብረን ቆይተናል። የዕረፍት ጊዜዬን ከእሱ ቤተሰብ ጋር አሳልፍ ነበር። እንደ ዶ/ር ጉደታ ሂኒካ ካሉ ጉምቱ ምሁራን ጋርም አሰተዋውቆኛል።

ለውጡ ሲመጣ በቀለ ገርባን ለሕክምና ዶ/ር ጉድታ ሂኒካ ጋር በወሰድኩበት ወቅት ሲራጅ እና ባለቤቱ ሊጠይቁን መጡ። ልክ እንዳዩን ሁለቱም ማልቀሰ ጀመሩ። ሁሉም ተደናግጠው ምን እንደተፈጠረ ሲጠይቋቸው፤ የኦሮሞ አንቂዎች እና ሚዲያዎች ለቦረና ወግነው ገሪን ማግለላቸው ፍትኃዊ እንዳልሆነ ቅሬታቸውን ተናገሩ። የእኔ ድርጊት ምናልባት ለሐዘናቸው አሰተዋጽዖ አድርጎ ከሆነ ብዬ ይቅርታ ጠየቅኩ። ወያኔ የሰማሌን ክልል ልዩ ኃይል በመጠቀም ድንበር ጥሶ ኦሮሞን ለመግደል የሚያደርገውን ዘመቻ ለመመከት እንጂ ለቦረና አድልተን ገሪን ለመጉዳት እንዳልሆነ ለማሰረዳት ሞከርኩ።

በገሪ ማኅበረሰብ ዘንድ የOMN አዘጋገብ ለቦረና እንደመወገን ተደርጎ መወሰዱን በመረዳት፤ ወደ ኋላ ሄጄ ሰበብ በመደርደር ባለውለታዬ የሆኑትን ሲራጅ እና ባለቤቱን የበለጠ ከማስከፋት፤ ይቅርታ ጠይቆ ወደፊት የሚፈጠሩ ግጭቶችን መከላከል ይሻላል የሚል አቋም ያዝኩ።

ከእነርሱም ጋር ያለፈውን ቁስል ከመነካካት ተጨማሪ ጉዳት እንዳይደርሰ ተባብረን ሰላም ማስፈን እንደሚሻል ተግባባን። ጠ/ሚኒሰትር ዐቢይ አሕመድ እና ለማ መገርሳ ወደ ሚኒሶታ የመጡ ዕለት ከሰሜን አሜሪካ ግዛቶች የተሰባሰቡ የገሪ ማኅበረሰብ መሪዎች መጥተው ሊያገኟቸው ቢሞክሩም አልተሳካላቸውም። በር ላይ ቆመው ሲጠብቋቸው ስላየሁ ወደ OMN ቢሮ ወስጄ እርቅ የሚወርድበትን ሁኔታ ተወያይተን፤ ግጭቱን በፍጥነት አስቁመው የሕዝቡን ስሜት ለእርቅ እንደሚያዘጋጁ ቃል ገብተው ተለያየን።

በእኔ እና በOMN ላይ የሚቀርበው ቅሬታ ከገሪ ማኅበረሰብ ብቻ አልነበረም። የቦረና ማኅበረሰብም በጦርነቱ ወቅት "በአግባቡ አልጮኸልንም" የሚል ቅሬታ ነበራቸው። ገሪዎች "ጀዋር ለቦረና የሚያዳላው አማቾቹ ስለሆኑ ነው" ሲሉ፤ ቦረናዎች በፊናቸው "እኛ የተገለልን (marginalized) ማኅበረሰብ በመሆናችን በቂ ትኩረት እና የሚዲያ ሽፋን እያገኘን አይደለም" ሲሉ ቅሬታቸውን ያቀርቡብናል። በሁለቱ ማኅበረሰቦች መካከል ሰላም ለመፍጠር ጥረት ማድረግ የጀመርነው በዚህ ዓይነት ጫና ውሰጥ ሆነን ነው።

በኦሮሚያ እና በሰማሌ መካከል ያለው የድንበር ጦርነት በአብዛኛው ቦታ ለውጡ እንደመጣ

ሲቆም፣ በገሪ እና በቦረና መካከል ያለው ግን ቀጠለ። ይህን ያደረገው በሁለቱ ማኅበረሰቦች መካከል ግጭት ሲፈጥሩ የነበሩ ወታደራዊ ባለሥልጣናት ከስልጣናቸው ባለመነሳታቸው ነው። ለምሳሌ በአካባቢው ከሀያ ዓመታት በላይ የቆየ እና በኮንትሮባንድ ንግድ የሚታወቅ አንድ ኮሎኔል በሞያሌ በጠራራ ፀሐይ አምስት ሰዎችን ቢገድልም እዚያው ወታደራዊ ካምፕ ውስጥ 'ታሰሮ' ሕዝቡን ማጋጨቱን ቀጥሎበት ነበር።

እርቅ ለማውረድ የምናደርገውን ሙከራ ሽማግሌዎችን በማስፈራራት እና አንዳንዶቹን በገንዘብ በመደለል ሲያከሽፍብን ቆየ። በወቅቱ የመከላከያ ኢታማዦር ሹም እና ምክትል ለነበሩት ለጄ/ል ሰዓረ መኮንን እና ጄ/ል ብርሃኑ ጁላ አቤቱታ አቅርበን፤ ኮሎኔሉ እና ከእሱ ጋር ትስስር ያላቸው መኮንኖች ከቦታው እንዲነሱ ተደረገ። ከዚያ በኋላ የሁለቱን ጎሳ ሽማግሌዎች ወደ ፊንፊኔ ጠርተን ውይይት መጀመር ተቻለ። ወደ ናይሮቢ፣ ኬንያ በመጓዝም ከሁለቱ ጎሳዎች የተውጣጡ የመንግሥት ባለሥልጣናትን እና ባለሀብቶችን በጋራ ሰብስቤ ሰላምን ለማምጣት ሚናቸውን እንዲወጡ አወያየሁ።

የሞያሌን አካባቢ ለተደጋጋሚ ግጭት ተጋላጭ ያደረገው የኮንትሮባንድ ንግድ ስለሆነ ዋና ዋና የሆኑትን ነጋዴዎች በመለየት ሰላም ለማስፈን በሚደረገው ጥረት ገንቢ ሚና እንዲኖራቸው ለማሳመን ሞከርኩ። እነሱም ከጀርባቸው የነበሩት ጄኔራሎች ከአካባቢው በመነሳታቸው ፍራቻ ውስጥ ሰለነበሩ ለመተባበር ፍላጎት አሳዩ። በዚህ ሁኔታ በሁለቱ ጎሳዎች መካከል ለዓመታት ሲካሄድ የነበረው ጦርነት ሊቆም ቻለ። የገሪ እና የቦረና ግጭትን ለማስቆም ባደረግነው ሙከራ ለማ እና ሙስጠፋ የሁለቱ ክልሎች ፕሬዝዳንቶች መሆናቸው በጣም ጠቅሞናል። በተጨማሪም በወቅቱ የፌደራል ፖሊስ ኮሚሽነር የነበረው ዘይኑ ጀማል ሙከራው እንዲሳካ ከፍ ያለ አስተዋጽዖ ነበረው።

ለወራት በተደረገ ያሰለሰ ጥረት የቦርና እና የገሪን ግጭት ማስቆም ቢቻልም፣ ሁለቱን ጎሳዎች የሚያጣሉ ቀሪ ጉዳዮችን ከመሠረቱ ለመቅረፍ ተጨማሪ ሥራዎች ቢያስፈልጉም፤ ወደኃላ ላይ የመንግሥት ትብብር እየቀነሰ ስለሄደ ሥራዎቹን ለመስራት አሰቸጋሪ ሆነ። አንዳንድ የመንግሥት ባለሥልጣናትም ጥረቱን ማደናቀፍ ጀመሩ። ለዚህ ምክንያቱ በእኔ እና በመንግሥት መካከል ያለው ግንኙነት እየሻከረ መሄዱ ሳይሆን አይቀርም። ሆኖም ላለፉት አምስት ዓመታት ሁለቱ ማኅበረሰቦች ወደ ግጭት ሳይመለሱ በአንጻራዊ ሰላም መቆየታቸውን ስመለከት ባደረኩት ጥረት እደሰታለሁ።

በሶማሌ እና በኦሮሞ መካከል ሰላም እንዲሰፍን የሶማሌ ክልል ፕሬዝዳት ሙሰጠፌ ሙሐመድ ልዩ ምስጋና ይገባዋል። በቀድሞው ሥርዓት ወንድሙ በግፍ የተገደለ በመሆኑ የኦሮሞ ሕመም የሚሰማው ሰው ነው። ከዚህም በላይ የሶማሌ እና የኦሮሞ ሕዝቦች ማኅበራዊ ብቻ ሳይሆን ጠንካራ የኢኮኖሚ ትሰሰር እንዳላቸው ይረዳል። የሁለቱ ብሔሮች ፖለቲካዊ እና ኢኮኖሚያዊ ዕጣ ፈንታ ሊነጣጠል እንደማይችል ከልቡ በማመኑ ሰፊ ሥራ ሠርቷል። ከእኔ ጋር ከትግሉ ጊዜ ጀምሮ ሰለምንተዋወቅ አብሮ ለመሥራት ቀሎናል። በሶማሌ እና በኦሮሞ መካከል የተደረገው እርቅ እንዲሳካ ለማ መገርሳም የሚያስመሰግን ትብብር አድርጓል።

በአጠቃላይ በኦርሞ እና በሶማሌ መካከል ሰላም እንዲሰፍን ያደረግነው ጥረት ከምከራባቸው ሰኬታማ ሥራዎች አንዱ ነው። በሺዎች የሚቆጠር ሕይወት ሲቀጥፉ የነበሩ ግጭቶች ረግበው ሕዝቦች በአጭር ጊዜ ውሰጥ ወደ ሰላም ተመልሰው ቀደም ሲል የነበረው ማኅበራዊ እና ኢኮኖሚያዊ ግንኙነታቸው የበለጠ ተጠናክሮ በማየቴ አጅግ በጣም አስደሰቶኛል።

በቀጣይ በሶማሌ እና በኦሮሞ መካከል ያለውን ስትራቴካዊ ግንኙነት የበለጠ ለማጠናከር አመራሩ፣ ምሁራን እና ነጋዴዎች የበለጠ መቀራረብ እና በትብብር መሥራት አለባቸው። ሶማሌ ስንል ኢትዮጵያ ውስጥ የሚያዋስኑን ብቻ ሳይሆኑ ሞቃዲሾ፣ ሀርጌሳ እና ጅቡቲ ያሉትንም ይጨምራል። ከአፍሪካ ውስጥ ከሶማሌ ሕዝብ በላይ ከሀገራችን ጋር ጥቅሙ አብሮ የተሳሰረ የለም። በተለይም በኢኮኖሚ ረገድ ከሶማሌ ሕዝብ ጋር ያለን ግንኙነት ከየትኛውም የአፍሪካ ሀገር ይበልጣል። ከሶማሌ ሕዝብ ጋር የምናደርገው የንግድ ልውውጥ በዓመት ከሁለት ቢሊዮን እንደሚበልጥ ይገመታል። ስለዚህ ታሪካዊ ቁርሾዎችን በማከም፣ ይህንን ግንኙነት የበለጠ በማጠናከር፣ የሶማሌ ማኅበረሰብ ሰላም፣ አንድነት እና መረጋጋት እንዲኖረው መርዳት እራስን መርዳት እንደሆነ ማወቅ አስፈላጊ ነው።

## 8.4. የብሔር ብሔረሰቦችን ትግል መደገፍ

ወደ ሀገር ቤት እንደተመለስኩ ትኩረት ካደረግኩባቸው ቀዳሚ ሥራዎች ውስጥ አንዱ በደቡብ ብሔር ብሔርሰቦች እና ሕዝቦች ክልል የሚገኙ የተለያዩ ወገኖች ለረጅም ጊዜ ሲያነሱ የነበሩትን የመብት ጥያቄዎች መደገፍ ነበር። በለውጡ ማግሰት በቄሮ ትግል አርአያነት እና አነሳሽነት የክልሉ ወጣቶች በተለያየ መልኩ ተደራጅተው የብሔራቸውን የክልልነት ጥያቄ እውን ለማድረግ ትግላቸውን አጧጧፉ። OMN በሚዲያ ሽፋን፤ እኔ ደግሞ በሰላማዊ ትግል ሰልት እና ሰትራቴጂ ላይ ሥልጠና በመስጠት እንድናግዛቸው ያቀረቡልንን ጥያቄ በደሰታ ተቀብለን ከጎናቸው በመሆን አግዘናቸዋል።

የኢትዮጵያ ዘመናዊ ሀገረ-መንግሥት ከተመሠረተበት ጊዜ ጀምሮ እንደ ኦሮሞ ሁሉ በደቡቡ የሀገሪቱ ክፍል የሚገኙ ብሔሮች ለባሕል እና ለቋንቋ ጭቆና እንዲሁም ለከፍተኛ የኢኮኖሚ ብዝበዛ ተዳርገዋል። ሰቃያቸው ከእኛም ይከፋል። የኦሮሞ ትግል ገና ከጥንስሱ ከደቡብ ብሔሮች ጋር በመተባበር ይህን የጋራ ጨቋኝ ሥርዓት በጋራ ማሰወገድ ላይ ያተኮረውም ለዚህ ነው።

የሜጫ እና ቱለማ ማኅበር ሲመሠረት በደቡብ ክልል የሚገኙ የተለያየ ብሔር ተወላጆች አጋርነታቸውን ለማሳየት የማኅበሩ አባል መሆናቸውን ታሪክ ያሳያል። የኦሮሞ ትግል በፓለቲካ ድርጅት መመራት ሲጀምርም፤ የኦነግ መሥራቾች በደቡቡ የኢትዮጵያ ክልል ከሚገኙ ጭቁን ብሔሮች ጋር ያላቸውን አጋርነት የበለጠ ለማጠናከር የኢትዮጵያ ጭቁኖች አብዮታዊ ትግል (ኢጭአት) የሚባል ድርጅት መሥርተዋል። የደቡብ ብሔሮች ጭቆና ከኦሮሞ ጋር ተመሳሳይ ስለነበር፤ የኦሮሞ ትግል ፍሬ ሲያፈራ እነዚህ ብሔሮችም ተጠቃሚ ነበሩ። ለምሳሌ የመሬት፣ የቋንቋ እና የክልልነት ጥያቄ ሲመለስ እነዚህ ብሔሮች በጋራ ተጠቃሚ ሆነዋል።

ከኦሮሞ ጋር ሲጨቆኑ ከቆዩ እና ለረጅም ጊዜ የትግል ትብብር ከነበራቸው ውሰጥ አንዱ የሲዳማ ብሔር ነው። ኦሮሞ እና ሲዳማ የጋራ የጭቆና ታሪክ ብቻ ሳይሆን ጠንካራ የባሕልና የቋንቋ ትስስር አላቸው። በ1970ዎቹ የትጥቅ ትግል ሲጀመር የሲዳማ ታጋዮች ከኦሮሞ አቻዎቻቸው ጋር በሀገር ውሰጥ እና በጎረቤት ሶማሊያ በጋራ ሲታገሉ ነበር። የ1983 ዓ.ም ለውጥን ተከትሎ ሲዳማ የራሱን ክልል መመሥረት የቻለ ቢሆንም፤ በኃላ ላይ ያለ በቂ ምክንያትና ያለፍላጎቱ በደቡብ ብሔር ብሔረሰቦች ክልላዊ መንግሥት ሥር መጠቃለሉን በመቃወም ትግሉን ቀጠለ። በዚህ ትግል ምክንያት የሲዳማ ሕዝብ ብዙ ሰቆቃ ደርሶበታል። በተለይ በ2002 ሉቄ በተባለ አካባቢ ሰላማዊ ሰልፍ የወጡ የብሔሩ ተወላጆች በጅምላ ተገድለዋል፤ ሆኖም የግፍ ግድያው ሕዝቡ መብቱን ከመጠየቅ አላገደውም።

የቄሮ ትግል ሲፋፋም እኛም እንደ አባቶቻችን ከተጨቆኑ ብሔሮች ጋር ለመተባበር ሙከራ አድርገናል። በOMN ላይ የሲዳማ ቋንቋ (sidaamu Afoo) ፕሮግራም እንዲሰራጭ የአየር ሰዓት እንዲሰጣቸው ማድረግ ከእነዚህ የትብብር ሙከራዎች አንዱ ነው። ፕሮግራሙ

የሕዝቡን ትግል በአዲስ መልክ አቀጣጠለ። ኤጀቶ የተሰኘው የወጣቶች ንቅናቄ ተወልዶ ትግሉን ማደራጀት እና መምራት ጀመረ። የኤጀቶ ንቅናቄ ከቄሮ ጋር በመተባበር ብዙ የትግል ሥራዎችን አከናውኗል። በሻሸመኔ እና በሐዋሳ አካባቢ በሚደረገው ተቃውሞ ላይ የሲዳማ ወጣቶች (ኤጄቶዎች) ወሳኝ እገዛ አድርገዋል።

በተለይ በአስቸኳይ ጊዜ አዋጁ ወቅት መንግሥት ለሚያሳድዳቸው ቄሮዎች ከለላ በመሆንና በቀዬያቸው በመሸሸግ ሕይወታቸውን አትርፈዋል። እንዲሁም ቄሮዎች መንገድ ሲዘጉ የሲዳማ ሽማግሌዎች የመንግሥት ጦር በሲዳማ መሬት አልፎ እንደ አጄ እና ሻላ ባሉ በታዎች ላይ ጥቃት እንዳያደርስ ተከላክለዋል።

ከለውጡ በኋላ የሲዳማ ሕዝብ በአንድነት ተነሰቶ የክልልነት ጥያቄውን አጠናክሮ ሲቀጥል፤ እኛም ሲዳማ ሚዲያ ኔትዎርክ (SMN) የተባለውን የራሳቸውን የሚዲያ ተቋም እንዲያቋቁሙ አግዘናል። የሀገር ሽማግሌዎች እና ወጣቶችን በተለያዩ ዝግጅቶች ላይ በመጋበዝ ጥያቄያቸውን ለኦሮሞ ሕዝብ እንዲያሰተዋውቁ ዕድል ሰጥተናል። በ2022 ዓ.ም የሲዳማ ዓመታዊ ክበረ በዓል (ጨምበላላ) ዝግጅት ላይ የኦሮሞ ሕዝብ ከመላው የክልሉ ዞኖች ወደ ሐዋሳ ተጉዞ በመሳተፍ አጋርነቱን አሳይቷል። በወቅቱ አዲስ የተሾሙት የኦሮሚያ ፕሬዝዳንት ሽመልስ አብዲሳ የመንግሥት ልዑካንን ይዘው ሄደው ነበር። እኔም ከአባገዳዎች እና ከሀይማኖት አባቶች ጋር በመሄድ በዓሉን አድምቀነዋል። በዝግጅቱ ላይ የመናገር ዕድል ሲሰጠን የሲዳማ ብሔር ጥያቄ የሕግ እና የፍትሕ ጥያቄ እንደሆነና ሕዝቡ ይን መብት ከሃምሳ ዓመት በኋላ እውን ሊያደርግ መቃረቡን በመግለጽ፣ «በውዴታም ሆነ በግዴታ መጎናጸፋችሁ አይቀርም›› ብዬ ተናገርኩ። የብሔሮችን ራሰን በራሰ ማሥተዳናደር የሚቃወሙ ሚዲያዎች ንግግሬን በማውገዝ ሌሎች ብሔሮችን ለማፈናቀል እና ለመጉዳት እንደተናገርኩ አድርገው ሰፊ ፐርፓጋንዳ ሠሩ። እነዚያ ሚዲያዎች የሲዳማ ክልል መፈጠር ኢትዮጵያን ያፈርሳል በማለት ቀድሞውንም ሲያራግቡ ስለነበር፤ ለሲዳማ ትግል ባደረግነው ድጋፍ በመናደድ ሰፊ የስም ማጥፋት ዘመቻ ማካሄዳቸው የሚያስደንቅ አይደለም።

የፌደራል መንግሥት በሲዳማ ጥያቄ ላይ የጠራ አቋም አልነበረውም። መጀመሪያ ላይ ጠቅላይ ሚኒስትሩ እና ሌሎች ባለሥልጣናት ለሲዳማ ትግል አጋርነት አሳይተው ነበር። ጠ/ሚኒስትር ዐቢይ የኢሕአዴግ ሊቀመንበር ሆኖ እንዲመረጥ የሲዳማ ተወካዮች ድምፅ በመሰጠት ሰለደገፉት ውለታችንን ይመልሳሉ የሚል ተስፋ ነበራቸው። የፌደራል መንግሥት የሲዳማን ክልል ለመፍጠር ሕዝበ-ውሳኔ ለማካሄድ ፈቃደኛ ይሆናል በሚል ግምት የሲዳማ ዞን ምክር ቤት ክልል ለመሆን በሙሉ ድምፅ ወስኖ በሕገ-መንግሥቱ መሠረት ምለሽ እንዲያንኝ ወደ ፌዴሬሽን ምክር ቤት ላከ። አዎንታዊ መልስ እንደሚያገኙም በመገመት ሕዝበ-ውሳኔው የሚካሄድበትን ቀን ወሥነው ወደ ዝግጅት ገቡ። የፌደራል መንግሥት ግን ቀደም ሲል የገባውን ቃል ማጠፉን የሚጠቁሙ ምልክቶች መታየት ጀመሩ። ለዚህ የአቋም ለውጥ የተለያዩ ምክንያቶች ነበሩ።

አንደኛው፣ ለሲዳማ ክልል ቢሰጥ ሌሎች ብሔሮችም ተመሳሳይ ጥያቄ ሊያነሱ ሰለሚችሉ የደቡብ ክልል የብጥብጥ ማዕከል ይሆናል የሚል ሥጋት ነበር። ሁለተኛው ብሔሮች የራሳቸውን ክልል መመሥረታቸውን የሚቃወሙ ኃይሎች ከተለያዩ አቅጣጫዎች በሚያካሄዱት የሚዲያ ዘመቻ የፌደራል መንግሥቱ ላይ ጫና ማሳደር መቻላቸው ነበር። ሦስተኛው ምክንያት በኋላ

ላይ ግልጽ እንደሆነው ጠቅላይ ሚኒስትሩ አዲስ ለማቋቋም ያቀደው ፓርቲ ህብረብሄራዊ ፌደራሊዝምን የማይደግፍ በመሆኑ ለሲዳማ ክልልነትን መፍቀድ ከአዲሱ ፓርቲ እቅድ እና አመለካከት ጋር ሰለሚቃረን ነበር።

ወደ ሀገር ቤት እንደገባሁ በነበረኝ ግምገማ የፌደራል ባለሥልጣናት የሲዳማን ክልል ለመፍጠር ቁርጠኛ እንዳልሆኑ ጥርጣሬ የሚያጭሩ ምልክቶችን ታዝቢያለሁ። ከዚህ በመነሳት ባለሥልጣናቱን ባገኘሁ አጋጣሚ በአንድ በኩል ለሕዝቡ ቃል እየገቡ፤ በሌላ በኩል በተቃራኒው መሄድ አደገኛ አንደሆነ ሥጋቴን ገልጫለሁ። አሁን ክልል ለመፍጠር ዝግጁ ካልሆኑ ለአመራሮች፣ ለሽማግሌዎች እና ለሲዳማ ኤጀቶዎች በግልጽ በመንገር ጊዜው እንዲራዘም እንዲያሰምኑ ምክረ-ሐሳብ አቅርቤያለሁ።

በወቅቱ የሕዝብ ተወካዮች ምክር ቤት አፈ-ጉባኤ እና የደሕዴን ሊቀ መንበር ከነበረችው ወይዘሮ ሙፈሪያት ካሚል ጋር ለሁለተኛ ጊዜ ስንገናኝ፤ የሲዳማ ጥያቄ እየጋበዘ ያለውን የጸጥታ ሥጋት በማንሳት ኤጀቶን በማረጋጋት ረገድ መንግሥትን እንዳግዝ ጠየቀችኝ። በወቅቱ «መንግሥት የሲዳማ ክልልን ለመፍጠር ዝግጁ ካልሆነ የውሸት ተሰፋ ከመስጠት ይልቅ አሁን እንደማይቻል በመናገር ጊዜ እንዲሰጧችሁ ጠይቁ›› ብያት ነበር። በእኔ በኩል ኤጀቶ እና የሲዳማ አመራር በትዕግሥት እንዲጠብቁ ለመምከር እንደምጥርም ነገርኳት።

የሲዳማ ዘን እና የኤጀቶን አመራሮች ሳማክራቸው የፌደራል መንግሥት ጊዜ አንዲሰጠው በቅንነት እና በግልጽነት ቢጠይቃቸው ኖሮ ጥሩ እንደነበር፣ ነገር ግን የክልልነት ጥያቄውን ለመቀልበስ ያለመ ሤራ እንዳለ መጠርጠራቸውን ነገሩኝ። የጥርጣረያቸው መነሻ የደቡብ ብሔሮችን ጥያቄ ለማጥናት አንድ የጥናት ኮሚቴ ተቋቁሞ የሐሰት ሪፖርት ማቅረቡን ጠቆሙኝ። የሪፖርቱ ጭብጥም ሲዳማን ጨምሮ ሌሎች ብሔሮች በወቅቱ የነበረው የደቡብ ብሔር ብሔረሰቦች ክልል እንዲቀጥል ይፈልጋሉ የሚል መደምደሚያ እንዳለው ገለጹልኝ። ከሌሎች ምንጮች ሳጣራም የፌደራል መንግሥት የሲዳማ ሕዝብን የክልልነት ጥያቄ ለመቀልበስ ምክንያቶች እያፈላለገ እንደሆነ ግልጽ ሆነልኝ።

የሲዳማን ሕዝብ የክልልነት ጥያቄ ለማክሸፍ ሲካሄድ ከነበረው ፕሮፓጋንዳ አንዱ ሲዳማ ሐዋሳ ከተማን ተቆጣጥሮ ክልል ከሆነ በሌሎች ብሔሮች መካከል ግጭት ይፈጥራል የሚለው ቀዳሚው ነው። ሐዋሳ የደቡብ ክልል መቀመጫ እና የበርካታ ብሔሮች መኖሪያ እንደመሆኗ ሲዳማ ከተቆጣጠራት ከሌሎቹ ከፍተኛ ተቃውሞ ይከተላል ሲባል ነበር። በለውጡ ማግስት በሲዳማ እና በወላይታ ብሔሮች መካከል ግጭት ተፈጥሮ በሐዋሳ እና በሶዶ ከተሞች ከፍተኛ ጉዳት መድረሱ እንደምሳሌ ሲጠቀስ ቆየ። ግጭቱን በመጠቀምም የወላይታ አመራሮች የሲዳማን ጥያቄ እንዲቃወሙ ሲደረግ ነበር።

ይህንን ከተረዳሁ በኋላ በሲዳማ ክልልነት ላይ ያላቸውን ሥጋት ለማቃለል ከሲዳማ እና ከወላይታ የተውጣጡ የተወሰኑ አመራሮችን በማግኘት ወሳኝ በሆኑ ጉዳዮች ላይ ተነጋገረው አንዲተማመኑ አደረግኩ። ይህ የሁለቱ ወገን አመራሮች ሰምምነት በምሥጢር ሰለተከናወነ፤ የወላይታ አመራር እንደበፊቱ የሲዳማን ክልልነት የሚቃወም መሰለ። ደሕዴን የክልልነት ጉዳዮችን ለመወሰን ባደረገው ሰብሰባ ላይ የወላይታ አመራሮች የሲዳማን ጥያቄ በመደገፍ ብሎም አጋርነታቸውን በማሳየት የሲዳማን ሕዝብ የክልልነት ጥያቄ ለማፈን በተለያየ መልኩ የተቀነባበረውን ሤራ አከሸፉ።

በዚህ መልኩ ንትርኩ ቀጥሎ ሳለ ምርጫ ቦርድ በሕገ-መንግሥቱ መሠረት ሕዝበ-ውሳኔ የሚያደርግበት ቀን ተቃረበ። የፌደራል መንግሥት ግን በሕገ-መንግሥቱ መሠረት ሕዝበ-ውሳኔ ከማድረግ ይልቅ ከሲዳማ ሕዝብ ጋር ግብግብ ውስጥ ገባ። ጠቅላይ ሚኒስትሩ የሲዳማን መሪዎች እና ሽማግሌዎች ወደ ፊንፊኔ ጠርተው ሊያሰፈራሯቸው ቢሞክሩም አልተሳካላቸውም። ቀኑ ሲቃረብ ፍጥጫው እና ሥጋቱ ጨመረ። የኤጀቶ መሪዎችን ጠርቼ ቀኑን በትዕግሥት እንዲያሳልፉ እና ወደ ሁከት እንዳይገቡ ልመክራቸው ሞከርኩኝ። የፌደራል ሲቪል እና ወታደራዊ አመራሮችን ሰብስቤ ሊከተል የሚችለውን ግጭት በውይይትና በመናበብ እንዲያሰቀሩ ባደረግኩት ጥረት ውይይታቸው በስምምነት ቢጠናቀቅም ወደ ተግባር አልተቀየረም።

በሕጉ መሠረት ሕዝበ-ውሳኔው መካሄድ የነበረበት ኅምሌ 1 ቀን 2011 ዓ.ም ደረሰ። ኤጀቶ “11/11/11" በሚል መፈክር ሕዝበ-ውሳኔው ተደረገም አልተደረገም ክልል እንደሚመሠርቱ አሰታወቁ። የኤጀቶ አሰተባባሪዎችን በማግኘት ቀኑን እንዲያሳልፉ በመወትወት ለዕለቱ አቅደውት የነበረውን ትዕይንት እንዲሠርዙ ማሳመን ቻልን። መንግሥት ግን "ያለፈቃድ ክልል ሊያውጁ ነው” ብሎ የጦር ኃይል በማሰማራቱ፤ በተፈጠረው ግጭት ከስልሳ በላይ ሰዎች ተገደሉ፤ የዞን አመራሮች ከሥልጣን ተባረሩ፤ የኤጀቶ አስተባባሪዎች በጅምላ ታሰሩ። በኤጄቶ አሰተባባሪነት የሲዳማ ሕዝብ ሲያደርገው የነበረው ትግል ፍጹም ሰላማዊ ሰለነበር፤ የጦር ኃይል ማሠማራት የሚያሰፈግበት ምንም ምክንያት አልነበረም። አንዳሰቡት ክልል ቢያውጁ እንኳን የፌደራሉ መንግሥት እውቅና በመንፈግ ብቻ ሊያከሽፈው ይችል ነበር። በጦር ኃይል እርምጃ መውሰድ የተፈለገው ሕዝቡን አሸማቆ የክልልነት ጥያቄውን እንዲተው ለማስገደድ ቢሆንም አልተሳካም፤ ከጥቂት ወራት በኋላ ኅዳር 10 ቀን 2012 ዓ.ም የሲዳማ ሕዝብ በሕዝበ-ውሳኔ ክልል ለመሆን ቻለ።

ሲዳማ ክልልነትን መጎናጸፉ ለተቀሩት የደቡብ ብሔሮችም መነቃቃትን ፈጠረ። ቀደም ሲል የሲዳማን ትግል በከፍተኛ ሁኔታ ስለደገፍን፤ የወላይታዎችን የክልልነት ጥያቄ የምንቃወም መስሏቸው ነበር። እኛ ግን የማንኛውንም ሕዝብ ራሰን በራሰ የማሥተዳደር መብት የምንደግፈው በመርህ እንጂ ለብቻ የምንደግፈው ብሔር አልነበረም። ከሲዳማ እና ከወላይታ አመራሮች ጋር በነበረን ውይይት ቃል በገባሁት መሠረት ሲዳማ ክልልነቱን አንዳረጋገጠ የወላይታን ትግል ወደ መደገፉ አተኮርኩ። OMN ላይ በቋንቋቸው ፕሮግራም እንዲኖራቸውም አመቻቸን። ልክ እንደ ሲዳማዎቹ ሁሉ፤ ወጣቶች፣ ተቃዋሚዎች እና አሥተዳደር ላይ ያሉት አመራሮች ሳይከፋፈሉ በአንድነት እንዲንቀሳቀሱ መከርን።

እነሱም በአጭር ጊዜ ውሰጥ ሕዝባቸውን ቀስቅሰው እና አደራጅተው የክልልነት ጥያቄያቸው በሁሉም ሕዝብ የሚደገፍ መሆኑን ለማረጋገጥ ትላልቅ ሰልፎችን አዘጋጁ። አሥተዳደሩ እና የዞኑ ምክር ቤት ጥያቄውን በሙሉ ድምፅ አጽድቆ ለፌዴሬሽን ምክር ቤት አሰተላለፈ። የፌደራል አመራር ጥያቄያቸውን አንዲያቆሙ በማባበል እና በዛቻ እያፈራረቀ ቢሞክርም ሰላልቻለ፤ በሰላማዊ ሰልፈኞች ላይ የኃይል እርምጃ በመውሰድና ብዙ ሰዎችን በመግደል፤ የዞን አስተዳዳሪዎችን፣ ምሁራንን እና ወጣቶችን በጅምላ በማሰር ለጊዜውም ቢሆን ጥያቄያቸውን ማዳፈን ቻለ።

## 8.5. ሰላም ለኦሮሚያ

ባለፈው ምዕራፍ ውስጥ እንደገለጽኩት የቄሮ ትግል ተሳክቶ ለውጥ ሲመጣ፣ የኦሮሞን ትግል ስኬት እና ኢትዮጵያ ወደ ዴሞክራሲ የምታደርገውን ጉዞ ሊያደናቅፉ ይችላሉ ብዬ ከገመትኳቸው ጉዳዮች አንዱ ገዢው ፓርቲ የትጥቅ ትግል ሲያካሄዱ የነበሩ ድርጅቶችን የሚያስተናግድበት ሁኔታ ነው። ከእነዚህ ድርጅቶች ጋር በመደራደር፣ የትጥቅ ትግል ትተው በሰላማዊ ፖለቲካ ለመሳተፍ ወደ ሀገር ቤት እንዲመለሱ ማሳመን ሀገሪቷን ወደ ዴሞክራሲ ለማሸጋገር ወሳኝ ጉዳይ ነበር።

ኦነግ እና ኦሕዴድ ለረጅም ጊዜ የጠላትነት ግንኙነት የነበራቸው በመሆኑ፤ እርቅ ወርዶ ተቻችለው በሰላማዊ ፖለቲካ መራመድ ካልቻሉ፤ በኦሮሞ ፖለቲካ ምህዳር ውስጥ ትርምስን በማስፋፋት ለውጡን ያደናቅፋል። አንድ የኦሮሞ ቡድን በሥልጣን ላይ እያለ ሌላ ታጥቆ የሚፋለመው የኦሮሞ ኃይል መኖሩ የኦሮሞን አቅም ያዳክማል። ሀገሪቷም ወደ ጦርነት ተመልሳ፣ የፖለቲካ ምህዳሩ እየጠበበ አዲስ አምባገነናዊ ሥርዓትን ያዋልዳል አልያም ወደ ተራዘመ የእርስ በእርስ ጦርነት ይወስደናል የሚል ሥጋት ነበረኝ።

በለውጡ ሰሞን የኦሮሞ ነጻነት ሠራዊት እንቅስቃሴ በቄለም ወለጋ አካባቢ እየተስፋፋ እንደሆነ ሰለማውቅ በፍጥነት እርቅ ካልተፈጸመ ችግር ይፈጥራል የሚል ፍርሀት አደረብኝ። ለውጡ መጥቶ ጠ/ሚኒስትር ዐቢይ አሕመድ ሥልጣን እንደያዘ የመንግሥት ባለሥልጣናትን በተደጋጋሚ እያነጋገርኩ ከኦነግ አመራር ጋር በፍጥነት ተደራድረው ሰምምነት ላይ በመድረስ ወደ ሀገር እንዲያስገቡ ስማጸን ነበር። ከወታደራዊ፣ ከደኅንነት እና ከፌደራል ባለሥልጣናቱ ጄኔራል ሰዓረ መኮንን፣ ጄነራል ብርሃኑ ጁላ፣ ጄነራል አደም መሐመድ እና ኮሚሽነር ዘይኑ ጀማል ጋር በመነጋገር፤ የምዕራብ ኦሮሚያው አለመረጋጋት እንዳይስፋፋ ጥንቃቄ እንዲደረግ ለማግባባት ሞክሬያለሁ። በሲቪል አመራር በኩል አባ ዱላ ገመዳ፣ ወርቅነህ ገበየሁ እና ብርሃኑ ፀጋይ (በወቅቱ የፌደራል አቃቤ ሕግ የነበሩትን) በማነጋገር፤ በምዕራቡ የሀገሪቱ ክፍል ያለው አለመረጋጋት ከመባባሱ በፊት ከኦነግ አመራር ጋር ሰምምነት ላይ ደርሰው ወደ ሀገር ቤት እንዲመልሱ ደጋግሜ ጠይቄያለሁ። በተጨማሪም በአስመራ የሚገኙትን የኦነግ አመራሮች እንዲሁም ኦሮሚያ ውሰጥ በመንቀሳቀስ የፌደራል መከላከያ አዛዦችን በማነጋገር ግጭቱ እንዳይባባስ ለማድረግ ሞክሬያለሁ። አቶ አዲሱ አረጋ ወደ አሜሪካ በመጣበት ወቅት ስለዚሀ ጉዳይ በዝርዝር ተነጋግረን ወደ ሀገር ቤት ሲመለስ ከሌሎች የመንግሥት አመራሮች ጋር በመመካከር በፍጥነት መፍትሔ እንደሚፈልጉ ቃል ገባልኝ።

ቀደም ሲል እንደገለጽኩት ጠ/ሚኒስትር ዐቢይ እና ለማ መገርሳ ሚኒሶታ በመጡበት ወቅት የተነጋገርንበት ዋናው ጉዳይም ይህ ነበር። ጠ/ሚኒስትር ዐቢይ ቀደም ብሎ ኤርትራ በሄደበት ወቅት ከአቶ ዳውድ ኢብሳ ጋር ተገናኝተው እንደተወያዩ አስታውሶ፤ ከኦነግ ጋር የሚደረገው ሰምምነት በአጭር ጊዜ እንደሚጠናቀቅ ተሰፋ ሰጠኝ። ወዲያውም ለማ መገርሳ እና ወርቅነህ ገበየሁ ይህን ኃላፊነት እንዲወሰዱ አዘዛቸው። በኦነግ አመራሮች ላይም ጫና

ሳደርግ ነበር። በወቅቱ የድርጅቱ ሥራ አስፈጻሚ (ሸኔ ጉሚ) አባል በነበሩት አቶ ኢብሳ ነገዎ በኩል ከሊቀመንበሩ አቶ ዳውድ ኢብሳ ጋር ተወያይተናል። አቶ ዳውድም ከመንግሥት ጋር ተወያይተው መግባባት ላይ ከተደረሰ ወደ ሀገር ለመመለስ ፈቃደኛ መሆናቸውን አረጋገጠልኝ። ከጠ/ሚኒስትር ዐቢይ ጋር ሲገናኙ ዝርዝር ጉዳዮችን በወጉ ማውራት እንዳልቻሉና ሌላ ልዑክ ለመላክ ቃል በመግባቱ ያንኑ እየጠበቁ እንደሆነም ገለጸልኝ። ወደ ሀገር ቤት እንደተመለስኩ አቶ ለማ መገርሳ እና ወርቅነህ ገበየሁ ወደ አሰመራ ሄደው ከኦነግ አመራሮች ጋር በመወያየት ኦነግ ወደ ሀገር ቤት በሚገባበት ሁኔታ ላይ ስምምነት ላይ መደረሱን አሰታወቁ።

በዚህም መሠረት በአቶ ኢብሳ ነገዎ የተመራ የልዑካን ቡድን ቀደም ብሎ ወደ ፊንፊኔ በመምጣት ለቀረው አመራር አቀባበል በሚደረግበት ሁኔታ ላይ ዝግጅት ማድረግ ጀመረ። ቀኑ እየተቃረበ ሲመጣ ቄሮዎች አቀባበሉን ለማሳመር የትግሉን ባንዲራ ፊንፊኔ ውሰጥ መስቀል ሲጀመሩ የተደራጁ ቡድኖች ሁከት ፈጠሩ። ከዚሀም አልፎ በአቀባበል ሥነ-ሥርዓቱ ዋዜማ ወደ ከተማዋ የሚያቀኑ ወጣቶችን መንገድ ላይ መግደል እና ለአቀባበል የሚመጣውን ሕዝብ የሚያዳጉዙ ተሽከርካሪዎችን መሰባበር ጀመሩ። ከጥቂት ሳምንታት በፊት የአርበኞች ግንቦት ሰባት ቡድን ወደ ሀገር ሲገባ ከተማዋ በእነሱ ባንዲራ እና ዓርማ ሰትሞላ ማንም ሰላልነካቸው፤ የኦነግ ሲሆን ጥቃት መድረሱ የኦነግ ደጋፊ ያልሆነውን ኦሮሞ ጭምር አሰቆጣ።

በከተማዋ ያለው ሁከት ስለተባባሰ ወደ ድሬደዋ ላደርገው የነበረውን ጉዞ ሰርዤ፤ ግጭቱን ማረጋጋት ላይ ከሚመለከታቸው አካላት ጋር ለመሥራት ወሰንኩ። ሁከት ፈጣሪዎቹ ወደ ፊንፊኔ የሚወሰዱትን መንገዶች በሙሉ ዘግተው ወደ ከተማዋ የሚገባውን ሕዝብ ሲያጠቁ ሰለነበር፤ ቀድሞ ለመምጣት እቅድ ያልነበራቸው ቄሮዎች ከሁሉም ዞኖች ወደ ፊንፊኔ በማቅናት ኃይል እንዲጨመር ተደረገ። የፌደራል የጸጥታ አካላትን በማነጋገር ሕዝቡን የሚያጠቁትን ቡድኖች በመቆጣጠር መንገዱን ካልከፈቱ ቄሮ ሰብሮ ለመግባት እንደሚገደድ አቋማችንን ገለጽን። ቄሮ ወደ ከተማዋ ገብቶ ሊረብሽ ይችላል የሚል ፍርሀት እንዳላቸው ሲነግሩኝ፣ ምንም ኮሽታ እንደማይኖር እና ኃለፊነት እንደምወሰድ አሳወቅኳቸው። በዚህም መሠረት የሀገር መከላከያ ሠራዊት መንገዱን ከፍቶ ቄሮዎች ወደ ከተማዋ እንዲገቡ ሁኔታዎችን አመቻቸ። ቄሮዎቹ ምንም ችግር ሳይፈጥሩ በመስቀል አደባባይ ተሰበሰቡ።

በአቶ ዳውድ የሚመራው የልዑካን ቡድን መስከረም 5 ቀን 2011 ዓ.ም ከአሰመራ ተነሰቶ ከጠዋቱ 12፡00 ሰዓት ይደርሳል ቢባልም ዘግይቶ ከቀኑ 6፡00 ላይ ደረሰ። ከየዞኖቹ ብዙ ርቀት የተጓዙት ቄሮ እና ቀሬ ፀሐይ እና ሀሩሩ ሳይበግራቸው ውጪ አድረው ጠበቁ። እኛም ከአቶ በቀለ ገርባ እና ከፕሮፌሰር ሕዝቅኤል ገቢሳ ጋር በመሆን ልዑካኑ እሰኪመጡ ድረሰ በትዕግሥት እንዲጠብቁ አበረታታናቸው። ከዚያም አቶ ዳውድን ከልዑካን ቡድኑ ጋር በቦሌ አየር ማረፊያ ተቀብለን ወደ መሰቀል አደባባይ አመራን። በነበረው አለመረጋጋት ምክንያት ከተማዋ ከፍተኛ ውጥረት ውሰጥ ሰለነበረች ከዝግጅቱ በኋላ ግጭት ሊፈጠር ይችላል የሚል ሥጋት ቢኖርም ዝግጅቱ ረጅም በመሆኑ ሕዝቡ ቀስ በቀስ እየተበተነ ወደ ቀዬው በሰላም ገባ። ማምሻውን ጄነራል ሰዓረ እና ኮሚሽነር ዘይኑ ጀማል ዝግጅቱ በሰላም መጠናቀቁ እንዳሰደሰታቸው ደውለው ነገሩኝ።

ኦነግ ወደ ሀገር ከተመለሰ ከአንድ ሳምንት በኋላ በአበራ ቶላ አማካኝነት እኔ እና አቶ ዳውድ በድጋሚ ተገናኘን። አቶ ዳውድም «Bygones are bygones» ብሎ ጨበጠኝና

የቀድሞ ልዩነቶቻችንን ትተን ይህንን ሽግግር ስኬታማ ለማድረግ እና የኦሮሞን ትግል ወደፊት ለማራመድ እንድንሠራ ሐሳብ አቀረበ:: ጥሩ ሐሳብ መሆኑን ገልጬለት ተስማማን።

ከአነሱ አንድ ወር ተኩል ቀድሜ ወደ ሀገር ቤት ገብቼ ሰለነበር የሀገሪቱን ሁኔታ እና ሰለ ጠ/ ሚኒስትር ዐቢይ አሕመድ የአመራር አካሄድ ያለኝን ግንዘቤ፣ ተሰፋ እና ጥርጣሬ ጨምሬ ነገርኩት። አቶ ዳውድም በአስመራ ከተማ ከአቶ ለማ እና ወርቅነህ ገበየሁ ጋር ስለተደረገው ውይይት እና ሰምምነት ነግሮኝ፤ የተገባው ቃል ካሁኑ እየተጣሰ መሆኑንና ይህም የባሰ ችግር ሊፈጥር እንደሚችል ሥጋቱን አጋራኝ። መንግሥት ስምምነቱን ከጣሰበት መንገድ አንዱ በሰላም ወደ ሀገር ገብቶ የነበረው የኦሮሞ ነጻነት ሠራዊት ያለበት ሁኔታ ጥሩ አለመሆኑና የድርጅቱ አመራር ሠራዊቱን ሊጎበኝ ቢሞክርም እንዳልተሳካ ነገረኝ። በምዕራብ ኦሮሚያ ስለሚንቀሳቀሰው የኦነግ ሠራዊት ሁኔታ ሰጠይቀው አስመራ ላይ ከመንግሥት ጋር ተወያይተው እንዲገቡ መስማማታቸውን፤ ነገር ግን አስቀድሞ ከኤርትራ መጥቶ መንግሥት ካምፕ ያለው ጦር አያያዙ ጥሩ ሰላልሆነ ጫካ የቀረውን አሳምኖ ለማስገባት አስቸጋሪ አንደሆነ ጨምሮ ነገረኝ።

ከአቶ ዳውድ የሰማሁትን ቅሬታ ለፕሬዝዳንት ለማ መገርሳ፣ ለጄነራል ብርሃኑ ጁላ እና በወቅቱ የሀገሪቱ የሰላላ ቢሮ ምክትል ዳይሬክተር ለነበረው ደምመለሽ ገ/ሚካኤል ነግሬያቸው በፍጥነት ለመፍታት ቃል ገቡ። ለማ በቃሉ መሠረት ከመንግሥት እና ከኦነግ የተውጣጣ የጋራ ኮሚቴ ማቋቋማቸውን ከጥቂት ጊዜ በኋላ አሳወቀኝ። ይህንን ከኦነጉ አቶ ኢብሳ ነገዎ ማረጋገጥ ብችልም፤ በጥቂት ሳምንታት ውስጥ ግን ከሁለቱም ወገኖች ቅሬታ መሰማት ጀመረ። በኦነግ በኩል ከኤርትራ የተመለሱ ወታደሮች አያያዝ እየተባባሰ ሰለመምጣቱ፤ ጉለሌ ያለው የድሮ ቢሯቸው አለመመለሱን ጨምሮ ሌሎች በአስመራ የተደረሱ ስምምነቶች እንዳልተፈጸሙ ቅሬታቸውን ዘረዘሩ። በመንግሥት በኩል ደግሞ የኦነግ ሠራዊት በምዕራብ ኦሮሚያ የሚገኙ የጸጥታ ኃይሎችን በመግደል እና ትጥቅ በማሰፈታት የመንግሥትን መዋቅር በማፈራረስ ላይ እንደሚገኝ ክስ ቀረበ። ከዚህ በላይ እንደማይታገሱም አሰጠነቀቁ።

በመንግሥት እና በኦነግ መካከል አተካሮው ውሎ አድሮ እየተባባሰ ሄደ። በምዕራብ ኦሮሚያ የተቀሰቀሰው አለመረጋጋት ከዕለት ወደ ዕለት የሰው ሕይወት እና ንብረት ማውደሙን ቀጠለ። እንቅሰቃሴው ወደ መሀል ሀገርም መታየት ጀመረ። በዚህ ጊዜ የሀገር ሽማግሌዎች ተሰብሰበው መንግሥትን እና ኦነግን አነጋገሩ። ኦነግ ጫካ የቀረውን ሠራዊት ለማስገባት ፈቃደኛ ያልሆነው ቀድሞ የገባው ሠራዊት ኢ-ፍትኃዊ በሆነ መንገድ ሰለተያዘ እንደሆነ ተናገረ። አቶ ዳውድ ራሱ ወደ ምዕራብ ኦሮሚያ ሄዶ ጫካ የቀረውን ጦር አዛዥ ጃል መሮን አግኝቶ ማነጋገሩን እና መንግሥት የአስመራውን ሰምምነት በመጣሱ ምክንያት ለመግባት ፈቃደኛ እንዳልሆነ ገለፀ። ከዚህ በመነሳት የሀገር ሽማግሌዎች ጃል መሮን ለማሳመን ወደ ወለጋ አመሩ።

ነገር ግን የሽማግሌዎቹ ተልዕኮ እንዳይሳካ ገና በማለዳው ሤራዎች መጠንሰሰ ጀመሩ። ሽማግሌዎቹ ነቀምቴን እንኳን ሳያልፉ እንዲሁም የአነግን ጦር ሳያገኙ ጦሩ ጥቃት ፈጽሞባቸዋል የሚል ዜና በመንግሥት አካላት መሰራጨት ጀመረ።

የኦነግ ደጋፊዎች ደግሞ የሀገር ሽማግሌዎቹ "የመንግሥት ተላላኪዎች ናቸው" የሚል የፕሮፓጋንዳ ዘመቻ በመክፈት በተለያዩ ቦታዎች መንገድ ላይ ያሰቆሟቸው ጀመር። ይሀን በመፍራት አንዳንድ ሽማግሌዎች ወደኋላ ተመለሱ። የተቀሩት በወ/ሮ መኪያ ማሙዮ እና በአቶ ኃይሌ ገብሬ አየተመሩ ከአስቸጋሪ ጉዞ በኋላ ጃል መሮ ጋር ደርሰው አነጋገሩት።

ከዚያ ሲመለሱ ጃል መሮ ለሰላም ፍላጎት እንዳለው እና መንግሥት ማሟላት ያለበትን ቅድመ ሁኔታዎች እንዳሰቀመጠ ተናገሩ። ከዚሀ በመቀጠል የመንግሥት እና የኦነግ አመራሮች ተነጋግረው ጉዳዩን በፍጥነት እንደሚጨርሱ ቃል ገቡ። ከዚሀ ሁሉ በኋላም ግን ምንም የሚጨበጥ ነገር ጠፋ፤ መንግሥት ለኦነግ ጥያቄዎች ምለሽ ለመስጠት ቃል ቢገባም በተጨባጭ ለማሳየት ተዳተተ። የኦነግ አመራሮችም ሠራዊቱ እንዲገባ ያላቸውን ፍላጎት በቃላት ቢገልጹም በተግባር ግን ተቃራኒውን ሲሠሩ ነበር።

አቶ ዳውድ ኢብሳ ከአንድ ሚዲያ ጋር ባደረጉት ቃለ-ምልልሰ ሰለ ትጥቅ መፍታት ተጠይቀው «ማነው ፈቺ? ማነው አስፈቺ?» ብለው መናገራቸው መንግሥትን እጅግ ስላስቆጣ በባለሥልጣናት እና በካድሬዎቹ በኩል ፕሮፓጋንዳው ተጠናክሮ ቀጠለ። ኦነግ ከሚለው ሰም ይልቅ "ሸኔ" የሚለውን ቃል በመጠቀም በማያባራ እርግማን ዘመቻው ተጧጧፈ። በተለይ አዲሱ አረጋ፣ ታዬ ደንደዓ እና ሚልኬሳ ሚደጋ ለያዥ ለገናዥ አስቸገሩ። የኦነግ ደጋፊዎች በበኩላቸው ATM (Addisu, Taye, Milkessa) የሚል ምህፃረ ቃል በመለጠፍ ከአነሱ ጋር ውዝግቡን ገፉበት። ነገሮችን አለዝበ ለማስታረቅ የተደረገው ሙከራ ተመናመነ። በምዕራብ ኦሮሚያ አለመረጋጋቱ ተስፋፍቶ የዜጎች ግድያ እና የንብረት ውድመት የዕለት ተዕለት አሳዛኝ ክሰተት ሆነ።

ችግሩ እየተባባሰ ሲሄድ እኔ እና በቀለ ገርባ ሁኔታውን በአካል ተገኝተን ለማየት ወደ ወለጋ ለመጓዝ ወሰንን። ይሀንን ሐሳብ ስናነሳ ብዙ ሰዎች ከእኛ ጋር እንደሚሄዱ ቃል ገብተው የነበረ ቢሆንም የመሄጃው ቀን ሲደርስ ከጠባቂዎቻችን እና ከወጣቶች በቀር ሌሎቹ የውኃ ሽታ ሆኑ። እኛም እንዳንሄድ ብዙ ምክሮች እና ማሰጠንቀቂያዎች ደረሱን። አንድ የመንግሥት ባለሥልጣን ደውሎ "ሸኔ" ለመግደል ካቀዳቸው ዋና ዋና ሰዎች ውሰጥ አምሰተኛ ላይ እንደሆንኩ ነገረኝ። እኔም «ወደ 1ኛ ደረጃ እሰክጠጋ ድረሰ የሕዝቡን ችግር ሄጄ አያለሁ» በማለት አቋሜን በቀልድ አሰመስዬ ነገርኩት።

በዚሀ ሁኔታ ከፊንፊኔ ወጥተን፣ ነቀምቴ ደርሰን አድርገን፣ በነጋታው ከሕዝቡ ጋር ለማድረግ ያቀድነው ውይይት እንዳይሳካ የመንግሥት እና የኦነግ ደጋፊዎች ከፍተኛ ጥረት እያደረጉ እንደሆነ ሰማን። እኛንም በማስፈራራት ሕዝቡን እንዳናነጋግር ለመከልከል የተለያየ ሙከራ ማድረጋቸውን ቀጠሉ። ሊገድሉን የተዘጋጁ ሰዎች ሰላሉ ስብሰባ እንዳናደርግ መከሩን። በማግስቱ ጠዋት ስንነሳ ሕዝቡን እንዳናናግር የተሸረበውን ሤራ በተጨባጭ አየን። አንድ ቡድን ሕዝቡን ሰታዲየም ውስጥ ለማናገር ማቀዳችንን በመንገር ሕዝቡን ወደዛው ጋበዘ። ሌላ ቡድን ደግሞ ወደ ከተማዋ የስብሰባ አዳራሽ ጠራ። የተፈጠረውን ብዥታ ለማጥራት ሁለቱም ቦታዎች ለመሄድ ወሰንን። መጀመሪያ ወደ ስታዲየም ጎራ ብለን እዚያ የተሰበሰቡትን ወጣቶች ካነጋገርን በኋላ ወደ አዳራሽ አመራን። አዳራሹ ጋ ሰንቃረብ ሕዝቡ በጣም በመብዛቱ እና ጥቂት ወጣቶች ረብሸው መፈተሽ ባለመቻሉ፣ ታዳሚው ሳይፈተሽ ገብቶ አዳራሹ መሙላቱ ተነገረን። በቦታው የነበረ የፖሊስ አዛዥ ለእኛ ደኅንነት አሰተማማኝ ስላልሆነ እንዳንገባ መከሮን፤ ለሚደርስብን አደጋ ፖሊሰ ኃላፊነት እንደማይወሰድ አስጠነቀቀን።

በዚሀ ወቅት በቀለ ገርባ ወደኔ ዞሮ ሲያየኝ ወደ ውሰጥ ለመግባት እንደወሰንኩ ተረዳ። «ዕድሜህ ስንት ነው?» ሲለኝ፤ «ሠለሳ ሦስት» አልኩት። ቀጥሎ «ስንት ልጆች አሉሀ?» ብሎ ሲጠይቀኝ፣ «አንድ» ስል መለስኩለት። «እኔ ሰልሳ ዓመት ኖሬያለሁ፤ አራት ልጆችም ወልጃለሁ፤ ብሞትም ምንም አይደለም። ይብላኝ ላንተ!» ብሎ ቀለደና ተያይዘን ከመኪናው ወረድን። ከሕዝቡ

ጋር እየተጋፋን ወደ አዳራሹ ገብተን መድረኩ ላይ ጉብ አልን። የዞንና የከተማ አሥተዳደሩን ካለበት አፈላልገን በማስመጣት ከእኛ ጋር እንዲቀመጥ አደረግን።

አጭር የመክፈቻ ንግግር ካደረግን በኋላ ሕዝቡ ባለው ችግር ላይ ሐሳቡን እንዲያካፍለን መድረኩን ክፍት አደረግን። ተሳታፊዎቹ በየተራ እጃቸውን እያወጡ ተናገሩ። የኦነግ ሠራዊት ደጋፊ የሆኑ ወጣቶች ተደራጅተው እንደመጡ ከሚያነሱት ጥያቄዎች እና ሐሳቦች መገንዘብ ይቻላል። አብዛኛው አስተያየት እኛ የምንሰብከውን ሰላም የሚቃወም እና የኦሮሞ ነጻነት ሰራዊትን የሚያሞካሽ ነበር። ከፊት የተቀመጡት ሽማግሌዎች ግን ከመናገር መቆጠብን መረጡ። መናገር ለፈለገ ሰው ሁሉ የቻልነውን ያህል ዕድል ሰጠን፤ ማንኛውንም ጉዳይ የፈለጉትን ያህል ጊዜ ወስደው እንዲናገሩ ፈቀድንላቸው። ይህን ያደረግነው ሕዝቡ ብሶቱን አውጥቶ እንዲያወራ ስለፈለግን ነበር። በርካታ ሰዎች ከተናገሩ በኋላ መልስ ለመስጠት ወሰንን። በተነሱት ጥያቄዎች ላይ በሹክሹክታ ከተወያየን በኋላ ተከፋፍለን መልስ ወደ መስጠቱ ገባን።

በቀለ ገርባ ትንሽ ወደ መንግሥት አዘንብሎ ሕዝቡን እንዲመክር፤ እኔ ደግሞ ለኦነግ ወግኜ በመንግሥት ላይ ጫና በሚያደርግ መልኩ እንድንሄድ ተሰማማን። በዚህም መሠረት በቀለ ሕዝቡ የኦሕዴድን መንግሥት እስከ ምርጫው ድረስ እንዲታገስ ተማጸነ። እኔ በበኩሌ ሕዝቡ እና የኦነግ ሠራዊት አውነት እንዳላቸው በመመስከር፣ መንግሥት እና ኦነግ በፍጥነት መፍትሔ እንዲፈልጉ አሳሰብኩ።

በዚያ ሰብሰባ ላይ ብዙ አሥቂኝ እና አሰገራሚ ነገሮች ተከሰተዋል። በቀለ «አሁን ሥልጣን ላይ ያሉት ሰዎች ኦሕዴድም ቢሆኑ ወንድሞቻችሁ ናቸውና እንድትታገሷቸው በአግዚአብሔር ስም እማጸናችኋለሁ» ሲል፤ ከተሰብሳቢው መሀል አንዱ «ሰለ አግዚአብሔር መስማት ብንፈልግ ወደ ቤተ-ክርሰቲያን እንኄድ ነበር። እዚህ የመጣነው ከእናንተ የፖለቲካ መፍትሔ ለመፈለግ ነው። የፈጣሪን ጉዳይ ተዉና ፓለቲካዊ መፍትሔ ንገሩን›» ብሎ ሲናገር ቤቱ በሣቅ ተሞላ። በፊተኛው ረድፍ ላይ ከተቀመጡ አንጋፋ ሰዎች አንዱ ብዙ ጊዜ እጅ ቢያወጣም ዕድል አላገኘም። በኃላ አይቼ ዕድል ሰጠሁት። እሱም «ኦሕዴድ ትርፍ አንጀት ነው። ትርፍ አንጀት ካልተቆረጠ አይድንም። ኦሕዴድን ለማጥፋት እንጂ ለመፈወሰ አትድከሙ» ሲል በቁጣ ተናገረ። ሰውዬው ዶ/ር ፊሌ እንደሚባል እና ኦሕዴድ በብረት አስሮ ለብዙ ዓመታት ሲያሰቃየው እንደቆየ በቀለ ኋላ ላይ ነግሮኛል።

ነቀምቴ በሄድንበት ወቅት በቤንሻንጉል ጉሙዝ እና በኦሮሚያ ድንበር አካባቢ በተፈጠረ ግጭት ብዙ ሰዎች ተፈናቅለው ኡኬ በተባለ ቦታ መስፈራቸውን ስለሰማን ወደዛው አመራን። ኡኬ ከነቀምቴ ከተማ ወደ ሠላሳ አምሰት ኪሎ ሜትር ርቀት ላይ ትገኛለች። እዚያም ከዓመታት በፊት ለሰፈራ ከሐረርጌ ወደ አካባቢው ተሰደው የነበሩና በወቅቱ በግጭት ምክንያት የተፈናቀሉ ሰዎችን አነጋገርን። የተፈናቃዮቹ ችግር አሳሳቢ መሆኑን ተረድተን ወደ ፊንፊኔ ሰንመለሰ መንግሥት እና ግብረሰናይ ድርጅቶች ትኩረት እንዲሰጧቸው ለማሰተባበር ቃል ገባን።

ክኡኬ ሰንመለስ እየመሸ ሰለነበር በዚያ ሰዓት ወደ ጊምቢ መሄድ አደገኛ እንደሆነና በነቀምቴ እና በጊምቢ መካከል ያለውን የአባ ሴና ተራራ በምሽት ይቅርና በቀን እንኳን ማቋረጥ አንደሚያስፈራ ተነገረን። እኛ ግን ጊምቢ ሄደን ለማደርና ጠዋት ሕዝቡን ለማነጋገር ወሰንን። በዚሀ ጊዜ ጥበቃ ሲያደርጉልን የቆዩት የሀገር መከላከያ ሠራዊት እና ፓሊሶች አብረውን

ሊሄዱ እንደማይችሉ አሳወቁን። እኛም ችግር የለውም ብለን ከነቀምቴ ወጥተን ወደ ጊምቢ አቀናን። ዲዴሳ ወንዝ ስንደርስ ወንዙ አጠገብ ወደተሰራ ሪዞርት ጎራ ብለን እራት በልተን ወንዙ ውሰጥ ታጠብን። በዚያ ገነት በሚመሰል ቦታ ላይ የተሠራው አሰደናቂ ሪዞርት በሁከቱ ምክንያት ኦና ሆኖ መታየቱ የጸጥታው ችግር ምን ያህል ኢኮኖሚውን እየጎዳው እንደሆነ ያመለክታል። እራት በልተን ስንነሳ ሁለት ሰዓት አልፉል፤ ከአሁን አሁን የተፈራው አደጋ አጋጠመን ብለን እንዲሁ ሰናማትር አለፍነው። በጉዟችን ላይ ያየነው ከዋሉበት ወደ ቤታቸው ለመግባት ያለፍርሀት በእግራቸው የሚኳትኑ ሴቶች እና ሕጻናትን ነበር።

የአባ ሴና ተራራን የሚያቋርጠው መንገድ በገነት መሀል የሚወስድ ጎዳና ይመስላል። በማንጎ የተሞላው ጫካ ከሩቅ ያውዳል። በዕለቱ ካሳዘነኝ ነገር አንዱ ከነቀምቴ ገዝተን የምንጠጣው የማንጎ ጁስ በአረብ ሀገር የተመረተ መሆኑ ነው። እኛ ግን በሰሎ መሬት ላይ የወደቀና እየበሰበሰ ያለ ማንጎ መሀል እያቆራረጥን አለፍን። ፈጣሪ የሰጠንን ሀብት መጠቀም ባለመቻላችን፤ ወደ ውጭ መላክ በሚችል መሬት ላይ ከውጭ የገባ ማንጎ እየጠጣን መሄዳችን በእጅጉ ያሳፍራል።

ጊምቢ ስንደርስ ከተማዋ ጸጥ ረጭ ብላለች። መብራት የለም፤ ሰው በመንገድ ላይ ሲንቀሳቀስ አይታይም። ባረፍንበት ሆቴል ውስጥ ጥቂት የውጭ አገር ሰዎች እና የማዕድን ባለሙያ የሆነ የአካባቢው ተወላጅ ኢንጂነር ብቻ ነበሩ። ልጁ እራት ጋብዞን ስናወራ ነጋዴ የሆኑ እና የተሻለ ገቢ ያላቸው ሰዎች በሙሉ ከተማዋን ለቀው መውጣታቸውን ነገረን። እሱ ግን ፊንፊኔ እንደሚኖር፣ ከጃፓን እና ከሌሎች ሀገር ዜጎች ጋር ማዕድን ለማውጣት ጥናት ላይ እንደሚገኝ ነገረን። ሌላው ሰው አካባቢውን ትቶ ሲሸሽ እሱ ለምን እንደመጣ ስጠይቀው «እኛ የተማርነው እና ሀብት ያካበትነው በሙሉ ከዚህ ሕዝብ ሸሸን ማለት ሕዝቡ ተሰፋ ይቆርጣል። እዚህ ያለሁት ተሰፋ ልሰጣቸው ነው›› አለኝ። ልጁ ብዙም ሳይቆይ ከእነዚያ የውጭ አገር ሰዎች ጋር በአንድ መኪና ሲጓዙ በሚዘገንን ሁኔታ ተገደለ። ወገኔን ጥዬ አልሸሽም ያለው ብቸኛው ምሁር በዚያ መልኩ መገደሉ የአካባቢው ሁከት እያንዣበበ ላለው ከባድ ችግር ማሳያ ነበር።

በማለዳው የመንግሥት አሠተዳዳሪዎችን ማፈላለግ ጀመርን። የዞኑ (የምዕራብ ወለጋ) አመራሮች ሸሽተው ፊንፊኔ ገብተው እንደነበር ሰማን። የከተማውን ከንቲባ ስንጠይቅ ያለበትን የሚያውቅ ሰው ጠፋ። ባለፉት ሦሰት ወራት ሦስት ከንቲባዎች ተሹመው ሁሉም በሚደርሰባቸው ዛቻ በጥቂት ቀናት ውሰጥ ጥለው መጥፋታቸው ተነገረን። በኋላ ላይ ከቀናት በፊት የተመደበውን ከንቲባ የሚያውቅ ሰው አግኝተን ከእኛ ጋር ሕዝባዊ ሰብሰባ ላይ እንዲሳተፍ ጋበዝነው። አዳራሽ ስንደርሰ ሕዝቡ ተሰብሰቦ እየጠበቀን ነበር። ከሕዝቡ አስተያየት እየተቀበልን እያለ የከተማው ከንቲባ «አዳራሹን ሞልተው ከምታያቸው በመቶዎች የሚቆጠሩ ወጣቶች መካከል ሥራ ያላቸው ከሀያ አይበልጡም። ይሀ የፖለቲካ ችግር በፍጥነት ካልተቀረፈ እና የሥራ ዕድል ካልተፈጠረ ወጣቱ መሣሪያ አንሰቶ ወደ ጫካ ከመግባት ውጭ አማራጭ የለውም›› ብሎ በጆሮዬ ሹክ አለኝ። የእሱ ትንቢት ሳይዘገይ ተፈፀመ።

ቀጥሎ ከጊምቢ ወደ ነጆ አመራን። ነጆም ሕዝቡ አንድ ሰፊ ሜዳ ላይ ተሰብሰቦ ጠበቀን። በቀለ ገርባ እዚያ አቅራቢያ ሰለተወለደና ቀደም ሲል ያሰተማረበት ከተማ ሰለሆነ ወዳጅ ዘመዶቹን ጨምሮ ብዙ ሰዎች ተገኝተዋል። ለሕዝቡ ስለ ሰላም አሰፈላጊነት ተናግረን እና ቅሬታቸውን ሰምተን ወደ ሆቴል አቀናን። በሆቴሉ የሀገር ሽማግሌዎች መጥተው እራት ጋብዘውን ወጣቶች እና ሚዲያ በሌለበት ከእኛ ጋር አወሩ። በከተማዋ የመንግሥት አሠተዳደር መፍረሱን እና ሥርዓት አልበኝነት ከባድ ችግር እንደሆነ ደጋግመው ተናገሩ። በኦነግ እና በመንግሥት መካከል

የተፈጠረው የፖለቲካ አለመግባባት በአስቸኳይ እልባት አግኝቶ ጫካ ያሉት እንዲመለሱና የአሥተዳደር ሥርዓቱ መልሶ እንዲዘረጋ ለመንግሥት እና ለኦነግ አመራሮች እንድንነግራቸው አደራ አሉን። ነጆ ከመድረሳችን በፊት ከተማዋ በሰፈረው የሀገር መከላከያ ሠራዊት ላይ ጥቃት ደርሶ ሠራዊቱ በወሰደው የአፀፋ ተኩስ ወጣቶችን በመግደሉ፣ ሠራዊቱ መሀል ከተማ በመሰፈሩና ንጹሀን ዜጎች ላይ ጉዳት በመድረሱ የሀገር ሽማግሌዎች ቅሬታ አሰሙ። ቅረታውን ይዘን የአካባቢውን የሀገር መከላከያ ሠራዊት የጦር አዛዥ አነጋገርን። እንኳን ሲቪሉን ሰው፣ ታጥቀው ጫካ ያሉትን ልጆች እንኳ የማጥቃት ፍላጎት እንደሌላቸውና የከተማውን ካምፕ ለቀው እንደሚወጡ ቃል ገባልን። የሀገር መከላከያ ሠራዊት አዛዦችም ልክ እንደ ሀገር ሽማግሌዎቹ መንግሥት እና ኦነግ የፖለቲካ አለመግባባቱን በፍጥነት እንዲፈቱ እና ግጭቱን እንዲያቆሙ አሳሰቡ።

ከነጆ ወደ ደምቢ ዶሎ አመራን። ጉሊሶ ላይ ወደ አንድ ቤተሰብ ቤት ጎራ ብለን ቁርስ በላን። አዚያው እያለን ከፊንፊኔ አብሮን የመጣው የቤተሰቡ ልጅ ስልክ ተደውሎለት እኛን በማስተናገዱ ዛቻ ደረሰው። ቤተሰቡ ግን እኛን ማስተናገዳቸውን ቀጠሉ። ከቁርሰ በኋላ በመንገድ ላይ የተሰበሰበውን ሕዝብ አነጋገርን። ጉሊሶ ቀደም ሲል የቄሮ ትግል ከተቀጣጠለባቸው ከተሞች መካከል ሰትሆን ከፍተኛ መሥዋዕትነት የተከፈለበት ቦታ ነው። ያን ታሪክ እያወሳን አመስግነን ወደ ደምቢ ዶሎ አመራን።

ደምቢ ዶሎ ስንደርሰ ታሪካዊቷ ከተማ ባዶ ሆና ጠበቀችን። ሁሉም መንገዶች ጭቃማ ነበሩ፤ የከተማዋ ነዋሪዎች ዓይኖች ላይ ፍርሀት ይነበባል። በሰታዲየም የተሰበሰበውን ሕዝብ አዳራሽ ወስደን ተወያየን። ከወረዳዎች የመጡት በንዴት ይናገሩ ነበር። «የመጣችሁት የኦሮሞ ነጻነት ሠራዊትን ትጥቅ አሰፈትታችሁ ልታሰገቡ ነው። ሠራዊቱ አይገባም እናንተ ራሳችሁ ተቀላቀሏቸው›› የሚሉ ብዙ ነበሩ። ሽማግሌዎቹን ግን እንደ ነጆ እና መንዲ ሁሉ፤ ለብቻ ወስደው እርቅ ወርዶ ጦርነቱ ቢቆም ጥሩ ነው በማለት አሳሰቡ።

ከደምቢ ዶሎ በኋላ ወደ መንዲ ስንደርስ የከተማዋ መግቢያ መንገድ በወደቀ ዛፍ ተዘግቶ ጠበቀን። ሊቀበሉን የመጡ ፖሊሶች መክፈት ፈርተው ቆመው አገኘናቸው። ከመኪናው ወርደን የዛፍ ግንድ ቆርጠን ማንሳት ሰንጀምር መጀመሪያ በዓይነ ቁራኛ ሲተያዩ የነበሩት ፖሊሶች እና ወጣቶች መጥተው ሰለረዱን መንገዱን ከፍተን አለፍን። አንድ ፖሊስ «ቄሮ ያሰተማርከውን መልሶ አንተው ላይ ደገመው›› ብሉ ቀለደብኝ።

ከመንዲ ሕዝብ ጋር ሰፊ ውይይት አደረግን። እዚሀም የሀገር ሽማግሌዎችን እና የሀይማኖት አባቶችን ነጥለን አነጋገርን። አንድ አዛውንት «ጀዋር እባክሀ፣ ጫካ ያለው እኛ ጋር ብቻ ነው? በሌሎች የኦሮሚያ ቦታዎች የለም? ጦርነቱ እኛ ጋር ብቻ ለምን ሆነ ትግል መቀጠል ካለበት በቄር ዘመን እንደነበረው መላው ኦሮሚያ በጋራ መታገል፤ ጦርነት የሚቆምም ከሆነም አንድ ላይ መቆም አለበት›› የሚል ሐሳብ አሰተላለፉ።

በመንዲ ከተማ ባደረግነው ውይይት ዋናው ቅሬታ ከቤንሻንጉል ጉሙዝ ጋር በተፈጠረው የድንበር ግጭት በደረሰው ጉዳት ላይ ያተኮረ ነበር። ክፊንፊኔ ወደ አሶሳ የሚወስደው ዋናው መንገድ በግጭቱ ከተቋረጠ ወራትን እንዳሰቆጠረ ነገሩን። በዚሀ ምክንያት የመንዲ ሕዝብ ወደ አሶሳ ማለፍ አልቻለም ነበር። የቤኒሻንጉል ጉሙዝ ነዋሪዎችም ከአሶሳ ተነሰተው ካማሺ ወደምትባል ዞናቸው ለመድረሰ በመንዲ በኩል ማለፍ ስላለባቸው፤ በግጭቱ ሳቢያ ካማሺ ከክልሉ ዋና ከተማ መቆራረጧን ለማወቅ ቻልን።

ከፊንፊኔ ስንነሳ መንዲን ለማለፍ እቅድ አልነበረንም። ስለሰማነው አሰከፊ የድንበር ግጭት ጉዳይ የቤኒሻንጉል ጉሙዝ ክልል አመራር እና ሕዝቡን አማክረን ለችግሩ መፍትሔ ለመፈለግ ወደ አሶሳ ለመሄድ ወሰንን። የዳቡሰን ወንዝ አቋርጠን ወደ አሶሳ ስናቀና መንገዱ ጭር ብሏል። አንድ መኪና ጎማው ተንፍሶ መሀል ላይ ቆመን ሰለነበረ የገጠሩ ሕዝብ እኛን ለማየት ወደ መንገዱ ቢወጣም ተጠግተው ሊያናግሩን አልሞከሩም። ይህም በአካባቢው ከፍተኛ መፈራት እንደነገሰ ተጨማሪ ማሰረጃ ሆነን። በጸጥታ ሥጋት ምክንያት የክልሉ ፖሊሶች እስከ ድንበር መጥተው ከኦሮሚያ ፖሊስ ተረክበው አጅበው አሶሳ ወሰዱን። ከተማ እንደደረሰን ወደ ክልሉ ፕሬዝዳንት ቢሮ ሄደን የመጣንበትን ጉዳይ ነገርናቸው። የድንበር ችግር የሁለቱን ክልል ሕዝቦች ለከፋ ጉዳት መዳረጉን መረዳታችንንና የክልላቸውን መንግሥት እና ሕዝብ አሰተያየት ሰምተን የሚመለከታቸው አካላት ጉዳዩን እንዲፈቱ ግፊት ለማድረግ እንደምንፈልግ ገለጽንላቸው። ከባድ ችግር ውሰጥ መሆናቸውን አምነው ለጉዳዩ ትኩረት ሰለሰጠን አመሰገኑን። በማግሰቱ ሕዝቡን ሊሰበሰቡልን ቃል ገቡ።

ማምሻውን በሆቴል የሚያናግረን አብዛኛው ሰው አፋን ኦሮሞ ሰለሚያወራ ሁሉም ኦሮሞዎች መሰለውኝ ነበር። በኋላ ግን አሶሳ ከተማ ውሰጥ አብዛኛው ሰው አፋን ኦሮሞ እንደሚናገር፤ ነገር ግን ተናጋሪው ሁሉ በብሔር ኦሮሞ አንዳልሆነና እንደ በርታ፣ ሺናሻ፣ ጉሙዝ እና ኮሞ ያሉ ብሔሮች ቋንቋውን አቀላጥፈው እንደሚናገሩ ተረዳሁ። አዳራሽ በተዘጋጀው ሰብሰባ ላይ በከተማው የሚገኙ ሁሉም ብሔሮች ተገኙ። በአሶሳ ውሰጥ ሁለት ዓይነት ሕዝብ እንዳለ ተገነዘብን። አንደኛው እንደ በርታ፣ ጉሙዝ፣ ሺናሻ አና ኮሞ ያሉ ነባር (native) ሲሆኑ፣ ሁለተኛው ቡድን ደግሞ ከሌሎች የሀገሪቱ ክልሎች ሄደው እዚያ የሚኖሩ እንደ ኦሮሞ፣ አማራ እና ትግሬ ያሉ ናቸው።

የከተማዋን ማኅበራዊ ክፍፍል ከሌሎች አካባቢዎች የሚለየው በቆዳ ቀለም ላይ የተመሠረተ መሆኑ ነው። የሀገሬውን ተወላጆች "ጥቁሮች"፣ ከሌላ አካባቢ የመጡትን ደግሞ "ቀይ" ይሏቸዋል። በሕዝባዊ ውይይታችን ወቅት ይህ የቀለም ክፍፍል ከጥቂት ወራት በፊት ብጥብጥ መፍጠሩን እና ብዙ ሰዎች መጎዳታቸውን ሰማን። ከሌላ ቦታ የሄዱት ከሀገሬው ቀላ ሰለሚሉ ብቻ የሚያሳዩት ንቀት አሳፋሪ መሆኑን በመድረኩ ላይ ተነገረ። ይሄ ነገር ለእኔ አዲስ ስለነበር «ምንም ያህል ብትቀላ አፍሪካዊ እስከሆንክ ድረሰ ዓለም ጥቁር እንደሆንክ ሰለሚያውቅ ምንም የሚያኩራራ ነገር የለውም» በማለት በተበሳጨ አንደበት ገሰጽኳቸው።

የካማሺ ዞን አመራሮች በነጆ ከተማ ስብሰባ ተካፍለው ሲመለሱ መንገድ ላይ በመገደላቸው በተቀሰቀሰ ግጭት ምክንያት ካማሺ ከስምንት ወራት በላይ ከአሶሳ እና ከሌሎች ከተሞች ተቆራርጣ መቆየቷን መንዲ ላይ ሰምተን ነበር። እኛም መፍትሔ ለማፈላለግ ከክልሉ አመራሮች ጋር ተወያየን። "ዝግ ነው" ወደተባለው መንገድ ተጉዘን ተቆራርጦ ችግር ውስጥ ያለውን ሕዝብ ማየት እንደምንፈልግ ገልጸን አብረውን እንዲሄዱ ጋበዝናቸው። እነሱም የዞኑ ተወላጅ የሆነውን የክልሉን ምክትል ፕሬዝዳንት ቢመድቡልንም በማግስቱ ለመሄድ ስንነሳ ግን ሰውዬው ደብዘው ጠፋ።ከአሶሳ ከመውጣታችን በፊት በፌዴሬሽን ምክር ቤት ለሚደረግ ሰብሰባ ባለሥልጣናት ከፊንፊኔ መጥተው ሰለነበረ፤ የፌዴሪሽን ምክር ቤት አፈ-ጉባኤ ወ/ሮ ኬሪያ ኢብራሂም፣ የጠቅላይ ሚኒሰትሩ ቃል አቀባይ አቶ ንጉሱ ጥላሁን አና ሌሎችንም አግኝተን በሀገሪቷ ምዕራብ አካባቢዎች ያለው ችግር ትኩረት አግኝቶ መፈታት እንዳለበት አሳሰብን።

የምዕራብ ጉዟችንን አጠናቀን ወደ ፊንፊኔ ሰንመለሰ አቶ ለማ መገርሳ እና ሌሎች የክልሉን

ባለሥልጣናት፣ ከሀገር መከላከያ ሠራዊት ጄኔራል ብርሃኑ ጁላ እንዲሁም ከኦነግ አቶ ዳውድ እና ሌሎች ሰዎች በተገኙበት በሀያ ሰባት ገጽ ያጠናቀርነውን ዘገባ አቀረብን። በዚያ ዘገባ ላይ በኦነገ/በኦሮሞ ነጻነት ሠራዊት እና በመንግሥት መካከል ለተፈጠረው ግጭት የተከሰቱትን ችግሮች እንደተረዳን በዝርዝር ገለጽን። እነዚህ ችግሮችም፣

- ሥርዓት አልበኝነት (anarchy) እንደተፈጠረ፤
- በማኅበረሰቦች መካከል መተማመን እየሣሣ መምጣቱን፣ ይህም ለግጭት መስፋፋት በር መክፈቱን፤
- ከአጎራባች ብሔሮችጋር ያለው ግንኙነት ወደ ከፍተኛ ጥላቻ እያደገ መምጣቱን እና ጸረ-ኦሮሞ አሰተሳሰብ እንዲስፋፋ እያደረገ መሆኑን፤
- የመንገድ መዘጋት ኢኮኖሚያዊ እንቅስቃሴን እያደናቀፈ እና ማኅበራዊ ግንኙነትን እያቋረጠ እንዳለ፤
- የሰብዓዊ እርዳታ አለመድረሱ (በተለይ ካማሺ) ነዋሪዎችን አሰከሞት ለሚደርስ አደጋ ማጋለጡን፤
- የመከላከያ ሰራዊቱ በየጊዜው ጥቃት የሚፈጸምበት ቢሆንም፣ ግልጽ ትዕዛዝ ሰላልተሰጠው እራሱን መከላከል አለመቻሉ ከፍተኛ ጫና እያደረሰበት መሆኑን፤ ይህ በዚሀ ከቀጠለ ሠራዊቱ ወደ አመጽ ሊያመራ እንደሚችል፤
- ፖሊስ ጥንካሬ፣ ሞራልም ሆነ በቂ ትጥቅ የሌለው መሆኑ በከተማ ውሰጥ የሚፈጸሙ ወንጀሎችን ወይም የድንበር ጥቃቶችን እንዳይከላከል ማድረጉን፤
- 7 የታችኛው የአሥተዳደር መዋቅር ፈርሷል። ብዙ ባለሥልጣናት ሸሽተው ጠፍተዋል። ያሉትም ከፍተኛ ፍርሃት ውሰጥ ናቸው። ይህ የአሥተዳደር መፈራረሰ ቶሎ ካልታረመ ሥርዓት አልበኝነትን የበለጠ የሚያባብሰ ይሆናል፤
- ይህ ግጭት በፍጥነት ካልቆመ በወለጋ ብቻ ሳይገደብ ሀገሪቷን በሙሉ ሊያዳርስ የሚችል ትርምስ እና የእርሰ በርሰ ጦርነት (civil war) ያሰከትላል በማለት አቅርበናል።

እነዚህ ችግሮች ካልተቀረፉ ለሁሉም የሚመለከታቸው አካላት ማለትም ለኦነግ፣ ለመንግሥት እና ለሰፊው ሕዝብ አደጋ እንደሆነ በአንክሮ አስገዘብን። እየደረሰ ያለው ሁከት የኦነግን ስም የሚያጎድፍ እና ሰላማዊ ፓርቲ ሆኖ ለመቀጠል አሰቸጋሪ እንደሚያደርገው፤ ለመንግሥት ደግሞ ሥርዓት አልበኝነቱ ከቀጠለ ለውጡን ማደናቀፍ ብቻ ሳይሆን ወደ ግጭት እና የሀገር ውድቀት (state collapse) ሊያመራ እንደሚችል አሰጠነቀቅን። ለሕዝቡም በውድ መሥዋዕትነት ያገኘውን የነጻነት ጭላንጭል ማጨለም ብቻ ሳይሆን ለኢኮኖሚ ውድቀት እና ለከፍተኛ ዕልቂት ሊያጋልጠው እንደሚችል፤ በሌላው ማኅበረሰብ ዘንድም ጸረ-ኦሮሞ አመለካከቶች እንዲሰፋፉ እንደሚያደርግ ሥጋታችንን ገለጽን። በአጠቃላይ "ኦሮሞ እንኳን ሀገር ለማሥተዳደር እርሰ በራሱም መሰማማት አይችልም" የሚለውን ፕሮፓጋንዳ እውን በማድረግ አዲስ ለሆነ የጋራ ሞራላዊ ውድቀት (collapse of collective self-esteem) ሊያጋልጥ እንደሚችል ለማስረዳት ሞከርን።

እንደ መፍትሔም የሚከተሉትን እርምጃዎች ተግባራዊ እንዲያደርጉ ጠቆምን።

- መንግሥት እና ኦነግ ካድሬዎቻቸውን ፕሮፓጋንዳ ከማራገብ ማገድ አለባቸው።
- ኦነግ በፍጥነት ቢሮዎችን ከፍቶ ኃላፊዎችን በግልጽ በመመደብ በስሙ ሕዝብ የሚያውኩትን ከራሱ ማራቅ አለበት።
- የኦሮሚያ እና የቤኒሻንጉል ጉሙዝ ክልል መሥተዳደሮች መንገዱን በቅንጅት እንዲያሰከፍቱ እና ተፈናቃዮችን ወደ ቦታቸው እንዲመልሱ።

- ነጋዴዎች ሥራ በመቆሙ ምክንያት ዕዳቸውን መክፈል ባለመቻላቸው መንግሥት ከባንኮች ጋር ተመካክሮ መፍትሔ እንዲፈልግ።
- ድንበር ለማስከበር እና የከተማ ወንጀሎችን ለመቆጣጠር የኦሮሚያ ፖሊስን አቅም ማጠናከር እንደሚያስፈልግ።
- የኦሮሞ ነጻነት ሠራዊት በተቻለ ፍጥነት ከጫካ እንዲወጣ፤ ይህን ለማድረግም፡-
- በመንግሥት ላይ ያለመተማመን ችግር ስላለባቸው መተማመንን ለመፍጠር የሚረዱ እርምጃዎችን መተግበር።
- የኦሮሞ ነጻነት ሠራዊትን ጥያቄዎች እና ቅሬታዎች ሰምቶ ጉዳዩን በሰላማዊ መንገድ ለመፍታት ከሚመለከታቸው አካላት (ከኦሮሚያ ክልል ከመንግሥት፣ ከኦነግ፣ ከመከለላከያ ሠራዊት እና ከምሁራን) የተውጣጣ የጋራ ግብረ-ኃይል (joint-task force) ማቋቋም ይገባል የሚሉት ይገኙበታል።

በሪፖርታችን ላይ ሰፊ ውይይት ከተደረገ በኋላ መሻሻል ያለባቸው ነጥቦች ተሻሽለው፣ መጨመር ያለባቸውም ተጨምረው ለሁሉም ባለድርሻዎች ተሰጡ። በሪፖርቱ የቀረቡትን እና በውይይቶቹ ላይ የተነሱ የመፍትሔ ሐሳቦችን ተግባራዊ ለማድረግ ፕሬዝዳንት ለማ መገርሳ እና አቶ ዳውድ ኢብሳ በኃላፊነት እንዲሰሩ፣ ከተቻለም በጋራ ወደ ምዕራብ ኦሮሚያ በመሄድ ሕዝቡን አወያይተው እንዲያረጋጉ መግባባት ላይ ተደርሶ ተለያየን። ይህንን ዘገባ ያቀረብነው ኅዳር 12 ቀን 2011 ዓ.ም ነበር። ሆኖም ሁለቱም ወገኖች ቃል በገቡት መሠረት ወደ ሥራ አልገቡም። ይልቁንም ፕሮፓጋንዳው ተባባሰ። ቀደም ሲል በወለጋ ተወስኖ የነበረው ሁከት ወደ ሸዋ ተዛመተ። የሕዝቡ ተማጽኖም በዚያው ልክ በረታ።

## 8.6. የሰላም ጥረቱ ተግዳሮት

በ2019 የመጀመሪያ ወራት የአባ ገዳዎች ምክር ቤት ጉዳዩን በኃላፊነት ወሰዶ ሁለቱን ወገኖች በተናጠል ካነጋገረ በኋላ ምሁራን፣ የፖለቲካ ፓርቲ መሪዎች፣ አባ ገዳዎች እና የሀገር ሽማግሌዎችን ያሰተፈ ጠቅላላ ጉባኤ በኦሮሞ ባሕል ማዕከል አዘጋጀ። በሰብሰባውም ላይ አስከዚያች ዕለት ድረሰ የተደረገ የእርቅ ሙከራ በዝርዝር ቀረበ። ቀጥሎ በተካሄደው ውይይት ብዙ ሰዎች እቅጩን ከመናገር ይልቅ ዳር ዳር ሲሉ ነበር። ኦነግም ሆነ መንግሥት ኃለፊነት ከመውሰድ እና የመፍትሔ ሐሳብ ከማቅረብ ይልቅ ጉዳዩን ከራሳቸው ላይ መግፋትን መረጡ። ሽማግሌዎቹ እና ምሁራኑ መንግሥትንም ሆነ ኦነገን ማስከፋት ስላልፈለጉ አደባብሰው ተናገሩ። ማደባበሱ ሰላበሳጨኝ እጄን አውጥቼ የችግሩ ምንጩ ኦነግ እና መንግሥት እንደሆኑ አፍረጥርጬ ተናገርኩ። ሁለቱ አካላት ቃል ገብተው ያልፈጸሟቸውን ሰምምነቶች እና ሰላም ለማሰፈን ያከናወኗቸውን ጥረቶች ዘረዘርኩ። ጉዳዩ መንግሥትን የሚመለከት ሆኖ እያለ የኦዴፓ ፓርቲ ጽ/ቤትን የሚመሩት አቶ አለሙ ሰሜ መምጣታቸው ትክክል እንዳልሆነ በቁጣ ተናገርኩ። አቶ ዳውድ ኢብሳም ጦሩ ከእሱ ቁጥጥር ውጭ እንደሆነ ማስመሰሉን ትቶ፤ እንዲገባ ከልቡ ከፈለገ አዚያው መድረክ ላይ ግልጽ እንዲያደርግ ሐሳቤን አቀረብኩ።

ሰብሰባው ቢቀጥለም ከሰዓት በኋላ ለጉዳይ ወደ ሌላ ቦታ ሄድኩ። ኦነግ እና መንግሥት ጦርነቱን ለማሰቆም አሁንም በደጋሚ ተሰማምተው የኦሮሞ ነጻነት ሠራዊትን ከጫካ አሰወጥቶ ወደ ሰላማዊ ኑሮ የመመለሱን ኃላፊነት የአባ ገዳ ምክር ቤት ተረከበ። ሠራዊቱን የማሰመለሰ ሥራ ለማሰፈጸም በተካሄደው ምርጫ ሰባ አንድ አባላት ያሉት ኮሚቴ ተቋቋመ። ከዚያ በፊት ካደረግነው ጥረት በመነሳት እኔን እና በቀለ ገርባን ኮሚቴው ውሰጥ አካተቱን። አባ ገዳ በየነ ሰንበቶ ቤት መጥተው እንደተመረጥኩ እና እንድሰተፍ ሲጠይቁኝ አሻፈረኝ ብልም ከሌሎች አባ ገዳዎች ጋር ሰለተማጸኑኝ ተቀበልኩኝ። ኮሚቴው ተቋቁሞ በጥቂት ቀናት ውሰጥ ተገናኘን። የመጀመሪያው ሥራችን መንግሥት እና ኦነግ ሦስት ሦሰት ተወካዮችን እንዲመድቡ ማድረግ ነበር። ሰፊ ውይይት አድርገን ሥራች የሚመራበትን የማጣቀሻ ውል (term of reference) አዘጋጀን።

ጦሩን ለማሰገባት የሚያሰፈልጉ ተጨባጭ ጉዳዮች ላይ መወያየት ስንጀምር ግን ከሁለቱም ወገኖች ግትርነት መታየት ጀመረ። ዛሬ በሰምምነት የቋጨነው ጉዳይ በነጋታው ፈርሶ ይጠብቀናል። አንድ ቀን የመንግሥት ቡድን ውሰጥ ያለ ሰው፤ ከጠቅላይ ሚኒሰትሩ ጋር ካልተነጋገርን በስተቀር ይህ ጉዳይ ይሳካል ብሎ እንደማያሰብ ሹክ አለኝ። ይህን ጉዳይ ለኮሚቴው አባላት ነግሬ ጠቅላይ ሚኒሰትሩን ለማነጋገር ቀጠሮ ለማስያዝ ስንጠይቅ ዛሬ ነገ በማለት አጓተቱት። ብዙ ጠብቀን ሲሰለችን ከአባ ገዳዎች ጋር ወደ ቤተ መንግሥት ሄደን በሩ ላይ ቁጭ በማለት ለመማጸን ወሰንን። ሆኖም ቀኑን ሙሉ ፀሐይ ላይ ውለን የሚያናግረን ሰው አጣን። ማምሻውን ጄኔራል ብርሃኑ ጁላ እና ደምመላሽ ገብረሚካኤል መጥተው ቀጠሮ እንደሚያሰይዙልን፤ እንዲሁም ለሥራችን አሰፈላጊውን ሁሉ እንደሚያሟሉልን ቃል ገብተው ወደ ቤታችን ተመለስን።

በመንግሥት በኩል ፈር ያዘልን ስንል ከኮሚቴው ጋር አብረው እንዲሰሩ የተመደቡ የኦነግ ተወካዮች ከሀገር ወጡ። አንድ ቀን ምሽት በኮሚቴው የኦነግ ተወካዮች የነበሩት አቶ ዱጋሳ በከኮ እና ዴንጌ ሁሴን ቤቴ መጥተው፤ ወደ ቦረና ሄደው እዚያ የሚገኘውን ጦር አወያይተው ማሳመን እንደሚፈልጉ ነገሩኝ። መንግሥት መንገድ እንዲያሳልፋቸው እንዳመቻችላቸው ጠይቀውኝ የመከለከያ ሰዎችን አናግሬ በሰለም እንዲያልፉ አስፈቀድኩላቸው። እነሱ ግን በዚያው ኬንያ ገቡ፤ ኦነግም ሌሎች ተወካዮችን ሾመ።

ሁለቱም ወገኖች መለገማቸውን ቢቀጥሉም፣ እኛ ግን እንደ ኮሚቴ የተሰጠንን ኃላፊነት ለመወጣትና እስከመጨረሻው ለመግፋት ወስነን ሥራችንን ቀጠልን። የመንግሥትን እና የኦነግን ተወካዮች አስተያየት አድምጠን፣ የሌሎች ሀገራትን ልምድ አጥንተን፣ ጦርነት እንዲቆም እና የኦሮሞ ነጻነት ሠራዊት እንዲመለስ ያስችላሉ ብለን ያሰብናቸውን መርሆዎች (principles) አዘጋጀን። ይህን እቅድ ለሁለቱም ወገን መሪዎች ልከን ከተቀበሏቸው በኋላ ስምምነቱን ይፋ ለማድረግ በአምቦ ትልቅ ሰብሰባ ተደረገ። የኮሚቴው እቅድ ዋና ዋና ነጥቦችም:-

1. ተኩስ ማቆም፤
1.1. የቴክኒክ ኮሚቴው እቅድ ይፋ ከሆነበት ቀን ጀምሮ በሁለቱም በኩል ውጊያው እንዲቆም
1.2. በተኩስ አቁሙ ወቅት ሁለቱም ወገኖች ወደ ጦርነት ከሚያመሩ ማናቸውም ድርጊቶች እንዲቆጠቡ
1.3. የኦነግ ደጋፊዎችን እና አባላትን ማዋከብ እና ማሰር እንዲቆም
1.4. የተኩስ አቁም ውሳኔውን የሚያደናቅፍ የሚዲያ ፕሮፓጋንዳ እንዲረግብ
1.5. ሁለቱም ወገኖች ቅሬታ ካላቸው የአቋም መግለጫና የሚዲያ ንግግር ከመስጠት በመቆጠብ ቅሬታቸውን ለቴክኒክ ኮሚቴው እንዲያቀርቡ
1.6. ኮሚቴው የሁለቱንም ወገኖች እንቅስቃሴ በቅርበት በመከታተል የተኩስ አቁም አዋጁን የጣሰ ድርጊት ሲፈጽም የተገኘ ማንኛውንም አካል በመገናኛ ብዙኃን ይፋ እንዲያደርግ። ከዚሁ ጋር በተያያዘ ሕዝባችን ይህንን ሕግ የጣሰ ማንኛውንም ቡድን ምንም ልዩነት ሳያደረግ ተከታትሎ እንዲጠቁም።

2. የኦሮሞ ነጻነት ሠራዊትን በተመለከተ፤

2.1. የኦሮሞ ነጻነት ሠራዊት የሚገባው ክብር ተሰጥቶት ሞቅ ያለ አቀባበል ይደረግለታል።
2.2. ይህ ስምምነት ከወጣበት ቀን ጀምሮ ባሉት ሀያ ቀናት ውስጥ የኦሮሞ ነጻነት ሠራዊትን ሙሉ በሙሉ የመመለስ ሥራ ይጠናቀቃል።
2.3. ይህም በመጀመሪያ አሥር ቀናት ውስጥ አስፈላጊው ቅድመ ዝግጅት፣ የአቀባበል ኮሚቴዎችን የማቋቋም፣ አስፈላጊ መረጃ የመሰጠት እና ለኦሮሞ ነጻነት ሠራዊት ካምፕ የማዘጋጀት ሥራ ይሰራል።
2.4. በሚቀጥሉት አሥር ቀናት ውስጥ የኦሮሞ ነጻነት ሠራዊት ጦር ተሰብስቦ አቀባበል ከተደረገለት በኋላ ወደተዘጋጀላቸው ካምፕ በየተራ እንዲገቡ ይደረጋል።
2.5. ለኦሮሞ ነጻነት ሠራዊት አቀባበል በሚደረግበት ቀን የሀገር መከላከያ ሠራዊት እንቅስቃሴው እንዳይደናቀፍ ለሦስት ቀናት መንገዱን በመክፈት ለኦሮሞ ነጻነት ሠራዊት መመለስ የራሱን ሚና እንዲጫወት ይደረጋል።

3. የኦሮሞ ነጻነት ሠራዊትን የመመለስ ሥራ በየደረጃው የሚከናወን ሲሆን፣

3.1. በመጀመሪያ የሚሰበሰበው በአቅራቢያው በሚገኙ የወረዳ ከተሞች ነው።
3.2. ከዚያም በተወሰኑ ዞኖች አቀባበል ይደረግላቸዋል።
3.3. በመቀጠልም ወደተዘጋጀለት ካምፕ በክብር የሚገባ ይሆናል።
3.4. በአቀባበሉ ወቅት አላስፈላጊ ችግሮችን እና መሰናክሎችን ለማስወገድ በየደረጃው አመቻች ኮሚቴዎች ይዋቀራሉ። ለኮሚቴው አስፈላጊው በጀት ይመደባል። በአቀባበሉ ላይ የገዳ አባቶች፣ በየደረጃው ያሉ የመንግሥት ባለሥልጣናት፣ የኦነግ እና የሁለቱም ወገኖች ወታደራዊ ባለሥልጣናት ይገኛሉ።
3.5. የኦሮሞ ነጻነት ሠራዊት አንዴ ካምፕ ከገባ በኋላ ከመንግሥት እውቅና ውጭ የሚንቀሳቀስ የታጠቀ ኃይል በኦሮሞ እና በኦሮሚያ ተቀባይነት አይኖረውም። የመሰል ኃይሎችን እንቅስቃሴ ለመግታት መንግሥት እና ሕዝብ ሰላም እና የሕግ የበላይነትን ለማስፈን በጋራ ይሠራሉ።
3.6. የኦሮሞ ነጻነት ሠራዊት ወደ ካምፕ እንደገባ የሀገር መከላከያ ሠራዊት ከሕዝብ መሀል ወጥቶ ወደ ካምፑ እንዲመለስ ይደረጋል።

4. የኦሮሞ ነጻነት ሠራዊት የካምፕ አያያዝን በተመለከተ፤
4.1. የኦሮሞ ነጻነት ሠራዊት ሰፈሮች ጦርነቱ ሲደረግባቸው ከነበሩ አካባቢዎች ይርቃሉ።
4.2. የኦሮሞ ነጻነት ሠራዊት በካምፑ ውስጥ ከሁለት ወር ላልበለጠ ጊዜ ይቆያል።
4.3. በካምፕ ውስጥ ባሉበት ጊዜ አስፈላጊው ሥልጠና በሕግ ባለሞያዎች እና በጸጥታ አካላት የሚሰጥ ሲሆን የግንባታ ሥራም ይከናወናል።
4.4. የቴክኒክ ኮሚቴው ስለ አያያዛቸው እና እንክብካቤያቸው በቅርበት ይከታተላል።

5. የኦሮሞ ነጻነት ሠራዊት የመንግሥት ጸጥታ ኃይልን መቀላቀል በተመለከተ፤
5.1. የኦሮሞ ነጻነት ሠራዊት አባላት ትክክለኛ ግምገማ እና ሥልጠና ከተሰጣቸው በኋላ የግል ፍላጎታቸውን መሠረት አድርገው ወደ ጸጥታ ኃይሉ መቀላቀል፣ የፖለቲካ ፓርቲ አባል መሆን እና ከፈለጉ ወደ ሕዝቡ በመቀላቀል የግል ሥራ ላይ ተሰማርተው ለመኖር ሙሉ መብት አላቸው። በግል ሥራ ላይ ለሚሰማሩ መንግሥት አስፈላጊውን ድጋፍ ያደርጋል።

6. ምሕረት (Amnesty) በተመለከተ፤
6.1. የኦሮሞ ነጻነት ሠራዊት አባላት ጦርነት ውስጥ በነበሩበት ወቅት በቡድን እና በግል ለፈጸሙት ወንጀል ይቅርታ ይደረግላቸዋል። ከዚህ በፊት ለፈጸሙት ማንኛውም ወንጀል ተጠያቂ አይሆኑም እንዲሁም አይቀጡም።

በአምቦው መድረክ ላይ እነዚህን መርሆዎች ሳነብ ሕዝቡ በደማቅ ጭብጨባ ተቀበላቸው። የቴክኒክ ኮሚቴው አባል እና ዕውቅ ምሁር የሆኑት ኃይሌ ገብሬ ወደ መድረክ ወጥተው፣ «ለዚህ እርቅ መሳካት የሚጠቅም ከሆነ እኔን እንደ ጭዳ አርዳችሁም ቢሆን ታረቁ» በማለት እያለቀሱ ሁለቱን ወገኖች እና ሕዝቡን ለመኑ። አባ ገዳዎች እና ሃደ ሲንቄዎች ተንበርክከው ተማጸኑ። በስብሰባው መጨረሻም አባ ገዳዎች ኮርማ አርደው የሁለቱን ወገን መሪዎች ጉበት በማጉረስ አስማሏቸው። ሕዝቡም በተስፋ ተለያየ።

ከአምቦ ከተመለስን በኋላም ሁለቱም ወገኖች የተለያየ ምክንያት በመደርደር የማደናቀፍ

ሙከራ ሲያደርጉ ነበር። መንግሥት በጦር ሜዳ ውጊያውን በማጠናከርና የቴክኒክ ኮሚቴው የሚፈልገውን ትብብር በማጓተት ተስፋ ለማስቆረጥ ሞከረ። የመንግሥት ትብብር እንዲፋጠን ለመጠየቅ ከአቶ ለማ ጋር ቀጠሮ ቢያዝልንም ወደ ቢሯቸው ስንሄድ እንደሌሉ ተነገረን። በኦነግ በኩልም ሠራዊቱ እንዲገባ ፈቃደኝነታቸውን ቢገልጹም በተግባር ግን በተቃራኒው እየሄዱ ነበር። በማኅበራዊ ድረ-ገጾች ላይ የኮሚቴውን ሥራ የማጥላላት ዘመቻ ከመክፈት በተጨማሪ ወደ ጦሩ ሰዎችን በመላክ ከጫካ ወጥው እንዳይገቡ ያሳስቡ ገቡ። በስምምነቱ መሠረት አቶ ዳውድ ኢብሳ ሠራዊቱ እንዲገባ ማዘዝ ነበረበት። ይህንን ትዕዛዝ ላለመፈጸም ለረጅም ጊዜ አጓተው ከብዙ ልመና በኋላ ደብዳቤ ጻፉልን። ደብዳቤው የምዕራብ ዕዝ አዛዥ ለሆነው ጃል መሮ ድሪባ እና ለደቡብ ዞን አዛዥ ጃል ጎሊቻ ደንጌ እንዲሰጥ የተዘጋጀ ነበር። በመንግሥት በኩል የኢትዮጵያ መከላከያ ሠራዊት አዛዥ ጄኔራል ብርሃኑ ጁላ ሠራዊታቸው አስፈላጊ በሆነበት ቦታ ለቴክኒክ ኮሚቴው ተገቢውን ድጋፍ እንዲያደርግ ደብዳቤ ጻፉልን።

ሁለቱም ወገኖች ኮሚቴው የሚጠብቅባቸውን ነገሮች በብዙ ጫና ቢያሟሉም ለእርት ያላቸው ፍላጎት በጣም የወረደ እንደሆነ ግልጽ ነበር። በአንደበታቸው ወታደራዊ ስምምነቱ ተግባራዊ እንዲሆን የሚፈልጉ መስለው፤ ከመጋረጃ ጀርባ ግን ለማክሸፍ ያሤራሉ። ለምሳሌ የኦነግ አመራር ሠራዊቱ እንዲመለስ በግልጽ በደብዳቤ ትዕዛዝ ቢሰጥም ከጀርባ ግን ደብዳቤው የተጻፈው ጫና ተደርጎባቸው እንደሆነ እና ሠራዊቱ ለመመለስ ፍቃደኛ እንዳይሆን ወደ አዛዦች ሰዎችን ይልኩ እንደነበረ ከራሳቸው ከፍተኛ ባለሥልጣናት እንሰማ ነበር።

በመንግሥት በኩልም በድርጊት እና በቃላት ለማደናቀፍ ይሞክሩ ነበር። ኮሚቴው ወደ ዞኖች እንደተንቀሳቀሰ ጀኔራል ብርሃኑ ጁላ የኦሮሞ ነጻነት ሠራዊትን በማውገዝ ያደረጉትን ቃለ- ምልልስ በሚዲያ አሰራጩ። ይህም ሕዝቡ ስምምነቱ ፈርሷል ብሎ እንዲያስብ እና ሰራዊቱም የበለጠ እንዲጠራጠር አደረገው። ጄኔራል ብርሃኑ ለምን እንዲህ ዓይነት መግለጫ እንደሰጠ ስንጠይቅ፤ ንግግሩ ከሁለት ወራት በፊት የተደረገ እንደሆነ ነገረን። የሚዲያ ዘገባው ሆን ተብሎ እየተደረገ ያለ ሤራ መሆኑን ተረዳን።

ኮሚቴው ግን በዚህም ተስፋ አልቆረጠም። እስከ መጨረሻው ሙከራ ለማድረግ ወስነን ሥራችንን ቀጠልን። ጦርነት ይካሄድባቸዋል ተብሎ በኦነግ ወደተነገሩን ዞኖች እና ወረዳዎች የሚሄዱ ሰዎች ተመደቡ። በዚሁ መሠረት ወደ ምዕራብ ኦሮሚያ የሚሄደውን የልዑካን ቡድን እንዲያስተባብሩ በቀለ ገርባ እና አባ ገዳ በየነ ሰንበቶ ተመደቡ። በደቡብ በኩል አቶ ኃይሌ ገብሬ፣ ሺኽ ሐጂ ኢብራሂም ቱፋ እና እኔ ተመደብን።

ከጉዟችን አንድ ቀን ቀደም ብሎ የመንግሥት ባለሥልጣናት ወደ ምዕራብ እንጂ ወደ ደቡብ (ጉጂ እና ቦርና) መሄድ እንደማያስፈልግ ነገሩን። በዚያ አካባቢ ያለው የኦሮሞ ነጻነት ሠራዊት ትጥቅ ለመፍታት ከዞን አስተዳዳሪዎች ጋር ስምምነት ላይ ስለደረሰ የኮሚቴው መሄድ አላስፈላጊ እንደሆነ አሳወቁን። በጉዳዩ ላይ ኦነግን ስንጠይቅ ግን እውነት እንዳልሆነ ሰማን፤ በዞኖቹ የሚገኙ ምንጮችም ይህንኑ አረጋገጡልን። ኮሚቴውም መንግሥት እንዳለው የኦነግ ጦር በዞን አሥተዳደር በኩል ለመግባት ተስማምተው ከሆነ አይተን ለማበረታታት፤ እውነት ካልሆነም ጦሩን አነጋግረን ለማሳመን ወደ ደቡብም ልንሄድ ወሰንን።

መንግሥት ለኮሚቴው ስምሪት የሚያስፈልጉትን ነገሮች ሁሉ ለማሟላት ቃል ቢገባም ቀኑ ሲደርስ በቃሉ አልተገኘም። ሌላው ይቅርና በቂ መጓጓዣ እንኳን አላዘጋጀም። የኮሚቴውን ልዑካን በተመደቡባቸው ወረዳዎች ለማድረስ ሀያ አምስት ተሽከርካሪዎች እንዲሰጡን

ብንጠይቅም ሦስት ያረጁ ተሽከርካሪዎች ብቻ አገኘን። ዓላማቸው የኮሚቴውን የማስታረቅ ጥረት እንደምንም ማደናቀፍ እንደሆነ ይበልጥ ግልጽ እየሆነ መጣ። አባ ገዳዎቹ በጣም ስለተከፉ፣ ሞራላቸውን ለመጠበቅ እና የሰላም ሙከራውን ለማስቀጠል ከባለሀብቶች ገንዘብ ሰብስበን ተሽከርካሪዎችን በመከራየት ኮሚቴው በቀጠሮው ቀን ወደ ተመደበበት ቦታ እንዲሰማራ አደረግን።

የኮሚቴ አባላት በተመደቡባቸው ወረዳዎች እንደደረሱ ችግሮች መፈጠር ጀመሩ። በኦነግ በኩል በማኅበራዊ ሚዲያ ጦሩ መግባት የለበትም የሚል ዘመቻ ተጠናክሮ ቀጠለ። አብዛኛው ሠራዊት የኮሚቴውን ጥሪ ተቀብሎ ወደተዘጋጀው ቦታ ለመሄድ ሲሞክር ተኩስ ተከፈተበት፤ የኮሚቴው አባላት የሆኑ አባ ገዳዎችን ማፈን እና ማስፈራራት ተጀመረ።

በመንግሥትም በኩል የኮሚቴውን ሥራ የሚያስተጓጉሉ ተግባራት ተፈጸሙ። ጄ/ል ብርሃኑ ጁላ ሰጥውታል የተባለውን ቃለ-መጠይቅ የኦነግ ጦር አዛዦች መንግሥት ትጥቅ አስፈትቶ ሊጨርሳቸው ማቀዱን ጠቋሚ እንደሆነ ተረዱት። በሌላ በኩል የወረዳ እና የዞን አስተዳዳሪዎች ቃል እንደተገባው ለመተባበር ፈቃደኛ አልሆኑም። በምዕራብ በኩል ጥሪውን አክብሮ ወደ አባ ገዳዎቹ የመጣው ሠራዊት በመንግሥት ቃል እንደተገባለት አስፈላጊው አቀባበል እና እንክብካቤ ተነፈገው። የመንግሥት ባለሥልጣናት ምግብ እና የማደሪያ ቦታ እንኳን አናቀርብም አሉ። በአንዳንድ ቦታዎች ለአባ ገዳዎች መሣሪያውን በሰላማዊ መንገድ ያስረከበውን ሠራዊት በኃይል ለመውሰድ ፖሊስ እና ወታደሮችን ይዘው ሄዱ። ሁኔታው የኮሚቴ አባላትን በጣም አስደነገጠ። ለመግባት ወስነው የነበሩ የኦነግ ጦር አባላትም በመንግሥት እርምጃ ጥርጣሬ ውስጥ ገብተው ሐሳባቸውን ቀየሩ። የኮሚቴው አባላት ዛቻ እና ድብደባውን በጽናት ተቋቁመው ከጫካ ወጥቶ መሣሪያ ያስረከባቸውን ሠራዊት ለመንከባከብ ጥረት አደረጉ።

እኔ የነበርኩብት ልዑክ በሄደበት ደቡብ ላይም ችግሮች ገጠሙን። በመጀመሪያ በጉጂ ዞን ቡሌ ሆራ ከተማ እንደደረስን በዞኑ የሚንቀሳቀሰውን ሠራዊት እንዲመልሱ የተመደቡትን የኮሚቴ አባላት ከአካባቢው አሥተዳደር ጋር አሰተዋወቅን። የነበረው ስምምነት ሠራዊቱን ተቀብሎ፣ መዝግቦ እና መሣሪያ ተቀብሎ የሚያስገባው እኛ ያለንበት የአባ ገዳዎች የቴክኒክ ኮሚቴ ነበር። የጉጂ ዞን አሥተዳዳሪዎች ግን «በዞናችን ያለውን ጦር እኛው አስፈትተን ለማስገባት ከሠራዊቱ ጋር ተወያይተን ተስማምተናል» አሉ። ከፊንፊኔ የመጣው የአባ ገዳዎች ኮሚቴ መሳተፍ ከፈለገ በዞኑ አሥተዳዳሪዎች አመራር ሥር መሆን እንዳለበት ተናገሩ። እኛ ገለልተኛ ኮሚቴ ስለሆን በአሥተዳደር መዋቅር ሥር መግባት እንደማንፈልግ ሞገትን። መስማማት ሲያቅተን የጉጂ አባ ገዳዎችን አመጡ። እነሱም እንደ ዞን አሥተዳደሮቹ ሁሉ እዚያ ያለው ጦር በዞን አሥተዳደር በኩል ለመግባት ዝግጁ መሆኑን አረጋገጡልን። የጦሩን አዛዦች ስንጠይቅ ግን የተባለው እውነት እንዳልሆነ ተረዳን። ከሰፊ ውይይት በኋላ የዞኑ አሥተዳደር እጁን እንዲያስወጣ እና የጉጂ አባ ገዳዎች ከፊንፊኔ ከመጣው ኮሚቴ ጋር በመተባበር ጦሩን እንዲያስገቡ ስምምነት ላይ ተደረሰ። ከቦረና ስንመለስ ጦሩን ሰብስበው እንደሚጡበቁን ቃል ገቡ።

ወደ ቦረና ዞን ዋና ከተማ ያቤሎ ስንደርስ እዚያም የበለጠ ሤራ ተጎንጉኖ ጠበቀን። ልናናግራቸው የጠራናቸውን አባ ገዳዎች እና የሀገር ሽማግሌዎች የዞኑ አሥተዳደር የራሱን ስብሰባ አዘጋጅቶ እንዳናገኛቸው እንቅፋት ሆነብን። ከረጅም ተማጽኖ በኋላ በሁለተኛው ቀን ስናገኛቸው ደግሞ

«የኦሮሚያ አባገዳዎች ምክር ቤት የቦረና አባገዳዎችን ስላስከፋ ውሳኔያቸውን አንቀበልም፤ ክኮሚቴው ጋርም አንሰራም» አሉ። የምክር ቤቱን ጥፋት ስንጠይቃቸው «ጦሩ እንዲመለስ የወሰኑበት ስብሰባ ላይ ስላልተጠራን ተንቀናል» ሲሉ ቅሬታቸውን አቀረቡ። «እንዳልተጋበዛችሁ አናውቅም። እናንተን አለመጋበዝ ትክክል አይደለም። ቅሬታችሁን እንነግራቸዋለን፤ እናንተም በገዳ ሥርዓት መሠረት ጠይቋቸው። ይህን ጦር መልሶ ሰላም ማስፈን ለቦረና እና ለኦሮሚያም ጥቅም ነው። ቅሬታችሁን ወደፊት እናስተናግዳለን ለአሁኑ ይህንን ጦር ተባብረን እናስገባ» ብለን ተማጸንን። እነሱ ግን «ይህን ጦር ያደራጀነው እኛ ነን፣ ለሀያ ሰባት ዓመት ደማችንን አፍሰን እና ሀብታችንን አሟጠን እዚህ አድርሰነዋል። እኛ የምንላቸውን እምቢ አይሉም። እኛ አሳምነን ከጫካ አስወጥተን እናመጣቸዋለን እናንተ አታስፈልጉም ሂዱ» አሉን።

አቋማቸውን እንዲቀይሩ አብዝቼ ተማጸንኳቸው። አካባቢው በመንግሥት እና በኦሮሞ ነጻነት ሠራዊት መካከል በሚደረግ ጦርነት፤ እንዲሁም በብሔር ግጭቶች ለረጅም ጊዜ ሲታመስ እንደነበረ አስታውሻቸው፤ ቀጥሎ የሚመጣውን የከፋ አደጋ ለማስቀረት ጦሩን እንዲያስገቡ ጠየቅኳቸው። አስቀድሞ ጦሩ “ጠላትን ይከላከልልናል” ስላሉ ጭንቀታቸው ይህ ከሆነ የኦነግ ጦር ጫካ ያደፈጠ አማጺ መሆኑ ቀርቶ፣ ከመንግሥት ጋር ታርቆ እና ከዞኑ የጸጥታ ኃይሎች ጋር በመቀላቀል ሕዝቡን ማገልገል እንደሚችል በመንገር ለማሳመን ሞከርኩ። ይህን ሐሳብ የሰሙ አባ ገዳዎች «ከተቻለ ጥሩ ነገር ነው» በማለት ተስማሙ። ይሄኔ አንድ ሰው ከውይይታችን መሀል ተነስቶ ስልክ ደወለና ሲመለስ ያቀረብኩት ሐሳብ ተቀባይነት እንደሌለው አሳወቀ። የገዳ አባቶች በድንጋጤ አቀረቀሩ። ሰውዬው ስብሰባው አልቋል ብሎ በተነን። በኋላ ሳጣራ ከሕወሓት ዘመን ጀምሮ ከመንግሥት የደኅንነት መሥሪያ ቤት ጋር ሲሰራ የነበረ መሆኑን ስሰማ አባ ገዳዎቹ ለምን ደንግጠው እንደተበተኑ ገባኝ። ውይይቱ እዚያው ቢገባደድም አባ ገዳዎቹ ከብት አርደው፣ ከቆዳው ሜዲቻ (በእጅ የሚጠለቅ ቆዳ) አስረውልን መርቀው ሸኑን።

በሌላ በኩል ያቤሎ እንደደረስን ከአቶ ዳውድ የተላከውን ደብዳቤ ለጦሩ የደቡብ ዕዝ አዛዥ ለጃል ጎሊቻ ዴንጌ እንዲደርስ ድርጅቱ በመደበው ሰው ልከን ምላሹን መጠባበቅ ጀመርን። ከሁለት ቀናት በኋላ ብዙ ቅድመ ሁኔታዎችን ዘርዝሮ፤ ካልተሟሉ ጦሩ እንደማይገባ መልስ ሰጠን። የዘረዘራቸው ቅድመ ሁኔታዎች ፊንፊኔ በተደረገው ስብሰባ ላይ መነሳታቸውን እና ለመፍታትም ስምምነት ላይ እንደተደረሰ በማስገንዘብ አቋማቸውን ቀይረው ጦሩን እንዲያስገቡ ለማሳመን ሌላ መልዕክት ላክን።

መልሱን እየጠበቅን እያለ ሌላ አስገራሚ ነገር አጋጠመን። አንድ ሰው ወደ እኔ መጣና «ሠራዊቱ እንዲገባ ከፈለጋችሁ አምስት ሚሊዮን ብር መክፈል አለብህ» አለኝ። ለምን ብዬ ስጠይቀው፣ «ሠራዊቱ እንዳይገባ የሚፈልጉ አራት ሚሊዮን ለመክፈል ቃል ገብተዋል። አንተ ከዚያ በላይ ከከፈልክ ጦሩን እናስገባለን» አለኝ። «አይ፣ ኮሚቴው በመንግሥት እና በኦነግ ስምምነት መሠረት መግባት የሚፈልገውን ጦር በሰላም እንዲገባ ማድረግ እንጂ በገንዘብ ለመደለል አልመጣም» አልኩት። ሰውዬው «አንተ ነገሩ አልገባህም። የማትከፍል ከሆነ ጊዜህን አታባክን ወደቤትህ ተመለስ» የሚል ምክር ሰንዝሮ ሄደ። ንግግሩን ሲያዳምጥ የነበረ ሰው በኋላ እንደነገረኝ ከሆነ፣ ገንዘቡን የተጠየኩት «እነ ጀዋር ጦሩን ለመመለስ ከውጭ መንግሥታት ብዙ ገንዘብ አግኝተዋል» የሚል ወሬ እየተናፈሰ ስለነበር ነው።

ወደ ጃል ጎሊቻ የላክናቸውን ሽማግሌዎች ምላሽ እየጠበቅን እያለ ከተማዋን ለቀን እንድንወጣ ግፊቱ በረታብን። የተከራየንበት ሆቴል አከራዮች ክፍሎቹን ለሌሎች ሰዎች

እንዳከራዩ በመግልጽ እንድንለቅላቸው ወተወቱን። እምቢ ብለን አንድ ምሽት ጨመርን። በዚያ ምሽት ራሷን "የኦሮሞ ነጻነት ሠራዊት አዛዥ" ብላ ያስተዋወቀች ሴት ደውላ ያቤሎን ለቅቄ ካልወጣሁ አንደሚገድሉኝ ዛተች። እኔም «ለሕዝብ እና ለሀገር ሰላም እንጂ የትኛውንም ቡድን የማስገደድ እቅድ እንደሌለኝ ነግሬያት፤ የኦነግ ጦር መመለስ ካልፈለገ የእናንተ ምርጫ ነው። ክፉ መነጋገር አያስፈልግም። ልታስፈራሪኝ እየሞከርሽ ከሆነ ግን ወደ ሀገር ስገባ በራሴ ላይ ሞት ፈርጀ እንደሆነ አታውቂ ይሆናልና አሁን ይግባሽ!" ብዬ በንዴት ስልኩን ዘጋሁባት።

ጫናው ከአንድ ወገን ብቻ አልነበረም። በማግስቱ የመንግሥት ባለሥልጣናት ሰው ልከውብን ከከተማው እንድንወጣ ከላይ ትዕዛዝ እንደደረሳቸው በመግለጽ እንድንሄድ ተማጸኑን። ትዕዛዙ ከእነማን እንደመጣ በማስረጃ አሳዩን። ተልዕኳችን እንዳይሳካ የተደራጀ ሤራ እንዳስ ተረድተን በማግስቱ ጠዋት መመለስ ጀመርን። ቡሌ ሆራ እንደደረስን ለጉጂ ዞን የተመደበው ኮሚቴ እንዳይሰራ መከልከሉን እና አንድም ወታደር መመለስ እንዳልቻሉ ተረዳን። የዞኑን አስተዳዳሪዎች አግኝተን ስናናግር ፤ ከጥቂት ቀናት በፊት በዚያ ስናልፍ በዞኑ ያለውን የኦነግ ጦር ለማስገባት ከአዛዦቹ ጋር መስማማታቸውን የነገሩንን ቃል በመቀየና ኦነግ የፈጸማቸውን ወንጀሎች በመዘርዘር በኃይል ለማጥፋት መወሰናቸውን ገለጹልን። በጦሩ ጉዳት ደርሶብናል የሚሉ ሰዎችን አምጥተው ከፊታችን ተንከባለው እንዲያለቅሱ አስደረጉ። ወደ ሻኪሶ ያቀናውና በአቶ ኃይሌ ገብሬ የሚመራው የልዑካን ቡድንም በተመሳሳይ መልኩ እንዳይሰራ መደረጉን ሰማን። ሠራዊቱ እንዳይገባ በሁለቱም ዞኖች ሤራ እንደተሰራብን በመረዳት ወደ ፊንፊኔ ለመመለስ ወሰንን።

ከእኛ ጋር ሲነጻጸር ወደ ምዕራብ የተጓዘው የቴክኒክ ኮሚቴ ልዑካን ውጤታማ ነበር። በመቶዎች የሚቆጠሩ ወታደሮችን አሳምነው መመለስ ችለዋል። ሆኖም ለበርካታ ችግሮችም ተጋልጠዋል፤ የታፈኑ አባላትም ነበሩ። የገባውን ጦር ይዘው የተረከቡትን መሣሪያ ለመንግሥት አስረክበው ወደ ፊንፊኔ ለመሄድ ሲነሱ የመንግሥት ሰዎች ምግብ እና መጓጓዣ ለማቅረብ ፈቃደኛ አልነበሩም። በቀለ ገርባ እና አባ ገዳ በየነ ሰንበቶ ገንዘብ ከሰዎች እየተበደሩ፤ የጎደለውን ከኪሳቸው እየሞሉ ምግብ እና መጓጓዣ ችለው ወደ ጦላይ ጦር ካምፕ በመውሰድ ለመንግሥት አስረከቡ። ከሆሮ ጉዱሩ ወለጋ ዞን የመጣውን የኦሮሞ ነጻነት ሠራዊት ቡድን፣ የኦነግ ሥራ አስፈጻሚ አባል ከሆነው ከጃል አብዲ ረጋሳ ጋር አምቦ በሚገኘው ሰንቀሌ ፖሊስ ማሰልጠኛ በመገኘት ጎበኘን። ምግብ ሰላልተዘጋጀላቸው በሬዎች ገዝተን ከአምቦ ሕዝብ እንጀራ ተቀብለን አበላናቸው።

በአጠቃላይ የመንግሥት ባለሥልጣናት ጦሩ ከጫካ እንዲወጣ እንደማይፈልጉ በብዙ ተግባራት አረጋገጡልን። ተስፋ ሳንቆርጥ የቀረውን ሠራዊት አሳምነን እና በሀገር ሽማግሌዎች አስመክረን ለመመለስ የአንድ ወር ዕድሜ እንዲጨመርልን ብንጠይቅም ፈቃደኛ አልሆኑም፤ ይባስ ብሎ ሰፊ የጦርነት ዘመቻ አወጁባቸው።

ሙከራችንን ከዚህ በላይ መግፋት እንደማንችል ስለተረዳን የሥራ አፈጻጸም ሪፖርት አዘጋጅተን የመንግሥት ባለሥልጣናት፣ የሀገር መከላከያ ሠራዊት አዛዦች እና የኦነግ አመራሮችንጠርተን እቀረብን። ያጋጠሙንን ችግሮች እና ስኬቶቻችንን ገልጸን፤ ያስመለስነውን የወታደር እና የጦር መሣሪያ ብዛት ገለጽን። ጫካ የቀረው ሠራዊት የመመለስ ፍላጎት እያለው የቀረበትን ምክንያቶች ዘረዘረን። ዋና ዋናዎቹ ምክንያቶች ሁለቱም ወገኖች የገቡትን ቃል ማጠፋቸው፣ አፍራሽ የሆነ የማኅበራዊ ሚዲያ ፕሮፓጋንዳ እና የጊዜ እጥረት ናቸው። የተቀሩትን የሠራዊት

አባላት ለማሳመን የአንድ ወር ጊዜ ጠይቀን መከልከላችንን አብራራን። ስለዚህ መንግሥት እና ኦነግ የቀረውን ጦር ለመመለስ ሌላ መንገድ እንዲፈልጉ በመጠቆም የአባ ገዳ ምክር ቤት ያቋቋመው የቴክኒክ ኮሚቴ ሥራውን ማጠናቀቁን አሳወቅን።

መንግሥትም ሆነ ኦነግ መፍትሔ ማምጣት ሳይችሉ አለመረጋጋቱ እየተባባሰ መጣ። አቶ ሽመልስ አብዲሳ ፕሬዝደንት ሆኖ እንደተሾመ ኮሚቴውን እና የኦነግ አመራሮችን በጽ/ቤቱ ጠራን። ጫካ በቀረው የኦሮሞ ነጻነት ሠራዊት እየደረሰ ያለውን ችግር ዘረዘረ። በኦነግ በኩል አቶ ዳውድ ኢብሳ ሠራዊቱን ለአባ ገዳዎች ማስረከቡን በማስታወስ፤ በወቅቱ በእሱ ድርጅት የሚመራ ጦር እንደሌለ ገለጸ። ከዚህ ሐሳብ በመነሳት የኦነግ፣ የኦሮሚያ መንግሥት እና የሀገር መከላከያ ሠራዊት ተወካዮች ኦነግ በጫካ ውስጥ ለቀረው ሠራዊት ተጠያቂ እንደማይሆን የሚገልጽ የተዘጋጀ ደብዳቤ ፈረሙ። እኛ የኮሚቴው ተወካዮችም የስምምነቱ ምስክሮች ሆነን ፊርማችንን አሰፈርን። ጫካ ለቀረው ሠራዊት የመጨረሻ ጥሪ ቀርቦ መንግሥት ከሕዝቡ ጋር በመሆን ሕግ ያስከብር ተባለ። ጦርነቱን ለማስቆም ሳደርገው የነበረው ሙከራም እዚህ ላይ ተደመደመ።

ሰዎች ብዙ ጊዜ የኦሮሞ ነጻነት ጦርን ትጥቅ በማስፈታታችን ይወቅሱናል። ይህ የምክደውም ሆነ የማፍርበት ጉዳይ አይደለም። በሀገራችን የትጥቅ ትግል አብቅቶ ወደ ሰላማዊ ፖለቲካ መሸጋገር አስፈላጊ ነው ብዬ በጽኑ አምን ስለነበረ፣ ጫካ የቀሩ አማጺያንን በማሳመን ትጥቅ ፈተው ወደ ሰላማዊ ኑሮ እንዲመለሱ ያላሰለሰ ጥረት ማድረጌ ግልጽ ነው። ጠ/ሚኒስትር ዐቢይ ወደ ሥልጣን ከመጣ ጊዜ አንስቶ በኦነግ እና በመንግሥት መካከል እርቅ መፍጠር ለሽግግሩ መሳካት በጣም ወሳኝ ጉዳይ እንደሆነ ስወተውት ነበር። ለዚህም አንዱ ምክንያቴ ሥልጣን የያዘው አዲስ መንግሥት ታጣቂ ኃይሎችን አስታርቆ ጦራቸውን ከጫካ አውጥቶ በሕብረተሰቡ እና በመንግሥታዊ ሥርዓቱ ማሳተፍ (Demobilization, Disarmament, and Reintegration) መቻሉ ለዴሞክራሲያዊ ሽግግር ስኬት ትልቅ ሚና ይጫወታል። ግጭት ከቀጠለ የጦርነት ፖለቲካን በማስፋፋት አምባገነናዊ አገዛዝ መገንባት ለሚፈልጉ ቡድኖች ዕድል ይሰጣል። ወደ ጫካ የተገፋው ኃይል ትግሉን አቁሞ በመታረቅ ክአሥተዳደሩ እና ከሕዝቡ ጋር አሳማኝ በሆነ አግባብ ተቀላቀለ ማለት የጦርነት ፖለቲካ ቀርቶ፣ ሰላማዊ ፖለቲካ ሥር እንዲሰድ ይረዳል።

የትጥቅ ትግል እንዲቆም አበክሬ የሠራሁበት ሁለተኛው ምክንያት፣ በኦነግ እና በኦሕዴድ መካከል ካለው የጠላትነት ታሪክ አንጻር ሁለቱ ኃይሎች ታርቀው ከጦርነት ፖለቲካ ካልወጡ በስተቀር፣ የኦሮሞ ሕዝብ መከፋፈሉን ይቀጥላል በሚል ነው። ይህም በደም የተገኘውን ለውጥ አሳክተን ሀገርን ወደ ዘላቂ ዴሞክራሲ እና ልማት ለማሸጋገር ያለንን ዕድል ያጨናግፋል። ስለሆነም ሥልጣን በኦሮሞ እጅ እንደሚወድቅ ከተረዳሁበት ጊዜ ጀምሮ የኦሕዴድ እና የኦነግ አመራሮች በፍጥነት መነጋገር እንዲጀምሩ እና በመካከላቸው እርቅ ፈጥረው ሀገሪቱን ለማሻገር በጋራ እንዲሰሩ ስማጸን ነበር። ተስፋ ቆርጬ ወደ ተቃውሞ ፖለቲካ እስክገባ ድረስ በተገኘው አጋጣሚ ሁሉ የመንግሥትም ሆነ የኦነግ ባለሥልጣናትን ያልተማጸንኩበት እና ያልተቆጣሁበት አጋጣሚ አልነበረም።

ወደኋላ መለስ ብዬ ሳውጠነጥን፣ በሁለቱም ወገን ያሉ የተወሰኑ ቡድኖች ከመነሻውም እርቅ ለማውረድ ፍላጎት እንዳልነበራቸው የሚጠቁሙ ብዙ ነገሮች ነበሩ። ለምሳሌ ገና ወደ ሀገር ቤት እንደገባሁ ሰሞን አንድ የኦሕዴድ አመራር «ኦነግን ለማስታረቅ ለምን እንዲህ ትለፋለህ? ኦነግ ጫካ መቆየቱ ለእኛ ጥሩ ነው። ወያኔ የኦነግን መኖር ተጠቅሞ በኦሮሞ ውስጥ

የሚነሳበትን ተቃውሞ በመደፍጠጥ ለሀያ ሰባት ዓመታት በሥልጣን ላይ ቆይቷል። ኦሮሞ አመጽን ባሕሉ አድርጓልና በእኛም ላይ የሚያምጽብን ስለማይጠፋ የኦነግን ስም ለጥፈን ቀጥቅጠን እንገዛለን» ብሎኛል።

ይህ እሳቤ የኦሮሞ ነጻነት ሠራዊት በሕወሓት ዘመን እንደነበረው መንምኖ በዳር ሀገር እና በጥቂት ወረዳዎች ብቻ ተወስኖ ይቀራል ከማለት ይመነጫል። ሐሳቡ የመጣው የኦሮሞን ውስጣዊ ሁኔታ፣ የአዲሱን መንግሥት ጥንካሬ እና የውጭውን ዓለም ሁኔታ በተለይም የዓለምን ተለዋዋጭነት በአግባቡ ካለመረዳት ነው። ከዚህ የተሳሳተ ትንታኔ በመነሳት ሥልጣን የያዘው ቡድን በኦሮሚያ ውስጥ የሽምቅ ኃይል ለማበብ ያለውን ዕድል አሳንሶ እንዲያይ አድርጎታል። የኦሮሞ ቡድን ሥልጣን ከተቆጣጠረ በኋላ በኦሮሚያ ውስጥ የትጥቅ ትግል ለማካሄድ ቢሞከርም ምንም ድጋፍ አያገኝም የሚል ግምት ነበራቸው። ይህ ግምት በአጭር ጊዜ እና በመጠነኛ ወጪ በውይይት ሊፈታ ይችል የነበረውን ጉዳይ ኦሮሚያን እና ኢትዮጵያን ሊያናጋ ወደሚችል የእርስ በእርስ ጦርነት እንዲሸጋገር አደረገው።

በኦነግ በኩልም የተወሰኑ አመራሮች ገና ከጅመሩ እርቅ የማይቻል እንደሆነ አቋም ይዘው ነበር። ከዚህ በመነሳት ከኤርትራ ወደ ሀገር ቤት ለመመለስ እንደወሰኑ የተወሰነ ሠራዊት ለመንግሥት ቢያስረክቡም፤ ሌላውን ደግሞ በሱዳን በኩል ወደ ምዕራብ ኦሮሚያ አስገብተዋል። ወደ ሀገር ከገቡ በኋላም፣ ፊንፊኔ ተቀምጠው ከመንግሥት ጋር ስለ ሰላምና ሽግግር እየተነጋገሩ፤ በጎን ወደ ጫካ የላኩትን ጦር በማጠናከር ላይ እንደነበሩ በሂደት ይፋ ሆነ። ይህን የኦነግ አመራር ስልት ከኤርትራ ከመውጣታቸው በፊት የስማሁ ቢሆንም፣ ከመንግሥት ጋር መተማመን ከተፈጠረ፣ በጫካ ያስቀሩትን ጦር እንደሚመልሱ ተስፋ አድርጌ ነበር። ኦነግ በአንድ ድርጅት ሥር በከተማ ሰላማዊ፣ በጫካ ደግሞ የትጥቅ ትግልን ጎን ለጎን ለማራመድ የነደፈው ስልት መጨረሻ ላይ ከሁለት ያጣ እንዳያደርገው በተደጋጋሚ አመራሩን ሳስጠነቅቅ ነበር። እንደሠጋሁትም ስላማዊ እና የትጥቅ ትግልን አጣምሮ መሄድ ኋላ ላይ የድርጅቱን አመራር በመከፋፋል፣ አንደኛው እንጃ ከገዢው ፓርቲ ጋር እንዲያብር አደረገ። የኦሮሞ ነጻነት ሠራዊትም ከኦነግ የፖለቲካ አመራር እራሱን ለይቶ በአዲስ አደረጃጀት ለመንቀሳቀስ ወሰነ።

በኦነግ እና በኦሕዴድ መካከል ለዘመናት የነበረው ጠላትነት እና መናናቅ፣ ከለውጡ በኋላ በውይይት አለመፈታቱ በከፍተኛ መሥዋዕትነት ያገኘነውን ሽግግር በማደናቀፍ ረገድ ትልቅ ሚና ተጫውቷል። የኦነግ አመራር የኦሕዴድን ሰዎች እንደ ተላላኪ እና አቅመ-ቢስ በማየት ይንቃሉ። ኦሕዴዶች በበኩላቸው ኦነግን እንደ ትምክህተኛ እና በወሬ እንጂ በተጨባጭ ለሃምሳ ዓመታት ፍሬ ያላፈራ ድርጅት እንደሆነ በመጥቀስ ያጣጥላሉ። ኦነግ ራሱን እንደ ቀደምት ብሔርተኛ ፓርቲ እና የምሁራን መከማቻ አድርጎ በመመልከት ሥልጣን ይገባኛል የሚል እምነት አለው። ኦሕዴድ ደግሞ ኦነግ ትቶት የሄደውን ትግል ሀገር ውስጥ ቀርተን የታደግን፣ ኦሮሚያንም በመመሥረት የአሥተዳደር ልምድ ስላለን ሥልጣን ይዘን ሀገር ማሻገር የምንችለው እኛ ብቻ ነን ይላሉ። ይህ መጠላላት እና መናናቅ ሥልጣን በድርድር የመካፈልን ጠቀሜታ እንዲሁም ተቻችሎ ሀገርን በጋራ ማሻገር ያለውን አስፈላጊነት እንዳይገነዘቡ ጋርዷቸዋል።

ኦሕዴድ እና ኦነግ ወደ እርቅ እንዳይሄዱ እንቅፋት የሆነው ሌላው መሰናክል የኦነግ አንጃዎች ናቸው። ኦነግ ከ2001 ጀምሮ በቡድን ሲከፋፈል ቆይቶ፣ ሽግግሩ ሲጀመር አራት እና አምስት ቡድን ሆነው የትላንቱን ሽኩቻ እንደያዙ ወደ ሀገር ቤት ገቡ። የተወሰኑት አንጃዎች ከገዢው ፓርቲ ጉያ በመሸጎጥ የመንግሥትን ተቋማት ተጠቅመው ባላንጣቸው የሆነውን

እንጃ ለመስቀል ሞክሩ። ለመንግሥት ያልተበገረው አንጃ ደግሞ ገዢው ፓርቲ ባላንጣዎቹን በማስጠጋቱ በጠላትነት ፈረጀው። ከመንግሥት ጋር ያበረው አንጃ መንግሥትን እና በዳውድ ኢብሳ የሚመራውን አነግ ለማስታረቅ ሲደረግ የነበረውን ጥረት ለማክሸፍ አፍራሽ ድርጊቶችን ሲፈጽም ነበር። በኦሮሞ ትግል ውስጥ በነበራቸው የአመራርነት ሚና እና የተከበረ ስም የነበራቸው አንጋፋ መሪዎች ሳይቀሩ በአርስ በእርስ ጥላቻ በመገፋፋት የእርቅ ሂደቱን የሚጎዳ መርዝ ሲራጩ ነበር።

በኦነግ እና በአሕዴድ መካከል ያለው ችግር በሰላማዊ መንገድ በፍጥነት ካልተፈታ በሕዝብ እና በሀገር ላይ ከባድ አደጋ ሊያመጣ እንደሚችል ብዙ ጊዜ ረጅም ጽሑፎችን ከመጻፍ እና በመገናኛ ብዙኃን ከመናገር ባለፈ መሪዎቹንም በተደጋጋሚ ስወተውት ነበር። ከሁለቱ ወገን አመራሮች ጋር የነበረኝን የግል ግንኙነት ተጠቅሜ ለማቀራረብ ብዙ ሞክሬያለሁ። በኋላም በቴክኒክ ኮሚቴው ውስጥ በቀጥታ ተሳትፌ እስከ መጨረሻው ድረስ ደከመኝ ሰለቸኝ ሳልል ሰርቻለሁ። በመጨረሻም የኦሮሞ ፖለቲካ ልሂቃን (elites) በቀጥታ እና ቀጣይነት ባለው መልኩ የሚወያዩበት እና የሚደራደሩበት መድረክ እንዲኖራቸው በማሰብ፤ የኦሮሞ አመራር መማክርት (Gumii Hoggansa Oromoo) አቋቋምኩ። በመሪዎቹ ስግብግብነት፣ ጥላቻ፣ ጥርጣሬ እና ሀገር የማሥተዳደር ልምድ ማነስ ምክንያት የተደርጉ ጥረቶች ሳይሳኩ ቀርተዋል። እንደፈራነውም ኦሮሚያን ወደ ከፍተኛ ትርምስ ውስጥ ከተታት፤ ሀገሪቷ ወደ ዴሞክራሲያዊ ሥርዓት ለመሸጋገር የነበራት ዕድልም ባክኗል።

በመጨረሻ ትክክል የነበረው ማን ነው? እኛ "ጦርነት ይበቃል ሰላም ይሻለናል" ያልነው፤ ወይስ "ፖለቲካ ያለ ጦርነት አይሰራም፤ ሥልጣንም በአፈሙዝ እንጂ አይገኝም፤ ከተገኘም አይጸናም" ያሉት ናቸው? ያኔ ቢያከራክርም አሁን ላይ መልሱ ግልጽ ይመስለኛል። ለማንኛውም በኦሮሞ መካከል የሚደረግ ግጭት ሊያመጣ የሚችለውን አደጋ ለማስወገድ እውቀቴን፣ ተሰሚነቴን እና ጊዜዬን ሳልቆጥብ ሙከራ በማድረጌ በጣም እኮራለሁ። እየመጣ ያለውን አደጋ አይቼ በዝምታ ብመለከት ኖሮ ዛሬ በፀፀት እንገበገብ ነበር።

## 8.7. የኦሮሞ አመራር መማክርት

ወደ ሀገር ቤት እንደተመለስኩ የኦሮሞ አመራር እና ምሁራን ተወያይተው የጋራ አቋም እና ግንዛቤ በመያዝ ሽግግሩን ለማሳካት በጋራ እንዲሰሩ ጥረት ማድረግ ጀመርን። ወደ ሀገሬ የመጣሁበት አንዱ ዓላማም ይሄው ነበር። ከፕሮፌሰር ሕዝቅኤል ገቢሳ ጋር በተለያዩ ቦታዎች ከምሁራን እና ከሕዝቡ ጋር ውይይት ካደረግን በኋላ ውይይቱ በአመራር ደረጃ በተደራጀ እና ዘላቂነት ባለው አኳኋን እንዲቀጥል ወሰንን። ይህንንም "Center for Development and Capacity Building (CDCB)" የተባለ መንግሥታዊ ያልሆነ ድርጅት እንዲያመቻች ተስማማን። በወቅቱ እየተንቀሳቀሱ የነበሩ የሁሉም የፖለቲካ ፓርቲ አመራሮች ባሉበት ከተለያዩ ዩኒቨርሲቲዎች የተመረጡ ምሁራንን በማሰባሰብ ውይይት ማካሄድ ጀመርን።

ጥር 2019 ውይይቱ ተጀምሮ ለስድስት ወራት ያህል ቀጠለ። የመጀመሪያው ቀን እኔ እና ፕሮፌሰር ሕዝቅኤል በወቅታዊ ሁኔታዎች፣ ከፊታችን ያሉ ዕድሎች እና አደጋዎች ላይ ሰፊ ትንታኔ አቀረብን። የታለመው ሽግግር እየተደናቀፈ እንደሆነ እና ሀገሪቷ ወደ እርስ በእርስ ጦርነት እየተንደረደረች መሆኗን የሚያሳዩ ዋና ዋና ጠቋሚዎችን (indicators) ዘርዝረን አቀረብን። ከዚያም በየሳምንቱ ምሁራን፣ አመራሮች እና ወታደራዊ ሹማምንት ወቅታዊውን ሁኔታ በተመለከተ ስለሚኖሩ ዕድሎች እና ሊያጋጥሙን ስለሚችሉ አደጋዎች ትንታኔ ማቅረብ ቀጠሉ። አቶ ሌንጮ ለታ፣ ጄኔራል ዓለምሸት ደግፌ፣ ገረሱ ቱፋ፣ ዶ/ር ታደሰ በሪሶ እና ሌሎችም ፖለቲካዊ፣ ኢኮኖሚያዊ፣ ማኅበራዊ እና ጸጥታ ነክ ጉዳዮች ላይ የጥናት ጹሑፎችን አቅርበው ተወያየንባቸው። ለሳምንታት በዚህ መልኩ ውይይት ከተካሄደ በኋላ የፖለቲካ ፓርቲዎች ብቻ እንዲቀጥሉ እና የጋራ አቋም እንዲያዘጋጁ ተወሰነ።

ከእያንዳንዱ ፓርቲ ሊቀመንበሩን እና ምክትል ሊቀመንበሩን ጨምሮ ሦስት ሰዎች እንዲሳተፉ፤ CDCB እንደ ድርጅት፣ እኔ ደግሞ እንደ ግለሰብ ውይይቱን እንድናስተባብር ተመደብን። የኦሮሞ ጥያቄ ምንድነው በሚለው ጀምረን ኢኮኖሚያዊ፣ ማኅበራዊ እና ፖለቲካዊ ጉዳዮችን አንድ በአንድ ለይተን ተከራከርን፣ ተወያየን። ለስድስት ወራት ያህል በየሳምንቱ እየተገናኘን ውይይት ከአካሄድን በኋላ "የኦሮሞ የፖለቲካ ፓርቲዎች የጋራ አቋም" የሚል ገዢ ሰነድ አዘጋጀን። ሰነዱ ውስጥ የሰፈረው የጋራ አቋም በኦሮሞ ውስጥ ለረጅም ጊዜ አወዛጋቢ በሆኑ ጉዳዮች ላይ ክርክር እና ድርድር ተካሂዶ የሁሉም ፓርቲ አመራሮች ስምምነት የደረሱበት ነው። በተጨማሪም "የኦሮሞ ፖለቲካ ድርጅቶች የሥነ-ምግባር ቃል ኪዳን" ሰነድም ተዘጋጀ። ይህንን ስምምነት ተግባራዊ ለማድረግም የኦሮሞ አመራር ምክር ቤት (Oromo Leadership Council) እንዲቋቋም ስምምነት ላይ ተደረሰ።

የስምምነት ሰነዱን ለሕዝብ ይፋ ለማድረግ የፊርማ ሥነ-ሥርዓት እያዘጋጀን ሳለን አቶ አበራ ቶላ የኦሮሞ የፖለቲካ ፓርቲ አመራሮችን ለማቀራረብ የሚረዳ ዓውደ ጥናት ማዘጋጀት እንደሚፈልግ፤ ይህንንም ከጠ/ሚኒስትር ዐቢይ አሕመድ ጋር ተወያይቶ ቀጥልበት እንዳለው ነገረኝ። በበኩሌ በፖለቲካ መሪዎች መካከል ሲደረግ የነበረው ውይይት እየተጠናቀቀ በመሆኑ

ዓውደ ጥናቱን እና የፊርማ ሥነ ሥርዓቱን ማዋሐድ እንደምንችል ሐሳብ አቅርቤለት ተስማማን። በዚሁ መሠረት በስካይላይት ሆቴል የሁለት ቀናት ስብሰባ ተካሄደ። ዓውደ ጥናቱ የመንግሥት እና የተቃዋሚ ፓርቲ መሪዎች በጥሩ መንፈስ የተሳተፉበት ነበር። በጥቅሉ እያንዳንዱ ፓርቲ በአሥር ሰው ተወከለ። በመንግሥት በኩል ለማ መገርሳ፣ አዳነች አቤቤ፣ ሽመልስ አብዲሳ፣ አዲሱ አረጋ እና ሌሎችም ተሳተፉ። ከተቃዋሚዎች ዳውድ ኢብሳ፣ ምክትሉ አራርሶ ቢቂላ፣ ፕሮፌሰር መረራ ጉዲና እና በቀለ ገርባን ጨምሮ ብዙ አመራሮች ተገኝተዋል። ጀኔራል ከማል ገልቹ፣ አባ ነጋ ጃራ፣ አቶ ሌንጮ ለታ እና አቶ ገላሳ ዲልቦም ታድመዋል።

የውይይቱ ተሳታፊዎች በሰብዓዊነት እና በኦሮሞነት ስሜት ከልብ የመነጨ ሐሳባቸውን ሲያቀርቡ ቆዩ። ጉምቱ መሪዎች ያሳለፉትን ውጣ ውረድ ሲናገሩ ብዙ ታዳሚዎች ያለቅሱ ነበር። በዓውደ ጥናቱ ሁለተኛ ቀን መጨረሻ ላይ የጋራ ስምምነቱ ላይ ለመፈረም ታቅዶ ስለነበረ ጠቅላይ ሚኒስትሩ እንደሚገኙ ተነገረን። መርሐ ግብሩ በሁለት መልኩ እንዲዘጋጅ ስምምነት ላይ ደረስን። እንዱ ጠቅላይ ሚኒስትሩ ያለ መገናኛ ብዙኃን ተሳትፎ መልዕክቱን በዝግ ስብሰባ ለተሳታፊዎች የሚያስተላልፍበት ሲሆን፣ ሁለተኛው በሚዲያ የሚተላለፍ ነበር። ጠቅላይ ሚኒስትሩ በሚዲያ ያልተላለፈ የመዝጊያ ንግግር ሲያደርግ ኦሮሞ ከአርባ ዓመታት በፊት ያነሳቸውን ጥያቄዎች ዛሬም ተሸክሞ መኬድ እንደሌለበት ተናገረ። የተናገረበት ስሜት እና የንግግሩ ዓውድ እዚያ የነበሩትን አንጋፋ ታጋዮች ቅር አሰኘ። ለመገናኛ ብዙኃን ክፍት በነበረው ዝግጅት ላይ ስምምነቱ የሚፈረምበት ጊዜ ሲደርስ የሁሉም ድርጀቶች ሊቀመንበሮች እንዲፈረሙ የተወሰነ ቢሆንም፤ ጠ/ሚኒስትር ዐቢይ ግን ምክትሉ ለማ መገርሳ እንዲፈርም ወከለው። እኛም የአቶ ለማ መገርሳን ውክልና የኦሕዴድ እና የመንግሥት አቋም አድርገን ወሰድን። የጋራ አቋሙን እንደፈረምን የአመራር ካውንስሉን የሚያስተባብሩ ሰዎች ተመርጠው ለማን ሊቀመንበር አድርገን ሾምን።

ከሳምንት በኋላ ከሁሉም ፓርቲ መሪዎች እና ከለማ መገርሳ ጋር በመሆን በአቶ አበራ ቶላ ቢሮ ተገናኝተን ስለሚከናወኑ ሥራዎች በዝርዝር ከተወያየን በኋላ ካውንስሉ መስራት ያለባቸውን ሁለት ጉዳዮችን ለይተን አስቀመጥን። አንደኛው በምዕራብ ኦሮሚያ እየተባባሰ ያለውን ግጭት የሚመለከት ሲሆን፣ ሁለተኛው በመጪው ሀገራዊ ምርጫ ላይ ያተኮረ ነበር። ይህንን እቅድ ይዘን ጠቅላይ ሚኒስትሩ ጋር ሄድን። በሁለቱ አጀንዳዎች ላይ ኢኮኖሚም እንዲጨመር ምክረ-ሐሳብ አቅርቦ ተስማምተን ተቀበልን።

የምዕራብ ኦሮሚያን ጉዳይ አስመልክቶ፣ ጠ/ሚኒስትር ዐቢይ አሕመድ «ኦነግ ቀድሞውንም ወደ ሀገር ሲገባ ለውጡን ለማደናቀፍ አቅዶ ነው» ሲል በቁጣ ተናገረ። እንደማስረጃ ካቀረበው ምክንያት አንዱ፣ የኦነግ አመራር ለራሱ በአውሮፕላን ፊንፊኔ ሲገባ ሠራዊቱን በሱዳን ወደ ወለጋ ማስገባቱ ለሰላም ዝግጁ እንዳልሆነ ያሳያል በማለት ከሰሰ። በሁለተኛ ደረጃ ሰኔ 16 ቀን 2010 ዓ.ም በመስቀል አደባባይ በተደረገው የድጋፍ ሰልፍ ላይ የተፈጸመውን ጥቃት ኦነግ እንዳቀነባበረ ተናገረ። «ሊገድለኝ ከሞከረው ዳውድ ኢብሳ ጋር እንዴት አምኜ አብሬው ልሰራ እችላለሁ?» ብሎ ቁጣ አዘል ቅሬታ አቀረበ። በዚህ ጊዜ ተሳታፊው ሁሉ በድንጋጤ ክው አለ። አቶ ዳውድ ኢብሳ በበኩሉ በጥቃቱ ውስጥ እጁ እንደሌለበት በመሞገት አስተባበለ። ጠ/ሚኒስትር ዐቢይ ያቀረበው ክስ አዲስ ስለሆነና በዚያ መድረክ ላይ ለመወያየት አስቸጋሪ ስለነበር፤ ሁለቱ ለብቻ ተነጋግረው መተማመን ላይ በመድረስ እንዲፈቱት ወሰንን። እነርሱም ከቀናት በኋላ ተገናኝተው እንደጨረሱ አሳወቁን።

የአመራር ካውንስሉ ለመሥራት የሞከረው ሁለተኛው አጀንዳ የ2012 ዓ.ም ምርጫ ዝግጅት ነበር። ይህን አጀንዳ በኃላፊነት ለማስኬድ በፕሮፌሰር መረራ ጉዲና የሚመራ እና እኔም የምሳተፍበት ኮሚቴ ተቋቋመ። በምርጫ ላይ ለመሥራት የተፈለገበት ሁለት ምክንያቶች ነበሩ። በመጀመሪያ፣ ከሽግግሩ በኋላ ለመጀመሪያ ጊዜ የሚካሄደው ምርጫ በሰላማዊ መንገድ መካሄድ መቻሉ ለዴሞክራሲያዊ ሥርዓት ግንባታ ወሳኝ ስለሆነ ነው። በተለይ ኦሮሚያ ውስጥ ሰላማዊ ምርጫ ማካሄድ ከተቻለ ለመላው ሀገሪቱ ስኬት ጠቃሚ ይሆናል ከሚል እሳቤ በመነሳት ነው። ከዚህ ቀደም ሥልጣንን በሰላማዊ ፉክክር የመያዝ ባሕል በሌለበት ሀገር በምርጫ ቅስቀሳ እና ውጤቱ በሚገለጽበት ወቅት ሁከት የመፈጠር ዕድሉ ሰፊ ነው። እንደዚህ ዓይነቱን ሁከት ለማስወገድ ፓርቲዎች አስቀድመው መተማመን እና መስማማታቸው አስፈላጊ ነበር። ካውንስሉ በምርጫ ጉዳይ ለመወያየት የፈለገበት ሁለተኛው ምክንያት የኦሮሞ ድምፅ በብዙ ፓርቲዎች መሀል ተከፋፍሎ በትልቅ መሥዋዕትነት የተገኘው ለውጥ ለአደጋ ሊጋለጥ ይችላል የሚል ሥጋት ነበር።

ከምርጫ ጋር ተያይዞ የሚፈጠር ሁከትን ለማስወገድ እና የድምፅ መባከንን ለመቀነስ የኦሮሞ ፓርቲዎች አስቀድመው መደራደራቸው እና መስማማታቸው ይጠቅማል ብለን አሰብን። ይህ ማለት የጊዜው ነባራዊ ሁኔታ ሙሉ በሙሉ በፉክክር ላይ የተመሠረተ ምርR (competitive election) ለማድረግ አመቺ ባለመሆኑ፣ ፓርቲዎች ሥልጣንን ለመጋራት ቀድመው የተስማሙበት ምርጫ (pre-negotiated election) ማካሄድ አስፈላጊ ብቻ ሳይሆን ግዴታ ሆኖ አገኘነው።

በዚህም መሠረት በወቅቱ የነበሩት አምስት ፓርቲዎች በኦሮሚያ ያለውን የምርጫ ወንበሮች እንዲከፋፈሉ የሚያስችል ቀመር ተዘጋጀ። ፓርቲዎቹም ኦዴፓ (ጠ/ሚኒስትር ዐቢይ አሕመድ)፣ ኦፌኮ (መረራ ጉዲና)፣ ኦነግ (ዳውድ ኢብሳ)፣ የተባበረው ኦነግ (አባጃራ ነጋ) እና የኦሮሞ ብሔራዊ ፓርቲ (ከማል ገልቹ) ነበሩ። የኦሮሚያ እና የፌደራል ምክር ቤት መቀመጫዎችን እንዴት እንደሚከፋፈሉ የተለያዩ ቀመሮች ቢቀርቡም ስምምነት ላይ መድረስ አልተቻለም። በኦዴፓ በኩል በሁለቱም ምክር ቤቶች (ክልል እና ፌደራል) አብላጫ ድምፅ መያዝ ፈለጉ። በተቃዋሚዎች በኩል ሁለት ችግሮች ነበሩ። አንደኛው ኦዴፓ አብላጫ ድምፅ ይዞ ከቀጠለ፣ የትላንትናውን አምባገነንነት መልሶ ሊያመጣ ይችላል የሚል ሥጋት ሲሆን፤ ሌላኛው በተቃዋሚዎቹ መካከል ወንበር የሚከፋፈልበት ቀመር ላይ አለመስማማት ነበር።

ይህንን ክፍተት ለማጥበብ የተለያዩ አማራጮች ቀረቡ። ከእነዚህ አማራጮች አንዱ ኦዴፓ የፌደራል ምክር ቤት ወንበር በበላይነት እንዲወስድና የጠቅላይ ሚንስትርነቱን ሥልጣን እንዲይዝ፤ ተቃዋሚዎች ደግሞ በኦሮሚያ አብላጫውን መቀመጫ ወስደው፣ የኦሮሚያን በበላይነት ያስተዳድሩ የሚል ነበር። የዚህ እሳቤ መነሻ ኦዴፓ በፌደራል ደረጃ የበላይነት እንዲይዝ መፍቀድ፣ ጠ/ሚኒስትር ዐቢይ በጠቅላይ ሚኒስትርነት እንደሚቀጥል ዋስትና መስጠት ስለሆነ ስምምነቱን ሊቀበል ይችላል የሚል ነው። በተመሳሳይ መልኩ ተቃዋሚ ፓርቲዎች ኦሮሚያን የማሥተዳደር ሥልጣን ከተሰጣቸው ኦዴፓ አምባገነን ይሆናል የሚለው ሥጋታቸው ስለሚቃለል፤ እንዲሁም የዳበው ተቋዳሽ ስለሚሆኑ ለአመጽ የሚኖራቸውን ፍላጎት ለማስቀረት ይረዳል የሚል ነበር። ሆኖም ፌደራልን ለኦዴፓ፣ ክልልን ለተቃዋሚ የሚለው እሳቤ ላይ መግባባት አልተቻለም።

በተቃዋሚ ድርጅቶች መካከልም በወንበር ክፍፍል ቀመር ላይ ስምምነት ጠፋ። ነባር ፓርቲዎች አብላጫው ወንበር ሊሰጠን ይገባል ሲሉ፣ አዲሶቹ ደግሞ ለሁሉም እኩል ክፍፍል እንዲኖር ተመኙ። በሕዝቡ ውስጥ ያላቸውን ድጋፍ፣ ያን ድጋፍ ወደ ምርጫ ውጤት ለመቀየር የሚያስችል ድርጅታዊ ቁመና ከግምት ባስገባ መልኩ፣ እንዲሁም የሰጥቶ መቀበልን መርህ በመከተል በተመጣጣኝነት (proportionally) መከፋፈል ላይ መስማመት አልቻሉም። በአብዛኛው ከራሳቸው የማሸነፍ ዕድል እና የተጋነነ ግምት በመነሳት እንጂ እውነተኛ አቅማቸውንም ሆነ ነባራዊ የሀገሪቷን ሁኔታ ከግንዛቤ ለማስገባት ፈቃደኛ አልነበሩም።

በኦሕዴድ (ኦዴፓ) እና በተቃዋሚዎች መካከል ያለ ልዩነት ብቻ ሳይሆን በለማ መገርሳና በጠ/ሚኒስትር ዐቢይ አሕመድ መካከል እየተባባሰ የነበረው መቃቃርም የካውንስሉ ጥረት እንዳይሳካ እንቅፋት ፈጥሯል። ለማ መገርሳ ከኦሮሚያ ፕሬዝዳንትነት ከተነሳ በኋላ የሁለቱ ግንኙነት እየሻከረ ሄደ። በጠ/ሚኒስትር ዐቢይ በኩል ለማ መገርሳ ካውንስሉን በመጠቀም የተቃዋሚዎችን ድጋፍ አግኝቶ ከጠቅላይ ሚኒስትርነት ሊገፋው እንደሚፈልግ ጥርጣሬ ነበር። ጠ/ሚኒስትር ዐቢይ፣ ለማ ኦዴፓን በካውንስሉ እንዲወክል መድቦ የካውንስሉ ሊቀመንበር አድርገን ብንሾመውም፤ በድርጅታቸው ውስጥ የሁለቱ ግጭት እየተባባሰ ስለመጣ፣ ለማ በካውንሰሉ ሥራ ላይ በልበ ሙሉነት ሊሳተፍ አልቻለም። በኋላ ለማ ሙሉ በሙሉ ቀርቶ በሽመልስ አብዲሳ ተተካ። ብዙም ሳይቆይ በተደረጉ ድርጊቶች እና ሁኔታዎች ጥርጣሬው ተባብሶ መማክርቱ የታሰበለት ቦታ ሳይደርስ ተጨናገፈ።

# ክፍል ዘጠኝ – የለውጡ መጓሸራተት

## 9.1.የእኔ እና የመንግሥት ግንኙነት ከድጡ ወደ ማጡ

ጠ/ሚኒስትር ዐቢይ ወደ ሥልጣን ከመጣ በኋላ ተቃውሞዬን በልቤ ይዤ ሽግግሩ እንዲሳካ ለማገዝ ወሰንኩ። ገና ከጅምሩ የኦሮሞን ትግል የሚቃረኑ ትርክቶችን እና ወደ ዴሞክራሲ የሚደረገውን ሽግግር ሊያደናቅፉ የሚችሉ እርምጃዎችን እየወሰዱ ስለነበር፤ በአመራራቸው ላይ ያለኝ ፍርሀት እና ጥርጣሬ እየበረታ መጣ። ይሁን እንጂ ከሩቅ ከመተቸት ይልቅ ሂሳዊ ድጋፍ (critical support) እየሰጡ ሽግግሩን ለማሳለጥ መሞከርን መረጥኩ። ወደ ሀገር ቤት ከተመለስኩ በኋላ ከጠ/ሚኒስትር ዐቢይ ጋር በተለያዩ ጊዜያት ተገናኝተን ስንወያይ በብዙ ጉዳዮች ላይ ብንስማማም በተግባር ግን መንግሥት ተቃራኒውን ይፈጽም ነበር።

ሀገሪቱን ወደ ዴሞክራሲ ለማሸጋገር በተደጋጋሚ ቃል ቢገቡም በተጨባጭ የሚወሰዱ እርምጃዎች አዲስ አምባገነናዊ ሥርዓት ለመገንባት መንደርደሪያ መሆናቸውን ጠቆሙ። በመሠረቱ ሀገሪቷን ወደ ዴሞክራሲ ለማሸጋገር የአውራ ፓርቲ (Dominant Single Party) ሥርዓትን ትቶ የመድበለ ፓርቲ (Multiparty) ሥርዓት መገንባት አስፈላጊ ቢሆንም፤ እያየን የመጣነው ከአንድ ፓርቲ አምባገነንነት ወደ አንድ ግለሰብ የበላይነት (Autocratic/Sultanistic Dictatorship) የመሸጋገሪያ አካሄድ ነበር ። ነባሩን ሕብረብሔራዊ የፌደራሊዝም ሥርዓትን ዴሞክራሲያዊ ከማድረግ ይልቅ በማፍረስ በአሃዳዊ አገዛዝ የመተካት እቅድም እንዳለ ብዙ ጠቋሚ እርምጃዎችን ማየት ጀመርን።

አወዛጋቢ ትርክቶችን በማቅረብ፣ አዲስ አምባገነናዊ ሥርዓት ለመገንባት መመኘት ወይም ፌደራሊዝምን ለማጥፋት መሞከር በሀገሪቱ ላይ ከፍተኛ አደጋ ሊያደርስ እንደሚችል በተለያዩ ጊዜያት በቃልም ሆነ በጽሑፍ ለማስጠንቀቅ ብሞክርም ሰሚ አላገኘሁም። ለምሳሌ ዩጎዝላቪያን ያፈረሱ ሁኔታዎች ላይ ትንታኔ በመጻፍ ኢትዮጵያንም ተመሳሳይ ችግሮች እንዳያጋጥሟት መወሰድ ያለባቸውን እርምጃዎች ለመጠቆም ስሞክር ሥጋቴን ከማዳመጥ ይልቅ በቁጣ ማጣጣል ይታይ ነበር።

መጀመሪያ አካባቢ በጠ/ሚኒስትር ዐቢይ አሕመድ የአመራር አካሄድ ላይ ያለኝን ትችት በይፋ (publicly) ከመግለጽ ብቆጠብም፤ በአጋጣሚ በቀጥታ ስንገናኝ ወይም በሰዎች በኩል ከመግለጽ ግን አልተቆጠብኩም። በተለይ ለማ መገርሳ፣ ዶ/ር ወርቅነህ ገበየሁ እና ብርሃኑ ጸጋዬ ጋር ብዙ ጊዜ በመመላለስ መወትወቴን አላቆምኩም። በእኔ እና በጠ/ሚኒስትር ዐቢይ መካከል ያለው የሐሳብ መራራቅ ስላሳሰባቸው ለማጥበብ ብዙ ሞክረዋል፤ በኋላ ግን እነሱ ራሳቸው ከመንግሥት ተገፍተው ወጡ።

ለማ መገርሳ ከኦሮሚያ የመነሳቱ ጭምጭምታ እንደተሰማ ምክንያቱን ስጠይቅ "ጠቅላይ ሚኒስትሩ ሥራ ስለሚበዛባቸው እሳቸውን ለማገዝ ወደ ፌደራል ሄዶ ነው" አሉኝ። እኔም ይህንኑ በማመን በለማ መገርሳ መነሳት ያኮረፈውን ሕዝብ በሚዲያ በኩል ለማረጋጋት ሞከርኩ። በኋላ ግን ለማ መገርሳ ያለ ፍቃዱ እና ፍላጎቱ መነሳቱን ከራሱ ተረዳሁ። የለማ መገርሳ ነገር እያሳሰበን ባለበት ሁኔታ የአራት ድርጅቶች ጥምረት የሆነውን ኢሕአዴግ አዋሕዶ ወደ አንድ ፓርቲ ለመቀየር እንደታቀደ ሰማን። ይህንኑ እቅድ ተግባራዊ ለማድረግ የመደመር መጽሐፍ ረቂቅ ቀረበ። የለማ መገርሳ መገፋት እና ገዢውን ፓርቲ ለማዋሐድ መታቀዱ በኦሮሞ እና በሌሎች ብሔር ብሔረሰቦች መካከል አለመረጋጋትን በመፍጠር አደጋ ሊያመጣ ይችላል ብዬ ስለጠረጠርኩ ከአቶ ሌንጮ ለታ ጋር በመሆን ጠቅላይ ሚኒስትሩን አነጋገርን።

በለማ መገርሳ ጉዳይ ምንም ዓይነት ግጭት እንደሌላቸውና እንደቀድሞው በፍቅር አብረው እየሰሩ መሆናቸውን ነገረን። ለማ መከፋቱን ካንደበቱ መረዳቴን ሳብራራ፤ «አይ ተሳስተኸል። ለማ ምንም አልተከፋም። አዲስ ነገር ካለ አነጋግሬው እፈታለሁ» አለኝ። ስለ ኢሕአዴግ ውሕደት ብዙ ሊያወራን አልፈለገም። የመደመር መጽሐፍ እየተዘጋጀ እንደሆነና እቅዱን እዚያ ውስጥ እንደምናገኝ በመንገር፤ የመጽሐፉን ረቂቅ (draft) እንደሚልክልን ቃል ገባልን። በእኛ በኩል ኢሕአዴግን ማክሰም ጊዜው እንዳልሆነና ሽግግሩን ሊጎዳ እንደሚችል ለማስረዳት ሞከርን። በሥጋትነት ያቀረብነው ምክንያት በ ገዢው ፓርቲ ውስጥ ግጭት ሊያባብስ ይችላል የሚል ነው። በተለይ ከሕወሓት ጋር ያለውን የሻከረ ግንኙነት የበለጠ ሊያባብሰው እንደሚችል ሥጋታችንን በመግለጽ፤ ኢሕአዴግን ከማፍረስ በፊት ከሕወሓት ጋር የተፈጠረውን ልዩነት መፍታት እንደሚያስፈልግ አሳሰብን። ይህን ዓላማ ለማሳካት በኦሮሚያ እና በትግራይ በኩል ያሉ ጉምቱ መሪዎች ቢነጋገሩ የሚል ሐሳብ አቅርበን እርሱም ተስማማ። ከሁለቱም ወገን ቢገናኙ ይጠቅማሉ ያልናቸውን ሰዎች ስም ጠቀስን። እርሱም እነዚያን ሰዎች አነጋግረን እንድናስፈጽም ጠየቀን። ይህንን ሐሳብ ለትግራይ ሰዎች ስናቀርብ በደስታ የተቀበሉት ቢሆንም የታሰበው ሽምግልና ከመተግበሩ በፊት የሀገሪቱ ፖለቲካ ተባባሰ።

እኔና አቶ ሌንጮ ለታ ጠቅላይ ሚኒስትሩን አነጋግረን ብዙም ሳይቆይ ቃል በገባው መሠረት የመጽሐፉን ረቂቅ ላከልን። አንብቤ ለእርምት ይጠቅማል ብዬ ያሰብኩትን ትችት አዘጋጀሁ። መልሶ የጠየቀኝ ግን አልነበረም። ከአቶ ሌንጮ ጋር ተገናኝተን ትችታችንን እንዴት ማቅረብ እንዳለብን ስንመክር፤ ሁሉም የኦዴፓ ሥራ አሥፈፃሚ ኮሚቴ በተገኙበት ማቅረቡ የተሻለ እንደሚሆን ተስማማን። ወደ ብርሃኑ ጸጋዬ ሄጄ ስለዚህ ሐሳብ ነገርኩትና ከጠ/ሚኒስትር ዐቢይ ጋር ተነጋግሮ የውይይት መድረክ እንደሚያዘጋጅ አሳወቀኝ። ከዛሬ ነገ መድረኩ ይዘጋጃል ብለን ስንጠብቅ ብርሃኑ በዚያው ዝም አለ። ጥሩ ምላሽ ከጠ/ሚኒስትርሩ እንዳላገኘ ተረድተን ሐሳባችንን ለመተው ተገደድን።

አንድ ቀን ሽመልስ አብዲሳ ደወለና በመደመር መጽሐፍ ላይ በቢሾፍቱ ውይይት ስለሚደረግ አወያይ እንድሆን ጋበዘኝ። ረቂቁን አንብቤ ያዘጋጀሁትን ትችት ከማቅረቤ በፊት መጽሐፉ ከታተመ በኋላ መጋበዜ እንደገረመኝ ነገርኩት። በመጽሐፉ ውስጥ የተካተቱ ብዙ ሐሳቦችን ስለማልደግፍ አወያይ መሆን እንደማልችል ገለጽኩለት። እርሱ ግን ቢያንስ እንደ ተሳታፊ ቀርቤ ትችቴን እንዳቀርብ ጠየቀኝ። በሐሳቡ ተስማምቼ በማግስቱ ወደ ቢሾፍቱ አቀናሁ።

በዚያ ስብሰባ ላይ ምሁራን መጽሐፉን አንብበው መጥተው ገንቢ አስተያየቶችን እንደሚሰጡ

ተነግሮኝ የነበረ ቢሆንም በአዳራሹ ያየሁት ሌላ ነበር። የዩኒቨርስቲ መምህራን፣ የማኅበራዊ ሚዲያ አንቂዎች፣ የሀገር ሽማግሌዎች፣ የፓርቲ ካድሬዎች እና ባለሀብቶች ተደባልቀዋል። ብዙ ሰዎች መጽሐፉን እንዳላነበቡት አጠገቤ ከተቀመጡት ተረዳሁ። ስብሰባው እንደተጀመረ የኦዴፓ ከፍተኛ ካድሬዎች ስለ መጽሐፉ ይዘት ተራ በተራ ማቅረብ ጀመሩ። ካቀረቧቸው ሐሳቦች መረዳት እንደሚቻለው ተሳታፊዎቹ ብቻ ሳይሆኑ አቅራቢዎቹም መጽሐፉን እንዳላነበቡት ፍንትው ብሎ ይታይ ነበር።

ካድሬዎቹ ቀኑን ሙሉ ሲያቀርቡ ውለው ማምሻውን ከተሳታፊዎች ጥያቄ እና አስተያየት ለመቀበል ዕድል ተሰጠ። ጥያቄ ለመጠየቅ ወይም አስተያየት ለመስጠት ፍላጎት አልነበረኝም። በኋላ ላይ መድረክ መሪው በስም ጠርቶ አስተያየት እንድሰጥ ጋበዘኝ። እኔም መጽሐፉ እሁን መታተም እንዳልነበረበት እና ብዙ የማሻሻያ ሥራ እንደሚያስፈልገው ተናገርኩ። ከሁሉም በላይ ኦሮሞን ከራስ የማራቅ እና ሌሎችን የማቅረብ አካሄድ ትክክል አለመሆኑን አንስቼ ተቸሁ። ምክንያቱ ደግሞ እኛ ለዚህ ውይይት ከመጠራታችን በፊት ዶ/ር ብርሃኑ ነጋ እና ሌሎች የተቃዋሚ ፓርቲ አመራሮች በመጽሐፉ ላይ በአማርኛ በተካሄደ ውይይት ላይ ተጋብዘዋል። በአፋን ኦሮሞ በተካሄደው ስብሰባ ላይ እንጋፋ የኦሮሞ የፖለቲካ መሪዎች የሆኑት አንዳቸውም አልተጋበዙም። ይህ መንግሥት እና ጠቅላይ ሚኒስትሩ ውግንናቸው ከጊዜ ወደ ጊዜ ከኦሮሞ እየራቀ መሆኑን ያሳያል በማለት ቅሬታዬን በቁጣ አቀረብኩ። አወያዮቹ በቁጣዬ ስለተደናገጡ የዕለቱ ውይይት በዚያው እንዲገባደድ ተደረገ።

በማግስቱ ከሰዓት በኋላ ጠ/ሚኒስትር ዐቢይ አሕመድ መጥቶ ለታዳሚው ንግግር አደረገ፤ እንደተናደደ ግልጽ ነበር። «መሳተፍ ያልነበረባቸውን ጋብዘናል» በማለት ፀፀቱን ገለጸ። ይህንን ሐሳብ ለሚቃወም ቡድንም ሆነ ግለሰብ ምንም ዓይነት ትዕግሥት እንደሌለው ጠቆመ። በአብዛኛው ንግግሩ ማስፈራሪያ ነበር፤ ከስብሰባው በኋላ እራት ጎን ለጎን ሆነን ስንበላ ላናግረው ብሞክርም አኮረፈኝ።

ስብሰባው ተደርጎ ከሳምንት በኋላ የጠቅላይ ሚኒስትሩን አካሄድ የምቃወምበትን ምክንያት ገልጬ ረጅም ጽሑፍ ፌስቡክ ላይ አሰፈርኩ። «ኢሕአዴግን ማፍረስ ወይስ ማደስ ይሻላል?»

በሚል ርዕስ ሥር የ ገዢውን ፓርቲ ጥምረት (coalition) ወደ አንድ ፓርቲ መቀየር ሊያመጣ የሚችለውን ጉዳት ዘርዝሬ ጻፍኩ። ኢሕአዴግን ከጥምረት ወደ አንድ ፓርቲ ለመቀየር የቀረበው ምክንያት በብሔር ስም የሚመሠረት ፓርቲ እንዳይኖር ታስቦ ስለሆነ፣ በብሔር መደራጀትን መከልከል የሀገሪቱ ሕዝቦች ጥቅም እና መብታቸውን ተደራጅተው ለማስከበር ያላቸውን አቅም ይቀንሳል የሚል ሥጋት ስለነበረኝ ነው። ይህ አስተሳሰብ ገዢውን ፓርቲ ብቻ ሳይሆን ተቃዋሚዎችን ወደ ማገድም ሊሄድ እንደሚችል ገምቼ ነበር። ሥጋቴን የበለጠ ያጠናከረው በወቅቱ በብሔር የተደራጁ ፓርቲዎችን የማገድ ዘመቻ ይደረግ የነበረ ከመሆኑም በላይ ዘመቻውን የሚያካሄዱት ቡድኖች ለጠቅላይ ሚኒስትሩ ቅርበት ነበራቸው። ኢሕአዴግን አክስሞ የብሔር ድርጅቶችን ለማፍረስ መንገድ መጥረግ የሀገሪቱን ጭቁን ብሔሮች ይጎዳል የሚል ጠንካራ ሥጋት ነበረኝ። እንደ ብሔር የተጨቆነ ሕዝብ የጋራ መብቱን እና ጥቅሙን ማስጠበቅ የሚችለው በማንነቱ መደራጀት ሲችል ስለሆነ፤ በብሔር ማንነቱ የተበደለን ሕዝብ በብሔር እንዳይደራጅ መከልከል በዚያ በደል ውስጥ እንዲቆይ መፍረድ ነው። ለውጡ የብሔሮችን መብት የበለጠ በማስከበር ለጠንካራ ፌደራላዊ እና ዴሞክራሲያዊ ሥርዓት ግንባታ መሠረት ይጥላል ተብሎ በሚታመንበት ወቅት በብሔር መደራጀትን መከልከል አመጽ እና ግጭት ሊያስከትል ይችላል የሚል ነበር ፍራቻዬ።

ሕብረብሔራዊ በሆነ ሀገር ውስጥ በልሂቃን (elite) መካከል ድርድር እና ስምምነት (bargain/negotiation and consensus)መደረጉ ግጭትና መድሎን ለመቀነስ እንዲሁም የተረጋጋ ዴሞክራሲያዊ ሥርዓት ለመገንባት ጠቃሚ ነው የሚለው ደግሞ ሁለተኛው ምክንያት ነበር። በመሠረቱ ጥምር ፓርቲ ማለት የፖለቲካ ልሂቃን ሀገርን ለማሥተዳደር የሚደራደሩበት መድረክ (bargaining forum) ነው። ሀገር ከአንድ ወጥ ፓርቲ የበላይነት ይልቅ፣ በተለያዩ ፓርቲዎች ጥምረት መተዳደሯ ለድርድር ዕድል ይሰጣል። ይህም የአንድ ቡድን አመለካከት ወይም ፍላጎት ብቻውን እንዳይተገበር ይረዳል። አመራሩ ለመደራደር እና ለመስማማት መገደዱ ጽንፈኛ እና አድሎአዊ አመለካከት ብሔራዊ ፖሊሲ ሆኖ እንዳይተገበር ዋስትና ይሆናል። በተለይ የብሔሮች ግጭት ባለባት እና ገና ወደ ዴሞክራሲ ለመሸጋገር በምትዳክር ሀገር ውስጥ በጣም አስፈላጊ ነው። በኢሕአዴግ ውስጥ የሕወሓት የበላይነት እንደነበረ የሚካድ ባይሆንም፣ የተለያዩ ፓርቲዎች ጥምረት በመሆኑ በመሪዎች መካከል የተወሰነ ውይይት እና ስምምነት ይደረግ ነበር። ስለዚህ የገዢውን ፓርቲ ግድፈቶች ለመቅረፍ አስፈላጊው እርምጃ ኢሕአዴግን ዴሞክራሲያዊ በማድረግ ፍትኃዊ ድርድር እና ስምምነት ወደሚካሄድበት መድረክ መቀየር ይሻላል የሚል አቋም ነበረኝ።

ኢሕአዴግ ላይ የሚቀርቡ ሁለት ቅሬታዎች ነበሩ። አንደኛው አባል ፓርቲዎች በድርጅቱ አመራር ውስጥ ያላቸው ውክልና ፍትኃዊ አይደለም የሚል ሲሆን፤ ሁለተኛው 'ታዳጊ' ክልሎችን የሚያስተዳድሩ ፓርቲዎች ፌደራል መንግሥቱን ከሚያስተዳድረው ጥምረት መገለላቸው ነው። ለዚህ መፍትሔው ከጥምር ፓርቲ ወደ ነጠላ ፓርቲ መቀየር ሳይሆን በማደግ ላይ ያሉ ክልሎችን የሚያስተዳድሩ ፓርቲዎች በፌደራሉ ጥምረት እንዲካተቱ፤ እንዲሁም በጥምረቱ አመራር ውስጥ ሁሉም ፓርቲዎች እንደየመጡበት ሕዝብ ቁጥር ተመጣጣኝ ውክልና እንዲኖራቸው ማድረግ ነው። ገዢውን ፓርቲ ፍትኃዊ ውክልና ወደሚታይበት ሁሉን አቀፍ ጥምረት መቀየር፤ የብሔር ብሔረሰቦች አመራር እንዲወያይ እና አስፈላጊው የልሂቃን የመደራደሪያ መድረክ እንዲፈጠር ይረዳል። ይህም ሀገሪቷን የሚያስተዳድሩ የየብሔሩ ልሂቃን የሚኖራቸው ቅሬታ ወደ ሕዝቡ ሳይወርድ በአመራር ደረጃ ተደራድረው እንዲፈቱ ያስችላቸዋል።

የኢሕአዴግን ጥምረት አፍርሶ ወደ አንድ ፓርቲ መቀየርን የተቃወምኩበት ዋነኛው ምክንያት፣ እርምጃው በሕወሓት ዘንድ ተቀባይነት እንደማይኖረው እና ይህም በፌደራል መንግሥት እና በትግራይ ክልል መካከል ያለውን ግንኙነት በማባባስ ወደ እርስ በእርስ ጦርነት ሊያመራ እንደሚችል በመስጋቴ ነበር። መንግሥት እና ፓርቲ ተቀላቅለው ሀገር በሚያስተዳድሩበት ተጨባጭ ሁኔታ ውስጥ አንድን ክልል የሚያስተዳድረው ፓርቲ የፌደራሉን መንግሥት ከሚያስተዳድረው ጋር ተጣልተው ከተቆራረጡ፣ ክልሉ እና ፌደራሉ ተባብረው ለመሥራት ያላቸው ዕድል ጠባብ ይሆናል። በወቅቱ በፌደራል መንግሥት አሥተዳደር እና ጸጥታ ተቋማት ውስጥ የነበሩት የትግራይ ተወላጆች ግማሹ በውዴታ ሌላው ተገፍቶ እየወጣ ስለነበር፤ ትግራይ እና ፌደራሉን የሚያስተሳስረው ቀሪ ተቋም የኢሕአዴግ ጥምረት ነበር። ሕወሓት ከጥምረቱ ወጣ ማለት መቀሌ እና አዲስ አበባን አስተሳስራ ያለችው ብቸኛዋ ገመድ መበጠሷ ነው። በአካባቢው የፖለቲካ ኃይሎች አሰላለፍ ለውጥ ምክንያት የትግራይ ሕዝብ የሕልውና ሥጋት (existential collective insecurity) ውስጥ ገብቶ ባለበት ሁኔታ፤ በልጆቹ ደም እና አጥንት የገነባው ብሎም ለ45 ዓመታት የመራውን ድርጅት ማፍረስ ሥጋቱን አባብሶ ወደ ጦርነት ሊያመራ ይችላል ብዬ ፈራሁ።

ስለሆነም የተሻለው አማራጭ ኢሕአዴግን ከማፍረስ ይልቅ የአደረጃጀት፣ የአሠራር እና የፖሊሲ ለውጥ አድርጎ ማደስ ይሻላል በማለት ተከራከርኩ። ለዚህ መከራከሪያዬ ከጠቅላይ ሚኒስትሩ በኩል የሚሰጠው መልስ «ሕወሓት የበላይነትን ስለለመደ በጥምረቱ ውስጥ ፍትኃዊ ውክልናን አይቀበልም» የሚል ነበር። እኔ ግን ከሕወሓት አመራሮች ጋር በነበረኝ ውይይት የተረዳሁት፣ በጥምረቱ ውስጥ ያላቸው ውክልና መቀነሱ ቢያስከፋቸውም፣ በሰከነ እና ሁለገብ ድርድር ማሳመን እንደሚቻል ነው። ይህን ሐሳብ ሳቀርብ፤ «እኛ አብረናቸው ከኖርነው የበለጠ አንተ ትላንት የመጣኸው ታውቃቸዋለህ?» በማለት ያጣጥለው ነበር።

የኢሕአዴግ አባል ሳልሆን የጥምረቱን መፍረስ የተቃወምኩት ያኔ እንደምወነጀለው ለሕወሓት ለመወገን አልነበረም። የመንግሥት እና የፓርቲ መዋቅር ተደበላልቆ ባለበት ሁኔታ በገዢው ፓርቲ ውስጥ የሚፈነዳ ግጭት ሽግግሩን ከማደናቀፍ አልፎ ሀገሪቷን ወደ እርሰ በእርስ ጦርነት ያስገባል የሚል ተጨባጭ ሥጋት ስለነበረኝ ነው። ብዙ በታ ተከፋፍለው የተራራቀ ጽንፍ ላይ ከቆሙ ተቃዋሚ ፓርቲዎች ይልቅ፣ ይብዛም ይነስም ለ27 ዓመታት አብሮ የመሥራት ልምድ ያለው የኢሕአዴግ አመራር የሽግግር ወቅት መንግሥት ለመምራት የሚያስችል የተሻለ መቀራረብ አለው ከሚል ግምት ነበር።

ጽሑፉን ባወጣሁ በጥቂት ቀናት ውስጥ ጠቅላይ ሚኒስትሩ በፓርላማ ባደረጉት ንግግር ከእንግዲህ የሁለት ሀገር ፓስፖርት ይዘው በሚዲያ የሚረብሹንን አንታገስም በማለት ዛቱ። ማስጠንቀቂያውን በቀጥታ እኔ ላይ የተቃጣ አድርጌ ስለወሰድኩት በፌስቡክ በኩል ምላሽ ሰጠሁ። ወደ ሀገር የገባሁት የውጭ ፓስፖርት ወይም የኢትዮጵያ መንግሥትን ተስፋ አድርጌ ሳይሆን ፈጣሪን እና ሕዝቤን ተማምኜ እንደሆነ በመግለጽ፤ በምንም ዓይነት ማስፈራሪያ ከሀገር እንደማልወጣ እና የኦሮሞንም ትግል እንደማልከዳ ጨምሬ ጻፍኩ። ያንን መልስ የሰጠሁት በፓርላማ ንግግር ላይ ብቻ ተመስርቼ እልነበረም።

ከቢሾፍቱ የመደመር ስብሰባ ዕለት አንስቶ የመንግሥት ከፍተኛ ባለሥልጣናትን ጨምሮ ብዙ ሰዎች በስልክ እና በአካል ቀርበው ሕይወቴ አደጋ ላይ እንደሆነ እና ከሀገር እንድወጣ ሲነግሩኝ ከርመዋል። እንዲሁም በጠቅላይ ሚኒስትሩ እና በከፍተኛ ባለስልጣኖቻቸው መካከል በእኔ ላይ መወሰድ ስላለበት እርምጃ ተወያይተው ደረሱበት የተባለውን ውሳኔ ከተለያዩ ግለሰቦች ሰማቼ ነበር። እኔ ግን የምሰነዝራቸው ትችቶች ወደ መገዳደል የሚያደርሱ ስላልመሰለኝ ማስጠንቀቂያዎቹም እውነት አልመሰሉኝም። ምናልባትም ሰዎች የሐሰት ወሬ ወይም ነገሮችን በማጋነን የበለጠ ሊያጣሉን እየሞከሩ ይሆናል የሚል ግምት ነበረኝ።

በዚህ ሁኔታ ሳለሁ ጥቅምት 9 ቀን 2012 ዓ.ም በአሰላ ከተማ የተከበረውን የኢሬቻ በዓል እንድንታደም ተጋብዘን ከቄስ በላይ መኮንን፣ አቶ ገላሳ ዲልቦ እና አቶ ጇኔይዲ ሳዶ ጋር ሄድን። በቀደምት የኦሮሞ ትግል ጀግኖች እና በእኔ ስም የተሰየሙ መንግዶችን መርቀን ከፈትን።

በዕለቱ ባረፍንበት ሆቴል የአስተናጋጅ ልብስ ለብሰው ወደ ክፍሌ ሲያቀኑ የነበሩ ሰዎች ከጦር መሣሪያ ጋር መያዛቸውን፣ ነገር ግን "ከላይ" ተደውሎ የኔን ደህንነት በምሥጢር እንዲጠብቁ ከፊንፊኔ የተላኩ ሰዎች መሆናቸውን ተናግረው እንዳስለቀቋቸው ከዞኑ የጸጥታ አመራሮች ሰማሁ። አመራሮቹ ተይዘው የነበሩት ሰዎች እንዲገድሉኝ የተላኩ መሆናቸውን ከባድ ጥርጣሬ ስላደረባቸው፣ በማግስቱ የታቀደው የኢሬቻ በዓል ላይ መሳተፍ እንዲቀርብኝና ወደ ፊንፊኔ እንድመለስ መከሩኝ። በበኩሌ ግን «በእርግጥም እኔን ለመጠበቅ የተመደቡ ሊሆኑ ይችላሉ® በማለት አረጋጋኋቸው። በእውነትም እንደዛው ነበር ያሰብኩት።

## 9.2. **ጥቃት**

ጠቅላይ ሚኒስትሩ በፓርላማ የተቆጣበት ቀን አመሻሽ ላይ ሰዎች እየነገሩኝ የነበረው ማስጠንቀቂያ የበለጠ እውን ሆነ። ጠ/ሚኒስትር ዐቢይ ከፓርላማው ንግግር በኋላ ለስብሰባ ወደ ሩሲያ ሄደ። እኔም ቤቴ እራት አብረን የበላን ሰዎች እንደወጡ እኩለ ሌሊት ገደማ ወደ መኝታ ክፍሌ ገባሁ። ትንሽ ሸለብ ከማለቴ የጥበቃዬ ኃላፊ ጌቱ ተረፈ መጥቶ ቀሰቀሰኝ። ጌቱን ጨምሮ አራቱ ጠባቂዎቼ በመንግሥት የተመደቡልኝ የፌደራል ፖሊስ አባላት ነበሩ። ጌቱም የፌደራል ፖሊስ አዛዦች መጥተው ጠባቂዎቹን በሙሉ «መሣሪያቻችሁን ይዛችሁ ውጡ» እንዳሏቸው ነገረኝ። “በዚህ ውድቅት የተሰጠንን ኃላፊነት ትተን አንሄድም፤ ጠዋት እንወጣለን” ብንላቸውም አሁኑኑ ካልወጣችሁ እያሉን ነው» ብሎ ነገረኝ። ይልቁንስ «“ጀዋር እንዳያውቅ ተደብቃችሁ ውጡ” ብለውናል» አለኝ። ትዕዛዙን ከቤቴ ትንሽ ራቅ ወዳለ ሥፍራ ወስደው የነገሯቸው ሲሆን፣ ጠባቂዎቼ እምቢ ቢሉ እዚያው ሊያስቀሯቸው እንደሆነ በመጠርጠር፣ ትዕዛዙን እንደተቀበሉ ነግረዋቸው፣ መሣሪያቸውን ይዘው ለመመለስ ተስማምተው ወደ ግቢ ገብተው ቀሰቀሱኝ። ጠባቂዎቼ በሌሊት እንዲወጡ መታዘዛቸው እና መሄዳቸውን እኔ እንዳላውቅ መፈለጉ አጠራጠረኝ።

መንግሥት የመደበልኝን ጥበቃ መለወጥ ወይም ሙሉ በሙሉ ማንሳት ይችላል። ከዚያ በፊትም ቀይረው ያውቃሉ። በምሽት ጥበቃ ትታችሁ ሂዱ የሚሉበት ምክንያት ግን ሊገባኝ ስላልቻለ ልጆቹ የሚነግሩኝን ማመን ከበደኝ። ምናልባትም በአዛዦቹ እና በጠባቂዎቹ መካከል አለመግባባት ተፈጥሮ ይሆን ብዬ ጠረጠርኩ። እናም ለአዛዡ በድጋሜ እንዲደውሉለት በማድረግ እኔ እየሰማሁ ቀደም ሲል ለልጆቹ የሰጠውን ትዕዛዝ ደገመው።

የአዛዡን ትዕዛዝ በጆሮዬ ከሰማሁ በኋላ ሤራ እንዳለ ጠረጠርኩ። ትዕዛዙ ከየት እንደመጣ ለማወቅ ስለፈለኩኝ ለአዛዡ በቀጥታ ደወልኩለት። ኮማንደር እንዳለ እንደሚባል ነገረኝ። ጠባቂዎቼን እንዲያነሳ በአለቆቹ ትዕዛዝ እንደተሰጠው ነግሮኝ ያዘዘውን ባለሥልጣን ስም አሳወቀኝ። ጠባቂዎቹን ማንሳት ሥልጣኑ እንደሆነ አረጋግጬለት፤ ግን ደግሞ በዚህ ጨለማ ሳይሆን ጠዋት ውሰዳቸው አልኩት። እሱም የተሰጠው ትዕዛዝ ጠባቂዎቹን አሁኑኑ ማንሳት እንደሆነ፤ ይህ የእሱ ፍላጎት ሳይሆን የእንጀራ ጉዳይ መሆኑን ገልጾ እንዳልቀየመው ተማጸነኝ።

ከእሱ ጋር ስልኩን ከዘጋን በኋላ ጠባቂዎቼ ቤቴ በሁሉም አቅጣጫ በታጠቁ ወታደሮች እንደተከበበ ደረሱበት። በወቅቱ ወደ ነበርኩበት ቤት የሚወስድ አንድ መንገድ (dead- end road) ብቻ ነበር። የፌደራል ፖሊሶች ወደ ቤቴ በሚወስደው ብቸኛ መንገድ ሲመጡ፤ የታጠቁ ሲቪሎች ደግሞ በሰው ግቢ ውስጥ በጓሮ በኩል ለመግባት ሞከሩ። ጠባቂዎቹ አሞቺ ቦታ ይዘው ሲጠብቁ ስለነበረ የፌደራል ፖሊሶቹን ሲያስጠነቅቋቸው ቆሙ። ሲቪሎቹ ግን አቅጣጫ ቀይረው ወደ ቤቱ ለመጠጋት መሞከራቸውን ቀጠሉ።

ጉዳዩን ለማጣራት እና ለማስቆም የደኅንነት ቢሮ፣ የፌደራል ፖሊስ እና የሀገር መከላከያ ሠራዊት ኃላፊዎች ጋር ስደውል አብዛኞቹ አያነሱም፤ የተቀሩት ደግሞ የተላለፈውን ትዕዛዝ

እንደማያውቁና ምንም ማድረግ እንደማይችሉ ነገሩኝ። ይህም የቀደመ ጥርጣሬዬን አባባሰው።

ቤቱን የከበቡት ኃይሎች ከተለያየ አቅጣጫ ሰብረው ለመግባት እየሞከሩ ሳለ፤ በሌ ሚካኤል አካባቢ የሚኖሩ ቄሮዎች እየሆነ ያለውን ሰምተው ወደ ሰፈሬ መምጣት ጀመሩ። ራቅ ያለ ቦታ ያሉትም ተነጋግረው እየመጡ እንደሆነ ሰማን። በጠባቂዎቼ እና ቤቴን በከበቡ ሰዎች መካከል ያለው ፍጥጫ ወደ ተኩስ ካመራ ቤተሰቤን ብቻ ሳይሆን ጎረቤትም ለአደጋ እንደሚያጋለጥ ገባኝ። ምን እየተካሄደ እንዳለ ለሕዝብ ለማሳወቅና ወታደሮቹን የላኩትን ለማስጠንቀቅ ስለፈለኩ የፖሊስ አዛዡን ድምፅ ከነማብራሪያው ፌስቡክ ላይ ለጠፍኩ። ብዙ ሕዝብ በቤቲ አካባቢ በመሰብሰብ የተቃውሞ ድምፅ ማሰማት በመጀመሩ፣ ፖሊሶቹ እና የታጠቁት ሲቪሎች ወደኋላ አፈገፈጉ።

በእኔ ላይ የተደረገው ሙከራ በመገናኛ ብዙኃን እንደተሰራጨ በመላው ኦሮሚያ ተቃውሞ ተቀሰቀሰ። ሲነጋ ወደ ሚዲያ ወጥቼ ደህና እንደሆንኩ እና ሕዝቡም በሰላም ወደ ቤቱ እንዲገባ አሳሰብኩ። ነገር ግን በተለያዩ ቦታዎች ተቃውሟቸውን ጨርሰው ወደ ቤታቸው በሚመለሱ ሰዎች ላይ ጥቃት ደረሰ። ጥቃቱ የደረሰው በአንዳንድ ቦታዎች በመንግሥት የጸጥታ ኃይሎች ሲሆን፣ በሌሎች ቦታዎች ደግሞ በተደራጁ ዱርዬዎች ነበር። እንደ አምቦ ባሉ ከተሞች የመንግሥት ታጣቂዎች የተኩስ እሩምታ በመክፈት ሰላማዊ ሰዎችን ሲገድሉ፣ አዳማ እና ባሌ ሮቤ የተደራጁ ዱርዬዎች ድንጋይ፣ ቢላ እና ጠብመንጃ በመጠቀም በሰላማዊ ሰልፈኞች ላይ ጥቃት ፈጸሙ። የደረሰው ጉዳት በፊት ቀዝቀዝ ብሎ የነበረውን ሕዝብ እንደ አዲስ አስቆጥቶ ተቃውሞው እንዲስፋፋ አደረገ።

ከተፈጠረው ጥቃት በስተጀርባ ሤራ እንደነበረ ብዙ ማሳያዎች አሉ። ለምሳሌ፣ በአዳማ ከተማ ሕዝቡ ከተቃውሞ በኋላ ወደ ቤቱ እየሄደ እያለ፣ ቀደም ብሎ በሰላማዊ ሰልፉ ላይ ያልተገኙ ሰዎች በሁለት ቡድን ተደራጅተው አንዱ የድሮውን የኢትዮጵያ ባንዲራ (ልሙጡን) ፣ ሌላኛው ደግሞ የኦነግን ይዘው በመምጣት ሕዝቡ መሀል ሲደርሱ ብጥብጥ እሥነሱ። በቢላ፣ በጦር መሣሪያ እና በድንጋይ በሰነዘሩት ጥቃት ቀላል የማይባል ጉዳት አደረሱ። ሰልፈኛውን በዚህ መልኩ ካጋጩ በኋላ በየመንደሩ በመሄድ በሰው ሕይወት እና በንብረት ላይ ከፍተኛ ጉዳት አስከተሉ። ሤራ መኖሩን የሚያመለክተው ሌላ ክስተት ደግሞ በብዙ ከተሞች ሕዝቡ እርስ በእርስ ሲገዳደል የጸጥታ ኃይሎች ጣልቃ ገብተው ከማስቆም ይልቅ በዝምታ መመልከትን መርጠዋል። ይህንን ሰምተን በተለያዩ ከተሞች የሚገኙ የፖሊስ እና የመከላከያ ሠራዊት አዛዦችን ደውለን ጣልቃ እንዲገቡ ስንማጸን፣ «እርምጃ እንድንወስድ አልታዘዝንም» ይሉ ነበር። አንዳንድ ቦታ ወታደሮች በራሳቸው ተነሳሽነት ግጭቱን ለማስቆም ሲንቀሳቀሱ ወደ ካምፕ እንዲመለሱ መታዘዛቸውን ሰማን።

የዚያን ቀን ከሰዓት በኋላ ብዙ የሀገር ሽማግሌዎች ወደ ቤቴ መጥተው፣ በወቅቱ የኦሮሚያ ክልል ፕሬዝዳንት ከነበሩት አቶ ሽመልስ አብዲሳ ጋር የጋራ መግለጫ በመስጠት ግጭቱን እንድናስቆም ጠይቀውኝ ተሰማማሁ። ለመሄድ ስሰናዳ፣ ከመንግሥት ባለሥልጣናት መካከል አንዱ ጠባቂዎቼን አግኝቶ ከቤት መውጣት አደጋውን ሊያባብሰው እንደሚችል ነገራቸው። ስለዚህ እኔ እና ሽመልስ ለየብቻ መግለጫ ሰጠን። እኛ ሕዝቡን ለማረጋጋት እየሞከርን ባለንበት ወቅት በአማርኛ ቋንቋ የሚሰራጩ የመንግሥት እና የግል ሚዲያዎች መጠነ ሰፊ ዘመቻ ከፈቱብኝ። ለዘመቻው ምላሽ መስጠት ጉዳዩን ማባባስ ስለሚሆን በትዕግሥት ለማለፍ ወሰንኩ። ሕዝቡም ጥሪዬን ሰምቶ ከሁለት ቀናት በኋላ ሰልፉን አቆመ።

ጠ/ሚኒስትር ዐቢይ አሕመድ ከሩሲያ እንደተመለሰ ሕዝቡን ለማረጋጋት ለማ መገርሳን ይዞ ወደ ሐረር አመራ። የሐረርጌ ሕዝብ በቁጣ ተቀበላቸው። ጠ/ሚኒስትር ዐቢይም በፓርላማ ያደረገውን ዛቻ ለእኔ እንዳልነበረ ተናግሮ፣ ምሎ ተገዝቶ ለማሳመን ሞከረ። በዚያ ቀን ምሽት ሽመልስ አብዲሳ ወደ ቢሮው እንድመጣ ጠይቆኝ እሺ ብዬ ሄድኩ። ከሽመልስ ጋር እያወራን እያለ ጠ/ሚኒስትር ዐቢይ ሳላስበው በሩን ከፍቶ ገባ። ከለማ መገርሳ ጋር ሐረርጌ ቢውልም የመጣው ግን ብቻውን ነበር። ልክ እንደገባ እጄን ይዞ፣ «እውነት ልገድልህ የሞከርኩ ይመስልኻል? እውነት እኔ ነኝ የምገድልህ?» ሲለኝ ባላሰብኩበት ጊዜ የመጣ ያልጠበኩት ጥያቄ ስለሆነብኝ መልስ ሳልሰጠው ዓይን ዓይኑን ተመለከትኩ። መልስ ሲያጣ፣ «በእናቴ እምላለሁ፤ በተፈጠረው ነገር ውስጥ እጄ የለበትም!» አለኝ፤ መዳፌን በመሐላ መልክ እየመታ።

ለመሐላው እንድመልስለት እየጠበቀኝ መሆኑን ስረዳ፣ «ጠ/ሚኒስትር ዐቢይ፣ ስለተፈጠረው ነገር የራሴ ጥርጣሬ እና የደረስኩበት ድምዳሜ አለኝ። በእናትህ መማል የለብህም። በእኔ ላይ የተሞከረውን እርምጃ አዘህ ከሆነ ከባድ ስሕተት ነው። የመገዳደል ፖለቲካ ለሀገር እና ለኅብረተሰብ ከፍተኛ አደጋ ያመጣል። በተለይ የኦሮሞ ሕዝብ በመሪዎቹ ግድያ የከፋ ጠባሳ አለው። በዚህ ጥቃት ሞቼ ቢሆን ኖሮ ኦሮሞ እኔንም አንተንም ያጣ ስለነበር ፈጣሪ እኛንም ሆነ ሕዝባችንን እንኳን አተረፈ። ሁለተኛ እንዳይደገም ልንማርበት ይገባል» አልኩት። ቀጥዬም «ጉዳዩ የባሰ አደገኛ የሚሆነው አሁን እንዳልከው የሆነውን የማታውቀው ከሆነ ነው። በመንግሥትህ ውስጥ ያለአንተ ትዕዛዝ እና እውቅና እንደኔ ያለን ሰው ሊገድል የሚሞክር አካል ካለ እገዛዙ ብቻ ሳይሆን ሕይወትህ አራሱ አደጋ ላይ ነው» ብዬ ሥጋቴን ገለጽኩ። «ስለዚህ አንተ አድርገህም ከሆነ ይቅር ብዬሀለሁ። አንተ ካላደረክ ግን ሁላችንም ለከባድ አደጋ ሰለተጋለጥን ከዚህ የባሰ ነገር እንዳይመጣ ተባብረን መመከት አለብን» አልኩኝ።

ከሐሳብ ልውውጡ በኋላ ተቀምጠን በእርጋታ ማውራት ጀመርን። ሕዝቡ የበለጠ መረጋጋት በሚችልበት ሁኔታ ላይ ሐሳብ ተለዋወጥን። በማግስቱ ወደ አምቦ እንደሚሄድ ነገረኝ ፤ እኔ ግን መሄዱ ጥሩ እንዳልሆነ ነገርኩት። አምቦ ብዙ ሰዎች የተገደሉበት ቦታ ስለነበር እና ኃይለኛ ንዴት ውስጥ እንዳሉ ስለማውቅ የእሱ መሄድ ጉዳዩን ያባብሰዋል ብዬ ሠጋሁ። ፕሮፌሰር መረራ እና ሽመልስ ወይም ታከለ ኡማ እንዲሄዱ ሐሳብ አቀረብኩ። እሱ ግን ምክሬን አልተቀበለውም፣ «አምቦዎች እንደ ሐረርጌ አይደሉም" ብሎ ንግግሩን ዘጋ።

በማግስቱ ዐቢይ፣ ለማ እና ሽመልስ ወደ አምቦ ሄዱ። እዚያም ሕዝቡ በታላቅ ቁጣ አስተናገዳቸው። በአዳራሹ ውስጥ የነበረው ሕዝብ ጥያቄ እና ቁጣ ሲያዘንብባቸው፤ ውጪ ያለው በተቃውሞ መንገዱን አጥለቀለቀው። የOMN ጋዜጠኞች ወደ አዳራሹ እንዳይገቡ መከልከላቸው ውጪ ላይ ሰላማዊ ሰልፍ የሚያደርገውን ሕዝብ የበለጠ አስቆጥቶ ወደ አዳራሹ በጉልበት ሰብሮ ለመግባት ሙከራ ተጀመረ። ወሬውን የሰሙ ገበሬዎች ከገጠር መንደሮች ወደ አምቦ እየጎረፉ መሆኑ ተሰማ። ነገሩ እየተባባሰ ሄዶ እነዐቢይ ይዟቸው የመጣ መኪና ጋር መድረስ አቅቷቸው፤ በአዳራሹ ጀርባ በኩል በጭነት መኪና ማምለጥ እንደቻሉ ማታ ከመካከላቸው አንዱ ነገረኝ።

ከአምቦ እንደተመለሱ ከጥቂት ቀናት በኋላ የኦሮሞ አመራር መማክርት ሰብሰባ በቤተ- መንግሥት ተካሄደ። ስለ ተፈጠረው ሁከት ከተነጋገርን በኋላ በእኔ እና በጠ/ሚኒስትር ዐቢይ ጉዳይ ለመምከር ሐሳብ ቀረበ። ጠ/ሚኒስትር ዐቢይ ጣልቃ ገብቶ ሁለታችን ተነጋግረን እንደጨረስን በመንገር አጀንዳ መሆን እንደማይገባው ገለጸ። «ጨርሰናል አይደል?» ሲለኝ

"አዎ፣ ቀድሞም የግል ችግር የለብኝም፤ አሁንም በግል ጉዳዮች ተግባብተናል። ነገር ግን ለዚህ ችግር ያጋለጠን የሕዝብ እና የሀገር ጉዳይ በዚህ መድረክ ሊታይ ይገባል» አልኩት። ዐቢይ «የቀረን ነገር ካለ ለብቻችን አውርተን እንጨርሳለን፤ ይህ መድረክ በቀሪዎቹ አጀንዳዎች ላይ ያተኩር» ሰላለ ሌሎች አጀንዳዎችን ወደ መወያየት ተሸጋገርን።

ስብሰባው ሲጠናቀቅ ጠ/ሚኒስትር ዐቢይ አንድቆይ ጠይቆኝ ወደ ቢሮው ሄድን። እዚያም የእኔ ነገር ከውስጥም ከውጭም ችግር እየፈጠረበት እንደሆነ ነገረኝ። የአዴፓ (የአማራ ዴሞክራሲያዊ ፓርቲ) ሰዎች እንድታሰር ከፍተኛ ጫና እያሳደሩ መሆኑንና ከራሱ ከኦዴፓም «ሲያገኙህ በምላሳቸው ወዳጆችህ እንደሆኑ የሚያስመስሉ ሰዎች አዴፓን እየደገፉ ነው»አለኝ። በተጨማሪም አሜሪካኖች በICC (International Criminal Court) እንድከሰስ ጫና እያደረጉ እንደሆነም ገለጸልኝ። በበኩሌ «የሠራሁት ጥፋት ካለ ማንኛውም ሕጋዊ እርምጃ ይወሰድብኝ። እኔን ለመከላከል አትቸገር። ገለልተኛ ኮሚቴ ተቋቁሞ ምርመራ ያድርግ። የምርመራ ውጤቱ ላይ ተመርኩዤ ካስፈለገ በዚህ ሀገር ፍርድ ቤት ወይም በICC በሕግ ለመዳኘት ዝግጁ ነኝ» አልኩት። ዐቢይ ግን «እኔ እያለሁ ማንም አይነካህም» በማለት ንግግራችንን ቋጨው። የዚያን ዕለት አመሻሹ ላይ ለመጀመሪያ ጊዜ በሚዲያ ቀርቦ በጉዳዩ ላይ መግለጫ ሰጠ።

በእኔ ላይ ከተቀነባበረው ሙከራ ጋር ተያይዞ የነበረውን ጉዳይ እኔ እና ጠ/ሚኒስትር ዐቢይ በዚሁ አለፍነው። ለመንግሥት ቅርበት ያላቸው ሚዲያዎች እና ሰዎች ግን «ጀዋር ሰማንያ ስድስት ሰዎችን አስገደለ» የሚለውን ፕሮፓጋንዳ በየቀኑ ማሰራጨታቸውን ቀጠሉበት።

## 9.3. ይፋዊ ልዩነት

ከጥቂት ሳምንታት በኋላ ሌላ የመማክርት ስብሰባ እንደጨረስን ጠ/ሚኒስትር ዐቢይ በድጋሚ ወደኋላ እንድቀር ነገረኝ። ሁሉም መሪዎች ከሄዱ በኋላ ወደ ቢሮው አስጠርቶኝ የእኔ ጉዳይ አሁንም ችግር እየፈጠረበት እንደሆነ ገለጸልኝ። በአንድ በኩል የአማራ ኃይሎች ለምን አታስረውም በማለት ከውጪም ከውስጥም ጫና እያደረጉበት እንደሆነ፣ በሌላ በኩል ደግሞ እኔ እሱን ከመርዳት ይልቅ በመገናኛ ብዙኃን በኩል ትችቴን መቀጠሌ ከሁለት ያጣ እያደረገው እንደሆነ አስረዳኝ።

በዚህ ጊዜ አእምሮዬ ውስጥ ሲመላለስ የነበረውን ሐሳብ አውጥቼ ተናገርኩ። በሁለታችን መካከል ያለው ግንኙነት የኦሮሞን እና የኢትዮጵያ መፃዒ ፖለቲካ ላይ አሉታዊ ተጽዕኖ ሊኖረው ስለሚችል መፍትሔ መፈለግ አለብን» አልኩት። ምን ለማለት እንደፈለኩ ሲጠይቀኝ፣ «እንደ ዕድል ሆኖ ሁለታችንም በዘመኑ ፖለቲካ በግንባር ቀደምነት እየታየን ነው። የእኛ መስማማት ለኦሮሞም ሆነ ለኢትዮጵያ መረጋጋትን ያመጣል። የእኛ ውዝግብ ብጥብጥ ይፈጥራል። የሁለታችንን ግንኙነት ፈር ማስያዝ አለብን። ይህንን ለማድረግ እኔ እና አንተ አቋማችንን እና አመለካከታችንን ወደ መሀል ማምጣት አስፈላጊ ይመስለኛል» በማለት ሐሳቤን አቀረብኩ። አሁንም «ምን ለማለት እንደፈለክ ግልጽ አድርገው» ሲለኝ፣ «እኔ እና አንተ አጋሮች ወይስ ባላንጣዎች የሚለው ጉዳይ ሕዝቡ ውስጥ ብዥታ ፈጥሯል። ስለዚህ ከሁለቱ አንዱን መርጠን ሕዝቡ እንዲያውቀው ማድረግ አለብን» አልኩት። እሱም «በፈለከው በኩል ና። ከፈለክ ከእኔ ጋር ሥራ፤ ካልሆነም ተቃዋሚ ሁን» በማለት በአጭሩ መለሰልኝ። የዚያን ቀን በዚሁ ተለያየን።

በሌላ ቀንም ከመማክርቱ ስብሰባ በኋላ ጠራኝ። ባለፈው ያደረግነውን ውይይት አስታውሼ ወደ ተቃዋሚ ፓርቲ ተቀላቅዬ ምርጫ ለመወዳደር እንዳሰብኩ ነገርኩት። ፊቱ በድንገት ተለዋወጠ። «ወደ ምርጫ ከመግባት መነገድ ይሻልሃል። አስፈላጊውን ነገር እናመቻችልሃለን» አለኝ። እኔ ግን «አይ፣ የኦሮሞ ትግል በምትከተለው አመለካከት እና ስልት አደጋ ውስጥ እየገባ ያለ ይመስለኛል። ወደ አንተ ቀርቤም ሆነ ከዳር ሆኜ ነቅፌ ማስተካከል እንደማይቻል አይቻለሁ። ስለዚህ ለዚህ ሕዝብ አማራጭ ራእይ እና አመራር (alternative vision and leadership) በማቅረብ እየሄድክበት ያለው መንገድ ካልተሳካ መጠባበቂያ (backup) መፍጠር ያስፈልጋል አልኩት።

ጠ/ሚኒስትር ዐቢይ በውሳኔዬ መናደዱን ለመደበቅ እየሞከረ፤ «ለማንኛውም ከመወሰንህ በፊት ለእናትህ ንገራትና ኣሳምናት፣ ልታጣህ አትችልም» አለኝ። እኔም «መጀመሪያም እናቴን አማክሬ ወደ ትግል አልገባሁም። አሁንም ከእሷ ጋር መማከር አያሻኝም። ትግል ውስጥ ያለውን መሥዋዕትነት እና ዋጋ ዕድሜዋን ሙሉ ስታይ ስለነበረ ውሳኔዬን ለመረዳት አይቸግራትም» ብዬ የመጨረሻ ውሳኔዬ እንደሆነ አረጋገጥኩለት።

በዚህ ጊዜ ድንገት እጄን ይዞ ዓይን ዓይኔን እያየ፣ «የምትፈልገውን ነገር አውቃለሁ። አንድ ነገር በትክክል እወቅ። እዚህ ሀገር ውስጥ የምታስቸግሩኝ እንደ ድርጅት ሕወሓት፤ እንደ ግለሰብ ደግሞ አንተ ነህ። አታሸንፉኝም! አጠፋችኋለው! ካልቻልኩም ይህቺን ሀገር አበትናታለሁ

እንጂ ሥልጣን አሳልፌ አልሰጣችሁም!» ብሎ ቁጣ በተቀላቀለበት ድምፅ እየዛተ መዳፌን መትቶ ማለልኝ። ይህን ሲናገር ፊቱ ጠቁሮ እጁ እየተንቀጠቀጠ ነበር። ንዴቱን በቀልድ ለማብረድ በማሰብ፣ «ጠ/ሚኒስትር ዐቢይ እኔን ማጥፋት አትችልም። እናቴ ጊዮርጊስ፣ ሼኽ ሁሴን እና ሃደ አበዪ ጋር በየዓመቱ ሰለት ታስገባልኛለች። ሕይወቴ ለዛሬ የደረሰችውም በዚህ ስለት ነው። አሁንም በግራ በቀኝ ይጠብቁኛል» አልኩት፤ ፈገግ እያልኩ። እሱ ግን ንዴቱ አልለቀቀውም ነበር። «ይህ ቀልድ አይደለም! አስብበት!» ብሎ ተነስቶ አንድወጣ ወደ በሩ መራኝ።

ወጥቼ የግቢው በር ጋር ስደርስ አቶ ገላሳ ዲልቦን አገኘሁት። «መጣህ?» አለኝ መጨነቁን በሚያሳብቅ ሁኔታ። ከፊቱ ላይ ሥጋት ይነበባል። «ምነው መኪና አጣህ እንዴ?» ስለው፤ «አይ፣ ይኸው አለ። ጠ/ሚኒስትር ዐቢይ አንተን የጠሩበት መንገድ ስሜቴን ስለረበሸው ሆዴ አላስችል ብሎኝ ልጠብቅህ ወሰንኩ» አለኝ። የሆነውን ነገር እንድነግረው ሲጠይቀኝ ከዚህ በላይ እንዳላስጨንቀው ብዬ በሰላም ተነጋግረን መለያየታችንን ነገርኩት።

ወደ ፖለቲካ ፓርቲ ተቀላቅዬ በምርጫ ለመሳተፍ እንደወሰንኩ፤ ውሳኔዬን ለረጅም ዘመናት ደግፎ ለውጤት ላበቃኝ የዲያስፖራው ማኅበረሰብ ለመንገር እና ለማወያየት ወደ አሜሪካ አቀናሁ። ከOromo First ጀምሮ አዲስ የትግል ስልት ስቀይስ በተለያዩ ከተሞች ከሚኖረው የኦሮሞ ማኅበረሰብ ጋር በግልጽ ስብሰባ መወያየት ልማዴ ነው። ያሰብኩትን ስልት እና እቅድ በማቅረብ በስብሰባዎቹ በሚነሱ ጥያቄዎች እና ትችቶች ማዳበር እጅግ ጠቅሞኛል። ወደ ፓርቲ ለመቀላቀል ሰወሰንም ወደ ተግባር ከመግባቴ በፊት ተመሳሳይ ውይይት ማድረግ ፈለኩ።

ወደ አሜሪካ ለመብረር ያሰብኩ ዕለት ከሰዓት በኋላ ከሽመልስ አብዲሳ ጋር በመሆን ጠ/ ሚኒስትር ዐቢይ አሕመድ ዘንድ ሄድን። ምሽት ላይ ወደ አሜሪካ እንደምሄድ እና በጉዞዬም ስለወደፊቱ የፖለቲካ ተሳትፎዬ እንዲሁም በሀገራዊ ጉዳዮች ላይ ከውጭ ማኅበረሰብ ጋር ለመወያየት እንዳቀድኩ ነግሬው ተለያየን። እኔ በረራ ላይ እያለሁ አንድ ለመንግሥት ቅርብ የሆነ ሰው በየትኛው አየር ማረፊያ እና በምን ሰዓት እንደምደርስ በፌስቡክ ላይ ለጠፈ። እንደ አጋጣሚ የተሳፈርኩበት አውሮፕላን ኢንተርኔት ስለነበረው እየተካሄደ ያለውን ነገር እየተከታተልኩ ነበር። ያቀናሁበት የፊላዴልፊያ አውሮፕላን ማረፊያ ብዙ ሰዎች እኔን ለመቃወም እየጠበቁ እንደሆነ ሰማሁ። ኤርፖርት ውስጥ የሚሰሩ ኦሮሞዎች ይህንን ስላወቁ አውሮፕላኑ በር ድረስ በመምጣት ከፖሊስ ጋር ከበው አስወጡኝ።

OMN ላይ ራባዶሪ የተሰኘው ዝግጅት ተሳታፊ የሆነው ጓደኛዬ ዶ/ር ደረጀ ሀዋዝ ቤት አረፍኩ። የዚያን ዕለት ማታ በአሜሪካ ካሉ የድጋፍ መዋቅራችን ጋር ባደረግነው የስልክ ውይይት (conference call) ሕዝባዊ ስብሰባ ለማድረግ

በአቀድንባቸው ከተሞች ሁሉ ተቃውሞ ለማካሄድ እና ፕሮግራሜን አውኮ ለማስቀረት ዘመቻ እየተደረገ እንዳለ ተረዳሁ። መከናወን ስላለባቸው ቅድመ ዝግጅቶች እና ጥንቃቄዎች ተወያይተን የሥራ ክፍፍል አድርገን ወደ ተግባር ገባን።

ድሮ አሜሪካ ሆኜ ትግል ሳደርግ የኢሕአዴግ ባለሥልጣናት ሲመጡ ስብሰባቸውን ለማወክ ተቃውሞ እናስተባብር ስለነበር፤ ልምዱ አሁን ጠቃሚ ሆኖ ተገኘ። በእኔ ላይ ተቃውሞ ለማሰማት ሲዘጋጁ የነበሩ ሰዎች ምን ዓይነት ዘዴዎችን እንደሚጠቀሙ በመገመት የምናከሽፍበትን እቅድ ለማሰናዳት ጠቅሞናል።

በእኔ ላይ ሲደረግ የነበረው ዘመቻ በጣም ከባድ ነበር። ተቃውሞው የሚካሄደው በአብዛኛው በአማራ ተወላጆች ቢሆንም፤ በመገናኛ ብዙኃን፣ በአድሮች እና በሀይማኖት ተቋማት ሰፊ ቅስቀሳ ተደርጓል። ሆኖም በጥላቻ ቃላቶች የተሞላው ዘመቻ የኦሮሞን ማኅበረሰብ አስቆጥቶ በስብሰባዎቻችን ላይ ብዙ ሕዝብ እንዲገኝ አነሳሳ። የመጀመሪያ ስብሰባችንን በሚኒሶታ ስናደርግ ወደ ፖለቲካ ፓርቲ በመቀላቀል በመጪው ምርጫ ለመሳተፍ መወሰኔን አሳወቅኩ። ሕዝቡ ሐሳቤን በደስታ ተቀብሎ ረጅም ውይይት አደረግን።

በምርጫ ለመሳተፍ መወሰኔን ይፋ ካደረኩ በኋላ የሚካሄደው የተቃውሞ ዘመቻ እየተባባሰ መጣ። በአንዳንድ ከተሞች ሰዎች ወደ አዳራሽ እንዳይገቡ መንገዶችን ለመዝጋት ተሞከረ። ፖሊስ መጥቶ መንገዱን ሲከፍት ወደ አዳራሹ የሚሄዱትን ሰዎች አስነዋሪ የስድብ ናዳ ያወርዱባቸዋል። በብዙ ቦታዎች ለፖሊስ ደውለው የቦምብ ጥቃት (bomb threat) እንዳለ የውሸት ጥቆማ በመስጠት የተከራየነው አዳራሽ እንዲሠረዝ ያደርጋሉ። ይህንን ቀድመን ስለምንገምት ሦስት እና አራት አዳራሾችን በመከራየት አንዱን ሲያዘጉ ወደ ሌላኛው እየተዛወርን ውይይት እናደርጋለን። በዋሽንግተን ዲሲ ያቀድነውን ስብሰባ ለማክሸፍ ከሁሉም የሰሜን አሜሪካ ከተሞች ተቀናጅተው መጡ። በተለያዩ ጫናዎች ሦስት አዳራሾች እንዲሠረዝ አደረጉ። ስብሰባውን ከመሠረዝ ይልቅ በኦሮሞ ማኅበረሰብ ትንሽዬ አዳራሽ ውስጥ ለማድረግ ስንወስን ይህንንም ሰምተው አዳራሹን ከበቡት። ማኅበረሰቡ እልህ ውስጥ ገብቶ ስብሰባውን በቤተ-ክርስቲያን ውስጥ ለማድረግ ወሰነ።

በተለያዩ ከተሞች የተካሄደው ዘመቻ በእኔ ላይ ያነጣጠረ ቢመስልም የኦሮሞን ሕዝብ በሚነካ ማንቋሸሽ እና ዘለፋ የተሞላ ስለነበር፤ ማኅበረሰባችንን አስቆጣ፣ ሕዝባችን እንዲረጋጋ እና ሌሎች ብሔሮችን በቃልም ሆነ በተግባር እንዳይነካ በየመድረኩ አጥብቄ ስናገር ነበር። ሕዝቡም ትንኮሳዎችን በትዕግሥት በማለፍ አኮራኝ።

በዘመቻው ምንም እንኳን ውጪ ያሉ የአማራ ማኅበረሰብ አንቂዎች በግንባር ቀደምነት ቢታዩም፣ እቅዱ እና ፋይናንሱ ቤተ-መንግሥት ባሉ ሰዎች እንደሚቀርብ ማስረጃዎችን እናገኝ ነበር። የመንግሥት ሰዎች በኋላ በአካል መጥተው

ከባድ ረብሻ እና ዘለፋ ሲፈጽሙ ከነበሩ ሰዎች ጋር የተነሷቸው የፎቶግራፍ እና የቪድዮ ማስረጃዎችን ስንመለከት ቀደም ሲል ስንሰማ የነበረውን መረጃ አረጋገጡልን።

በሰሜን አሜሪካ እና በአውሮፓ ከሚገኙ ማኅበረሰቦቻችን ጋር ባደረግኩት ውይይት ሕዝቡ በምርጫው በመሳተፍ ትግሉን ለማስቀጠል መፈለጌን ቢደግፍም ወደ ሀገር ቤት መመለሴ ለአደጋ እንዳያጋልጠኝ በመሥጋት እንዳልመለስ ሲማጸኑኝ ነበር። አደጋ ሊደርስብኝ እንደሚችል ባውቅም ሕዝባችን ለሃምሳ ዓመታት መሥዋዕትነት የከፈለበት ትግል ሲከስር ዝም ማለት እንደማልችል እና አስፈላጊውን መሥዋዕትነት ለመክፈል መወሰኔን ነግሬያቸው ወደ ሀገር ቤት ተመልሼ ገባሁ።

## 9.4. ወደ ፖለቲካ ፓርቲ መቀላቀል

ያመንኩበትን ያለገደብ መናገር እና ያቀድኩትን በፍጥነት መሥራት ስለምወድ የፓርቲ ፖለቲካ አይመቸኝም። በፖለቲካ ድርጅት ማዕቀፍ የመንቀሳቀስ አቅድም ኖሮኝ አያውቅም። በሁኔታዎች አስገዳጅነት ወደ ፓርቲ ፖለቲካ ለመግባት ስወሰን ከሚቀናኝ እና ከለመድኩት አሠራር ለመውጣት ተገደድኩ።

ወደ ሀገር ቤት ከመሄዴ በፊት ወደ ፓርቲ ፖለቲካ በመግባት ምርጫው ላይ ለመሳተፍ ባስብም ምን ዓይነት ፓርቲ የሚለውን አልወሰንኩም ነበር። የነበረኝ አማራጭ አዲስ ፓርቲ ማቋቋም አለበለዚያ ካሉት አንዱን መቀላቀል ነው። አዲስ ፓርቲ መመስረት የራሴን ራእይ፣ ፖሊሲ እና ስትራቴጂ በነጻነት ለመቅረጽ ቢያመቸኝም ሌላ እንጃ በመፍጠር ሕዝቡን የበለጠ መከፋፈል ስለሚሆን አልሳበኝም። ምኞቴ ያሉት ሦስቱ ድርጅቶች ተጣምረው ከሌሎች ቄሮዎች ጋር መቀላቀል ነበር። በወቅቱ ከነበሩት የተቃዋሚ ድርጅት አመራሮች፣ ማለትም ፕ/ር መረራ ጉዲና (ኦፌኮ)፣ አቶ ዳዉድ ኢብሳ (ኦነግ) እና ጄ/ል ከማል ገልቹ (ኦብፓ) አንድ ላይ ተገናኝተን የትኛውን ፓርቲ ብቀላቀል እንደሚሻል አማከርኳቸው።

ሦስቱም አመራሮች የተለያየ ሐሳብ ሰጡኝ። ጀ/ል ከማል አንዳቸውንም ፓርቲ ባልቀላቀል እንደሚሻል መከረኝ። ፕ/ር መረራ በበኩሉ የእኔ ወደ ፓርቲ መግባት ጠ/ሚኒስትር ዐቢይን ሊያስደነግጠው ስለሚችል አስቀድሞ ማወያየት አስፈላጊ እንደሆነ አበክሮ ነገረኝ። አቶ ዳውድ ደግሞ «የፈለከውን ፓርቲ መግባት ያንተ ውሳኔ ነው» አለኝ። ከውይይታችን እንደተረዳሁት ወደ ድርጅታቸው እንድቀላቀል ፍላጎት ያሳዩት ፕ/ር መረራ ብቻ ነበሩ። ከውይይቱ በኋላ ይህንኑ በስልክ ስላረጋገጡልኝ፣ ፕሮፌሰሩን እና ምክትላቸው በቀለ ገርባን በጋራ አግኝቼ አብሬያቸው መሥራት የምችልበት መንገድ ላይ ተወያይተን ተስማማን።

ወደ ሀገር ቤት ዳግም እንደተመለስኩ በሦስቱ የኦሮሞ ተቃዋሚ ፓርቲዎች መካከል ጥምረት ለመፍጠር መሥራት ጀመርኩ። የምርጫ ጥምረት (electoral alliance) አስፈላጊነትን የሦስቱ ፓርቲዎች ሊቀመንበሮች ተወያይተው ስለተግባቡ፣ ሦስት ተወካዮች የስምምነት ሰነድ እንዲያዘጋጁና እኔ ደግሞ ውይይቱን እንዳመቻች ተመደብን።

ከረጅም ጊዜ ውይይት በኋላ በመወዳደሪያ ፖሊሲ እና ስትራቴጂዎች ላይ ስምምነት ላይ ተደረሰ። አንድ መቶ ሰማንያ (180) የፌደራል ፓርላማ መቀመጫዎች እና አምስት መቶ ሠላሳ አራት (534) የክልል ምክር ቤት መቀመጫዎች የሚከፋፈልበት ቀመር ላይ ግን መግባባት አዳጋች ሆነ። በተለይም የኦነግ እና የኦብፓ ተወካዮች አቋም የተራራቀ ነበር። ኦብፓ "ፓርቲዎችን ማበላለጥ አያስፈልግም መቀመጫዎችን እኩል እንከፋፈል" አለ። ይህ ካልሆነ ደግሞ እያንዳንዱ ፓርቲ የተሻለ ድጋፍ እና ተሰሚነት ባለው ዞን ይወዳደር የሚል አማራጭ አቀረበ። በሌላ በኩል ኦነግ ሁሉም ፓርቲ

በመላው ኦሮሚያ በሁሉም መቀመጫዎች ተወዳድሮ በውጤቱ መሠረት ከምርጫ በኋላ አስፈላጊ ከሆነ የጥምር መንግሥት እናቋቁማለን

የሚል ሐሳብ አቀረበ። ሐሳቡ ሕዝቡ በእውነተኛ ውድድር አሸናፊን የመለየት መብቱን መነፈግ የለበትም የሚል መከራከሪያ ነበረው።

ከረጅም ክርክር በኋላ አንድ ፓርቲ ሁሉንም መቀመጫዎች ቢወዳደር የምርጫ ጥምረት መመስረት ስለማይቻል ኦነግ ይህንን አቋም እንዲቀይር ማሳመን ቻልን። በተመሳሳይ ሁኔታ አብፓ ዞኖችን ለመከፋፈል ያቀረበው ሐሳብ ለሕዝቡ አንድነት አደጋ ስለሆነ እንዲቀር ተደረገ።

ምን ያህል መቀመጫዎች እንደሚካፈሉ ግን አሁንም መስማማት አልተቻለም። በመጀመሪያ፣ ኦነግ እና ኦፌኮ እያንዳንዳቸው አርባ በመቶ (40%)፣ አብፓ ደግሞ ሀያ በመቶ (20%) እንዲካፈሉ ሐሳብ ቀረበ። ኦነግ እና ኦብፓ ይህን ሐሳብ አልተቀበሉም። ኦነግ "ከሁሉም የበለጠ ሰፊ ድጋፍ ስላለኝ የትኛውም ፓርቲ ከእኔ ጋር ሊስተካከል አይገባም" አለ። ኦብፓ ደግሞ "ከማንኛውም ፓርቲ ያነስ ድርሻ ሊኖረን የሚችልበት ምክንያት የለም" በማለት ተከራከረ። ጉዳዩ ሲካረር የኦፌኮ ተወካዮች ከራሳቸው አምስት በመቶ (5%) በመልቀቅ ለኦብፓ ለመስጠት አስታራቂ የመሰላቸውን ሐሳብ አቀረቡ። መጀመሪያ ላይ ኦነግ ከ50% በታች አንቀበልም ቢልም 40% እንዲቀበሉ ማሳመን ተቻለ፤ ኦብፓ ግን 25% ለመቀበል ፈቃደኛ አልሆነም። በኮሚቴ ደረጃ መስማማት ስላልተቻለ ጉዳዩ ወደ ሊቀመንበሮቹ ተወስዶ ውሳኔ እንዲሰጥበት ተስማማን።

በዚህም መሠረት ለሊቀመንበሮቹ ስንገልጽ እነሱም መስማማት አልቻሉም። ኦብፓ ድርሻዬ ከሁለቱ ፓርቲዎች በአንድ ወንበርም ማነስ የለበትም በማለት አቋሙን አስታወቀ። ይባስ ብለው በብስጭት ከድርድሩ ራሳቸውን አገለሉ። ስለዚህ ኦፌኮ እና ኦነግ በመካከላቸው ጥምረት ለመፍጠር ተሰማሙ። የሁለቱ ፓርቲዎች ኮሚቴዎች ባደረጉት ውይይት በፌደራል ፓርላማ 52% ለኦፌኮ፣ 48% ለኦነግ እንዲሆን ከክልል ምክር ቤት ደግሞ ኦነግ 52%፣ ኦፌኮ 48% እንዲደርሳቸው ተግባቡ።

የትብብር ስምምነቱ በሰነድ ተዘጋጅቶ ተፈርሞ ለምርጫ ቦርድ እንዲቀርብ ቢታቀድም ሂደቱ ተጓተተ። አንድ ቀን ከሁለቱም ድርጅቶች አምስት አመራሮች ተገናኝተው በፈጠሩት ጫና ስምምነቱ ተፈርሞ ለምርጫ ቦርድ ተላከ። ሆኖም ትብብሩ ለሕዝብ ይፋ ሊደረግ በታቀደበት ዕለት ሀጫሉ ሁንዴሳ ተገደለ። ይህን ተከትሎ የሁለቱ ፓርቲዎች አመራር ላይ በደረሰው ወከባ፣ እሥራት እና አፈና ትብብሩ ከዳር አልደረሰም። በኋላ ሁለቱም ፓርቲዎች ከምርጫው ተገፍተው ሳይሳተፉ ቀሩ።

በምርጫው እንደምወዳደር አሳውቄ ከውጪ ከተመለስኩ ከተወሰነ ጊዜ በኋላ ኦፌኮን በግልጽ ለመቀላቀል ወሰንኩ። ይህንንም በፓርቲው ጽ/ቤት በተደረገ ዝግጅት ላይ በይፋ አስታወቅን። ቀጥሎም ከአመራሩ ጋር በመሰብሰብ የምርጫ እቅድ አዘጋጀን። ከዚህ አቅድ አንዱ የምርጫ ቅስቀሳ ጊዜ ባይደርስም ወደ ዞኖች በመሄድ ሕዝቡን ማናገር ነበር። ይህ ዘመቻ ሁለት ዓላማዎች ነበሩት። የመጀመርያው ሕዝቡን በመቀስቀስ ለፓርቲው አባላት እና ደጋፊዎችን ማፍራት ሲሆን፣ ሁለተኛው የኦሮሞን ብሔርተኝነት የማጥላላት ዘመቻ በመንግሥት እና በአጋሮቹ እየተደረገ ስለነበረ ሕዝቡን በማንቃት ለማክሸፍ ነው።

ለወትሮው የምርጫ ቅስቀሳ ዘመቻ የሚካሄደው ለምራጫው ሦስት ወራት ሲቀረው ነው። እኛ ግን ምርጫው ሲቃረብ ገዢው ፓርቲ የተቃዋሚዎችን እንቅስቃሴ ሊያስተጓጉል ይችላል ብለን በመጠርጠር፣ አገዛዙ ለአፈና ከመዘጋጀቱ በፊት ቅስቀሳ ለማድረግ ወሰንን። በተጨባጭም

መንግሥት ለአፈና እየተዘጋጀ እንደሆነ ብዙ ማስረጃዎች ነበሩን። ከእነዚህም አንዱ ነባሩን የኦሮሚያ ልዩ ኃይል ፖሊስ በማፍረስ በሺዎች የሚቆጠሩ አዳዲስ ምልምሎችን በማሰልጠን ላይ ነበሩ። በሥልጠናው ላይ የሚሰጠው ፕሮፓጋንዳ ተቃዋሚ ፓርቲዎችን እና መሪዎቻቸውን እንደጠላት በመፈረጅ ማጥላላት መሆኑን ስለደረስንበት ሳንቀደም መቅደም ፈለግን።

ከምርጫው አስቀድመን የቅስቀሳ ዘመቻ ማድረግ ጉዳት ሊኖረው እንደሚችል ገምተናል። ድጋፋችንን አስቀድመን ማሳየታችን ጠ/ሚኒስትር ዐቢይ አሕመድን እና መንግሥትን አስደንግጦ ወደ ኃይል እርምጃ ሊያስገባ እንደሚችል እሙን ነበር። ባላፉት ምርጫዎች ኦፌኮ ካለው ልምድ በመነሳትና ጠ/ሚኒስትር ዐቢይ አዲስ አምባገነናዊ ሥርዓት ለመገንባት መወሰናቸውን በመረዳታችን ምርጫው ሲቃረብ እንቅስቃሴያችንን ብቻ ሳይሆን ከምርጫውም ሊያግዱን ይችላሉ የሚል ግምት ነበረን። አስቀድመን ዘመቻ ማድረጉ ከምርጫ ቢገፉን እንኳን ያለንን ድጋፍ ለማሳየት እና የኦሮሞን እምቢተኝነት ለማቀጣጠል ይጠቅማል የሚል እምነት እደረብን።

የቅስቀሳ ዘመቻውን የጀመርነው ከሐረርጌ ነበር። መጀመሪያ ላይ አራት ከተሞችን ለመጎብኘት ብናቅድም በሕዝቡ ጥያቄ ወደ ስምንት ከተሞች በመሄድ ትልልቅ ሰልፎች ተካሂደው ሰፊ ውይይት አደረግን። ሐረር ከተማ በተደረገው ዝግጅት ላይ ፕሮፌሰር መረራ ጉዲና በቀደሙት ዓመታት ለምርጫ ዘመቻ በሄዱበት ወቅት ብዙ ሰው ባለመውጣቱ እና በወቅቱ ሕዝቡ ግልብጥ ብሎ መውጣቱ በእጅጉ አስደሰታቸው። በውይይታችን ወቅት የሐረርጌ ማኅበረሰብ ካነሳቸው ቁልፍ ጉዳዮች መካከል የአካባቢው ተወላጆች በፖለቲካ ፓርቲ አመራር እና በመንግሥታዊ የኃላፊነት ቦታዎች በበቂ ሁኔታ አለመወከላቸው ነው። «በሀገር አቀፍ ደረጃ ይቅርና የራሳችንን ዞኖች የሚያስተደድሩ እንኳን ከሌላ ቦታ በፖስታ የተላኩልን ናቸው» ሲሉ ቅሬታቸውን አቀረቡ።

ኦፌኮ የሕዝቡን ብዝኃነት የሚያንጸባርቅ አመራር ከላይ እስከታች ለመገንባት ማቀዱን ገለጸንላቸው። ለመጪው ምርጫ በሕዝብ ዘንድ ክብር እና ተደማጭነት ያላቸውን እንዲሁም አቅማቸው የተመሰከረላቸውን እጩዎች እንደምናቀርብ ቃል በመግባት፤ ማንኛውም እጩ በምርጫ ቦርድ ከመመዝገቡ በፊት ለኅብረተሰቡ አቅርበን እንደምናስገመግም፣ ኅብረተሰቡ ካልተቀበለው ከእጩነት እንደምንሠርዝ አሳወቅን።

ከሐረርጌ በኋላ ወደ አርሲ እና ባሌ አቀናን። በሄድንበት ሁሉ ሕዝቡ እያስቆመ ታሪካዊ ቦታዎችን ያስጎበኘናል። ወደ ምሥራቅ አርሲ ዞን ሮቤ ዲደዓ ስንሄድ "ሃሮ ቄሮ" የተባሉ ሁለት ጎን ለጎን ያሉ ትናንሽ ሐይቆች አየን። ቄሮ ነጌሶ የምኒሊክን ወረራ በጀግንነት ተፋልሞ ከታላቅ ተጋድሎ በኋላ ተይዞ የተኮላሸ ሰው እንደነበር የአካባቢው ሽማግሌ አስረዱን። የአካባቢው ሰው ያንን ሐይቅ ለቄሮ ነጌሶ መታሰቢያነት እንደ ቅርስ ተንከባክበው እስካሁን አቆዩት፤ አነስተኛ ሙዚዬምም እጠገቡ ገነቡ።

ሌንጂሶ ዲጋ የተወለደበት ቦታ፣ ድሮ እሱ የተዋጋበትን የሚመስል ፈረስ ሸለሙን። ሌንጂሶ ከጥንት ስመጥር የኦሮሞ ጀግኖች አንዱ ሲሆን፣ የአርሲን ሕዝብ አደራጅቶ፣ ዘመናዊ የጦር መሣሪያ የታጠቀውን የምኒሊክ ጦር በተለያዩ የጦር ሜዳዎች በባሕላዊ መሣሪያ ብቻ ደጋግሞ በማሸነፉ ኦሮሞ እስከዛሬ በስሙ የሚመካበት ነው። ሃሳሳ፣ ሲርካ፣ ዶዶላ እና አዳባ በተካሄዱ ሰልፎች ላይ የወጣው ሕዝብ ብዛት በጣም ያስፈራ ነበር። ፖሊሶች በጥበቃ እንዳያግዙን

የተከለከሉ ቢሆንም ያ ሁሉ ሕዝብ ያለምንም ችግር በሰላም ወደየቤቱ ገባ። ዴራ ላይ እነ ጄኔራል ታደሠ ብሩ ከምዕተ ዓመት በፊት እንዳደረጉት አንድ ኮርማ ክርስቲያን ሙስሊም ሳንል በጋራ አርደን ሕዝቡን በጋራ አበላን።

አርሲን አልፈን ወደ ባሌ ስናቀና፣ ሕዝባዊ መድረክ ከተዘጋጀባቸው ከተሞች በተጨማሪ በምናልፍባቸው የገጠር መንደሮች ሕዝቡ እያስቆመን እና እየተወያየን ጉዟችንን ቀጠልን። በታሪካዊቷ መደ ወላቡ እንደ ዋቆ ጉቱ ያሉ የባሌ ጀግኖችን መቃብር ጎበኘን። በድንበር ግጭት ምክንያት ለተፈናቀሉ ወገኖችም ይዘነው የነበረውን እርዳታ አደረስን። የሶፍ ዑመር ዋሻን ጎብኝተን ጊኒር ስንደርስ ለቁጥር የሚያዳግት ሕዝብ ጠበቀን። ድሮ ዱሙጋ አብሮ አደጌ የነበሩና ለእርሻ ሥራ ወደ ደሎ እና ጊኒር በረሃ ሄደው የሰፈሩ ሰዎችን አገኘሁ። የባሌ ተራሮች አናት ባለው የሳነቴ ኮረብታ ላይ ስንወጣ እንደዚያ ያለ ውብ መሬት ኦሮሚያ ውስጥ እንዳለ አለማወቄ ቆጨኝ። ከባሌ መልስ ወደ ምዕራብ አርሲ ጎራ ብለን በሻሸመኔ እና አካባቢዋ ካሉ የኮፈሌ፣ አጄ፣ አርሲ ነጌሌ፣ ሙኔሳ እና ባቱ ከተማ ነዋሪዎች ጋር ተወያይተን ወደ ፊንፊኔ ተመለስን።

በመቀጠል ወደ ሰላሌ አቀናን። እስከዚያች ዕለት ድረስ መንግሥት ከእኛ ጋር ባይተባበርም እንቅፋት አልሆነብንም። ወደ ሰላሌ ለመሄድ እየተዘጋጀን እያለ፤ የኦፌኮ ሥራ አስፈጻሚ አባል ጉርሜሳ አያኖን ጨምሮ ሌሎች ከእኛ ቀድመው የደረሱት ወኪሎቻችን በኩዩ ከተማ ታሰሩ። እኛንም መንገድ ላይ ባዙቃ የታጠቀ ፖሊስ ጠበቀን። የመኪናውን መስታወት ዝቅ አድርጌ «ይህን መሣሪያ ያመጣችሁት እኛን ልትዋጉበት ነው?› ብዬ እንደቀልድ ስጠይቅ፤ አንዱ ኮማንደር እንደ ማፈር ብሎ «አይ፣ እናንተን ለመጠበቅ ነው» አለኝ። በኩዩ ስብሰባ እንዳናካሄድ ብዙ መሰናክሎች ተፈጠሩብን። ወደ ስብሰባው አዳራሽ የሚወስደውን መንገድ አሸዋ በመኪና አምጥተው በመገልበጥ ዘጉት። ስብሰባ ማድረግ እንደማንችል ስለተገነዘብን *የድርጅቱን አዲስ ቢሮ መርቀን ለመመለስ ወሰንን። ቢሮ ገብተን መርቀን ስንወጣ ሕዝቡ ግልብጥ ብሎ በመውጣት ባሕር ዳር እና አዲስ አበባን የሚያገናኘውን መንገድ ስለሞላው መኪና ላይ ወጥተን አጭር ንግግር አደረግን።*

*ፕሮፌሰር መረራ ባለፉት ምርጫዎች ወደ አካባቢው በመጡ ጊዜ የሰላሌ ሕዝብ ዘፈን አውጥቶ እንደነበር ተናገሩ። ዘፈኑም፣*

Daandii gichaa gichaa

Mallas Zeenaa nurraa galchaa

Diqaalaa nutti dhalcha.

***ሲተረጎም፣***

*የጊቻ መንገድ*

*የጊቻ መንገድ*

*መለስ ዜናዊ ይወገድ*

*ዲቃላ እንዳይወለድ*

*መሆኑን አስታወሱ። አክለውም «የመለስ ዜናዊ ወገኖች ወደ ቀዬአቸው መቀሌ ገብተው፤ እሱ የፈጠራቸው እኩዮች ግን እዚህ ቀርተው አስቸገሩን» አሉ።*

እኔም ቀበል አደረኩና “የዘንድሮው ምርጫ በእነዚያ በመለስ ልጆች እና በእኛ በታደሠ ልጆች መካከል ይሆናል። የታደሠን ቆራጥነት ይዘን የመለስ ልጆችን ሤራ እናከሽፋለን» አልኩኝ፤ በመፈክር መልክ።

ከሰላሌ ስንመለስ የመንግሥት ባለሥልጣናት ንግግራችንን አዛብተው ጠበቁን። አንድ ሰው ደውሎልኝ፣ «ጠ/ሚኒስትር ዐቢይ አሕመድን ዲቃላ አልካቸው» ሲለኝ፤ «ፕሮፌሰር መረራም ሆነ እኔ 'ዲቃላ' የሚለውን ቃል የተጠቀምነው ኦሕዴድን የፈጠረው ሕወሓት በመሆኑ ዲቃላ ድርጅት (bastardized organization) እንደሆነ ለመግለጽ እንጂ በግለሰብ ማንነት ላይ ያነጣጠረ አይደለም» በማለት አብራራሁ።

ከሰላሌ በኋላ የመንግሥት እርምጃ ተጠናክሮ ቀጠለ። በመጀመሪያ ከእኛ ጋር ለመፎካከር ጠቅላይ ሚኒስትሩን የሚደግፍ ሰልፍ በጥቂት ከተሞች ቢያዘጋጁም ለእነርሱ የወጣው ሕዝብ ከእኛ ጋር ሲወዳደር በጣም ትንሽ ነበር። በሰልፍ ከእኛ ጋር መወዳደር እንደማይችሉ ሲገነዘቡ ዘመቻችንን ማደናቀፍ እና ማገድ ላይ አተኮሩ። የምርጫ ቦርድ የምረጡኝ ዘመቻ ከመጀመሩ በፊት የሚደረግ እንቅስቃሴ እንዲያግድ ቢጠይቁም፤ ቦርዱ እኛን ለማገድ የሚያስችል ሕጋዊ ምክንያት አጣ። ከዚያም በጸጥታ አካላት በኩል እርምጃ መውሰድ ጀመሩ።

ከሰላሌ በኋላ ብዙ ሕዝብ ለድጋፍ ሰልፍ አደባባይ ማስወጣት መንግሥትን ስለሚያስበረግገው በአዳራሽ ውስጥ በሚካሄድ ስብሰባ ማወያየት ይሻላል በሚል ሐሳብ ላይ መከርን። በዚሁ መሠረት ሰበታ ላይ ስብሰባ ለማካሄድ ከበቀለ ገርባ ጋር ወደዚያው ስናቀና ፖሊስ ወደ አዳራሽ የሚገባውን ሕዝብ እያዋከበ ነበር። በዚህ ድርጊታቸውም ከእንግዲህ ሕዝባዊ ስብሰባም ሆነ ሰልፍ እንደማይፈቅዱ ግልጽ ስለሆነልኝ ጠንካራ መልእክት ያለው ንግግር አደረኩ። በዚያ ንግግር ላይ ገዢው ፓርቲ የዴሞክራሲያዊ ሽግግር ጭላንጭልን በማክሰም አምባገነናዊ ሥርዓት መልሶ ለመገንባት እየተንደረደረ መሆኑን፤ ይህንንም የኦሮሞን ሕዝብ በኃይል በማፈን፣ በመከፋፈል እና ቄሮን በማዳከም ለማሳካት እንዳሰበ ተናገርኩ። ይህን ለማክሸፍ ሕብረተሰቡ አንድነቱን ጠብቆ ከአመራሩ ጋር እየተናበበ እንዲሄድ አሳሰብኩ።

ከሰበታ ስንመለስ የቡራዩ ከተማ ጸጥታ ዘርፍ ኃላፊ ኮሚሽነር ሰለሞን መገደሉን ሰማን። ከቀናት በፊት በቡራዩ ስብሰባ ለማድረግ ስንጠይቅ የሲቪል አሥተዳደሩ ፈቃደኛ ባለመሆኑ ኮማንደር ሰለሞን ነበር የፈቀደልን። የኮማንደሩን ግድያ ተገን በማድረግ ወጣቶችን በጅምላ አፍሰው አሰሩ ፤ ሌሎችንም ያለ አንዳች የፍርድ ሂደት ረሸኑ። ከቀናት በኋላ የኦሮሞ አመራር ካውንስል በኦሮሚያ ፕሬዝዳንት ቢሮ ባካሄደው ስብሰባ ላይ ስለተገደለው ፖሊስ አንስቼ ነገሮች ወደ ፖለቲካዊ ግድያ እያመሩ ስለሆነ ልንወያይበት እንደሚገባ ሐሳብ አቀረብኩ። ጠ/ሚኒስትር ዐቢይ ግን «መንግሥት ልዩነቶችን በፖለቲካዊ መንገድ ለመፍታት እስካሁን ያደረገው ጥረት ስላልሰራ ራሱን የመከላከል እርምጃ ይወስዳል» አሉ። ወደ ሽመልስ በመጠቆምም የፖሊሱን ገዳዮች አድኖ እንዲያጠፋቸው ነገሩት። ጠ/ሚኒስትር ዐቢይ ከተጠቀማቸው ቃላት እና መልዕክቱን ካስተላለፈበት ስሜት በመነሳት፤ ባለፉት ቀናት ወጣቶችን በጅምላ መግደል ፖሊሶች በንዴት የፈጸሙት ሳይሆን ከላይ የተላለፈ ፖለቲካዊ ውሳኔ ሊሆን እንደሚችል ገመትኩ። ከኮማንደር ሰለሞን ግድያ ጋር ተያይዞ የተጀመረው የተያዙ ሰዎችን ያለ ፍርድ ሂደት መግደል (Extrajudicial Killing)፤ ከዚያም ወዲህ በኦሮሚያ ውስጥ የጸጥታ ኃይሎች በየቀኑ የሚወስዱት ተመራጭ እና ተቀባይነት ያለው አካሄድ ሆነ።

መጀመሪያ ባወጣነው የቅስቀሳ ዘመቻ አቅድ መሠረት ከሰላሌ ቀጥሎ ወደ ጅማ መሄድ ነበረብን። በዞኑ ባሉ አባሎቻችን ላይ ከሚደርሰው ወከባ እና እስር በተጨማሪ አደገኛ የፕሮፓጋንዳ ዘመቻ በመከፈቱ ለመቅረት ወሰንን። ፕሮፌሰር መረራ "ጅማ መሬት እንጂ ሰው የለንም" ብሏል በሚል ጎጠኝነትን የቀላቀለ አስከፊ የስም ማጥፋት ዘመቻ ተከፈተብን። ጅማ የጠ/ሚኒስትር ዐቢይ አሕመድ የትውልድ ቦታ ስለሆነ ጉዟችን በጣም እንዳስፈራቸው ተረዳን።

መንግሥት ወደ ጅማ ለማድረግ ያቀድነውን ዘመቻ አምርሮ መቃወሙ አንድ ነገር አስታወሰኝ። ይህም በአንድ የመማክርት ሰብሰባ ላይ ስለምርጫ ስናወራ፤ ፕሮፌሰር መረራ «በሻሻ እንኳን ብንወዳደር እናሸንፋችኋለን» በማለት ሲቀልድ፤ ጠ/ሚኒስትር ዐቢይ ቁጣ በተሞላበት ድምፅ «እስቲ ሞክረውና እንተያያለን!» ብሎ ነበር። ይህን ያለው በትውልድ ቦታው መሸነፍን እንደ ትልቅ ኪሳራ ስለቆጠረ ነው። በጅማ ዘመቻ ለማድረግ በያዝነው እቅድ የተፈጠረውን ድንጋጤ እና ቁጣ ስናይ ጉዳዩን ወደ እርስ በእርስ ግጭት ሊያሸጋግር ይችላሉ ብለን ስለሠጋን ጉዟችንን ለመሠረዝ ወሰንን። ሌሎች ዞኖች ለመሄድ የያዝነውንም እቅድ አቋረጥን።

ከላይ እንደተገለጸው ያንን የቅስቀሳ ዘመቻ ስናደርግ የነበረው እውነትም ነጻ እና ሰላማዊ ምርጫ ይደረጋል ብለን ድጋፍ ለማግኘት አልነበረም። ገዢው ፓርቲ ወደ ዴሞክራሲ ለመሸጋገር ፈቃደኛ አለመሆኑን እና አምባገነናዊ ሥርዓት መልሶ ለመገንባት እንደወሰነ ባለፉት ሁለት ዓመታት በቅርበት ስንከታተል ስለነበር በሚገባ ተረድተናል። በተጨማሪም ፌደራሊዝሙን ለማፍረስ እየተንደረደረ መሆኑን እና ተመሳሳይ አሃዳዊ አመለካከት ያላቸውን ቡድኖች ወደራሱ እየሳበ ትብብር እያጠናከረ መሆኑንም ተገንዝበናል።

የኦሮሞ ተቃዋሚ ፓርቲዎች ከመጪው ምርጫ የመገፋት ዕድላቸው ሰፊ እንደሆነም መገመት ችለናል። የዘመቻችን ዓላማ ለማዳከም እየሞከሩ ያሉትን የኦሮሞ ብሔርተኝነት በመቀስቀስ እና በኦሮሚያ ድጋፍ እንደሌላቸው በማሳየት ፌደራሊዝሙን ለማፍርስ ያላቸውን አቅድ እንዲያጤኑት ማድረግ ነበር። በዚህም መሠረት በሄድንባቸው ከተሞች ሁሉ ብሔርተኝነትን በማቀንቀን ሕዝቡን ወደ ትግል ስሜት የሚመልሱ ንግግሮች አደረግን። እንዲሁም አገዛዙ የድሮውን አሃዳዊ አምባገነናዊ ሥርዓት ለመመለስ እየሞከረ መሆኑን ሕዝቡ እንዲገነዘብ ማድረግ ላይ አተኮርን። ሕዝቡ በከፍተኛ ቁጥር እና በጋለ ስሜት ይሳተፍ ስለነበር፤ የኦሮሞ ብሔርተኝነትን አዳክሞ ፌደራሊዝምን የማፍረስ ሐሳብ ያላቸውን ቡድኖች አስደነገጠ። ከዚህ ድንጋጤ በመነሳትም ሌሎች ተቃዋሚዎችን ለማዳከም የሚረዱ ስልቶችን መቀየስ ጀመሩ። ከእነዚህም ስልቶች አንዱ የዜግነቴ ጉዳይ ነው።

## 9.5. ሀገር አልባ

ምርጫ ቦርድ "ዜግነቱ ኢትዮጵያዊ ያልሆነን ሰው አባል ማድረግ ሕግ መጣስ ነው" በማለት ለኦፌኮ ደብዳቤ ፃፈ። የአሜሪካ ፓስፖርት ይመልሳል ብለው ስላልጠበቁ በቦርዱ እና በመገናኛ ብዙኃን ዘመቻ ጀመሩ። የአሜሪካ ፓስፖርቴን ለመመለስ የወሰንኩት ገና በ2010 ዓ.ም ወደ ሀገር ቤት ለመግባት የወሰንኩ ጊዜ ነበር። ሀገር ቤት በገባሁ በጥቂት ወራት ውስጥ አንድ ቀን ጠ/ሚኒስትር ዐቢይ አሕመድ የዜግነቴን ጉዳይ አንስቶ ተወያየን።

በፖለቲካዊ አመለካከቱ እና ተሳትፎዬ የሚጠሉኝ ሰዎች ጫና እየፈጠሩበት እንደሆነ ሲነግረኝ፣ «እሱ ችግር የለውም፤ የአሜሪካ ዜግነቴን መልሼ የኢትዮጵያ ፓስፖርት አወጣለሁ» አልኩት።

እሱ ግን «ያለንበት ሁኔታ አስተማምኝ ስላልሆነ ምናልባት አደጋ ካጋጠመን ውጪ ወጥተህ ትግሉን መቀጠል ስላለብህ የአሜሪካ ፓስፖርት እንደያዝክ ቆይ። እንዲያውም ጥምር ዜግነት (dual citizenship) የሚፈቅደውን ሕግ ልናወጣ ስለሆነ ሁለቱንም መያዝ ትችላለህ» አለኝ። እኔም የአሜርካ ፓስፖርት እንደያዝኩ ቆየሁ።

ምርጫ ለመወዳደር ሐሳብ እንዳለኝ ከጠ/ሚኒስትር ዐቢይ ጋር የተወያየን ጊዜ ስለ ፓስፖርት ሳነሳበት፣ «እርግጠኛ ሆነህ እንደወሰንክ ንገረኝና የኢትዮጵያን በአስቸኳይ እንሰጥሃለን»

ብሎኝ ነበር። ኦፌኮን ከተቀላቀልኩ በኋላ ግን የአሜሪካ ፓስፖርቴን መመለስ የማልፈልግ ይመስል ጠንካራ ዘመቻ ተከፈተብኝ። የሌላ ሀገር ፓስፖርት ይዞ በኢትዮጵያ ፖለቲካ ውስጥ የሚሳተፍ ሰው እኔ ብቻ አልነበርኩም። ከለውጡ ጊዜ አንስቶ የጠቅላይ ሚኒስትሩን ቢሮ ጨምሮ በተለያዩ የሚኒስቴር መሥሪያ ቤቶች እና የክልል መሥተዳደሮች ውስጥ የሌላ ሀገር ዜግነት ያላቸው በርካታ ሰዎች ሲሠሩ ነበር። በውጭ ሀገር የቆዩ የፖለቲካ ፓርቲ መሪዎች ሁሉም ሊባል በሚችል ደረጃ በሌሎች ሀገሮች ፓስፖርት ይንቀሳቀሳሉ። አንዳንዶቹ ወደ ሀገር ቤት ከገቡ በኋላ የውጭ ሀገር ዜግነታቸውን በሕጋዊ መንገድ ሳይመልሱ የኢትዮጵያ ፓስፖርት ሲሰጣቸው፤ ብዙዎቹ ደግሞ በውጭ ሀገር ፓስፖርቶች መንቀሳቀሳቸውን ቀጥለዋል። የአሜሪካ ፓስፖርት እንዳለኝ እና ያንን መልሼ የኢትዮጵያን ዜግነት መውሰድ እንደምፈልግ መጀመሪያ በቀጥታ ለጠ/ሚኒስትር ዐቢይ፣ በኋላ በሚዲያ በይፋ ለሕዝብ የገለጽኩ ብቸኛ ፖለቲከኛ እኔ ነበርኩ። እውነቱ ይህ ሆኖ ሳለ ምርጫ ቦርድ እኔ ላይ ብቻ አተኮረ።

በውጪ ሀገር ጉብኝቴ ወቅት በምርጫ እንደምሳተፍ አሳውቄ እንደተመለስኩ የአሜሪካ ዜግነቴን የመመለስ ሂደት ጀመርኩ። መጀመሪያ ስጠይቃቸው፣ በሕይወቴ ላይ ከፍተኛ ተጽዕኖ የሚፈጥር ውሳኔ ስለሆነ ጊዜ ወስጄ እንዳስብበት በመምከር፣ ዜግነት የመመለሴን ሂደት ለመፈጸም ተጓተቱ። እኔ ግን ወስኜ ስለነበር፤ ወደ ኤምባሲ ሄጄ ፓስፖርት በማስገባት ዜግነቴን በፍላጎት መቀየሬን የሚያሳይ ሰርተፊኬት ተቀበልኩ። የኢትዮጵያ ዜግነት በድጋሚ እንዲሰጠኝም የአሜሪካ ዜግነት መመለሴን የሚያሳይ ማስረጃ በማያያዝ አመለከትኩ። ፓስፖርት የመለስኩት የምርጫ መስፈርት ለማሟላት ብቻ አልነበረም። ወደ ሀገር ቤት ስገባ

ከሕዝቤ ጋር ደግ እና ክፉውን ለመቀበል ቃል ገብቼ ስለነበር፤ ችግር ሲመጣ ያንን ቃል አጥፌ እንዳልሄድ ሁሉም ዕድሎች እንዲዘጉ ለማድረግም ጭምር ነው። ይህ እርምጃዬ እስከ ዛሬ ድረስ በጣም ያኮራኛል። ምርጫ ቦርድ ግን የአሜሪካ ዜግነት መልሼ የኢትዮጵያን ለማግኘት ማመልከቻ ማስገባቴን የሚያሳይ ማስረጃ ባቀርብም ፓርቲው ከአባልነት እንዲሠርዘኝ መጨቅጨቁን ቀጠለበት። የወቅቱ የቦርዱ ሊቀመንበር ወ/ት ብርቱካን ሚደቅሳ የኢትዮጵያ ዜግነት ማግኘቴን የሚያሳይ ማስረጃ ማቅረብ እንዳለብኝ ለፓርቲው አሳወቀች። ሌሎች የቦርዱ አባላት አካሄዷ ትክክል እንዳልሆነ ቢማጸኗትም ልትሰማቸው እንዳልፈለገች ይነግሩኝ ነበር። በአንድ በኩል ምርጫ ቦርድ የኢትዮጵያ ዜግነት ያገኘህበትን ማስረጃ አምጣ ብሎ ሲያጣድፈኝ፣ በሌላ በኩል ደግሞ ዜግነት እንዲሰጠኝ ያመለከትኩበት የዜግነት እና የኢሚግሬሽን ተቋም ሂደቱን አጓተተው።

በሕጉ መሠረት ቀደም ብሎ የኢትዮጵያ ዜጋ የነበረ ሰው በኋላ የወሰደውን የውጪ ዜግነት ከመለሰ ወዲያውኑ የኢትዮጵያ ዜግነት ይሰጠዋል። የኢሚግሬሽን ሰዎች ግን አንዴ በኮሚቴ መታየት እንዳለበት እና በየቀጠሮው አባላቱ እንዳልተሟሉ በመግለጽ፤ በሌላ ጊዜ ወረፋ የሚጠብቁ ብዙ አመልካቾች ስላሉ ጠብቅ በማለት ሂደቱን አራዘሙት። የኢሚግሬሽን ሰዎች ዜግነት እንዳይሰጡኝ በቀጥታ ከበላይ ባለሥልጣናት እንደታዘዙ ስለሰማን ጉዳዩን ወደ ፍርድቤት ለመውሰድ ወሰንን።

በዚህ መልኩ የአሜሪካ ዜግነቴን መልሼ የኢትዮጵያን ሳላገኝ ሀገር አልባ (Stateless) ሆኜ ባለሁበት ሁኔታ፣ ያልተጠበቀ አደጋ ዓለማችንን አጋጠማትና ምርጫው ተራዘመ፣ እኔም ታሰርኩ።

## 9.6. የኮሮና ቫይረስ እና ምርጫ

ኦፌኮ ያካሄደው የቅስቀሳ ዘመቻ ሀገሪቱን ወደ ምርጫ ድባብ አስገብቷት እያለ ፍጹም ያልተጠበቀ አደጋ ዓለምን አጋጠማት። ይህ ያልተጠበቀ አደጋ የኮሮና ቫይረስ፣ የCOVID-19 ወረርሽኝ በድንገት መከሰት ነበር። ከቻይና ተነስቶ በከፍተኛ ፍጥነት ዓለምን በማዳረስ ላይ የነበረውን የኮሮና ቫይረሰ ወረርሽኝ ለመግታት፣ በሀገራት መካከልም ሆነ በሀገር ውስጥ የሚደረግን የሕዝብ እንቅሰቃሴ መገደብ አንደ መፍትሔ ተቀመጠ። በዚሀም ምክንያት ግንቦት 2012 ዓ.ም ሊደረግ የታቀደውን የኢትዮጵያ ምርጫ ማራዘም ግድ ሆነ።

ሕገ-መንግሥቱ ምርጫማራዘምን ስለማይፈቅድ፣ በአስገዳጅ ምክንያት ማራዘም በሚቻልበት ሂደት ላይ ውዝግብ ተነሳ። በኦፌኮ በኩል በወረርሽኝ ምክንያት ምርጫው መራዘሙ ትክክል መሆኑ ቢታመንም ሕገ-መንግሥቱ ምርጫ የሚራዘምበትን መንገድ በግልጽ ባለማሰቀመጡ፤ እንዴት እና መቼ ይተላለፋል በሚለው ላይ የገዢው ፓርቲ አመራር እና ተቃዋሚዎች ተወያይተው መወሰን አለባቸው የሚል አቋም ያዝን። ገዢው የብልጽግና ፓርቲ ግን ከተቃዋሚ ፓርቲዎች ጋር መደራደር አልፈለገም። ይልቁንም "ሕገ-መንግሥታዊ ትርጓሜ" በሚል አሠራር በሚቆጣጠራቸው ፍርድ ቤቶች እና ምክር ቤቶች በመጠቀም ምርጫውን በደፈናው ማሰተላለፍን መረጠ። ኦፌኮ ገዢው ፓርቲ ምርጫውን ለማስተላለፍ የተከተለው መንገድ ኢ-ሕገመንግሥታዊ መሆኑን እና ከአካታች ውይይት ይልቅ ምርጫውን ለብቻው ለማራዘም መወሰኑ ሀገሪቱ የገባችበትን የፖለቲካ ቀውስ የሚያባብሰ እንደሆነ አሳሰበ። ሳይታሰብ ባጋጠመን አደጋ ምርጫ መራዘሙን እንደ ዕድል ተጠቅመን ሀገራዊ መግባባት ለመፍጠር መሥራት እንደሚሻል ብንጠቁምም ገዢው ፓርቲ ለመስማት አልፈቀደም።

እንደፈራነው የትግራይ ክልል የፌደራል መንግሥት ምርጫውን ማራዘሙን በመቃወም በክልል ደረጃ ምርጫ እንደሚያካሄድ አስታወቀ። የሀገሪቱ ምርጫ ቦርድ በበኩሉ ውሳኔያቸውን አልቀበልም ቢልም የትግራይ ክልል መስተዳደር በውሳኔው ጸና። የምርጫው ውዝግብ ላለፉት ሁለት ዓመታት ሲባባስ ቆይቶ ቋፍ ላይ የደረሰውን የትግራይ ክልል እና የፌደራል መንግሥት ግንኙነት እንዲቋረጥ አድረገ፡ ከጥቂት ወራት በኋላ ወደ ጦርነት አመራ።

ምርጫው የተራዘመበትን አሠራር በጽሑፍ እና በመገናኛ ብዙኃን አጥብቄ ስቃወም ነበር። ከልደቱ አያሌው ጋር በOMN ቃለ-መጠይቅ ባደረግንበት ወቅት ገዢው ፓርቲ ምርጫውን ለማስተላለፍ ሕጋዊ እና አካታች አሠራር ካልተከተለ ያሁኑ ፓርላማ ዘመን ከመሰከረም 30 በኋላ ስለሚጠናቀቅ ሀገርን ማሰተዳደር የሚያስችል ቅቡልነት እንደማይኖረው ገለጽን። ይህ ደግሞ በዜጎችም ሆነ በመንግሥት የጸጥታ ኃይል አመጽ ሊያሥነሳ እንደሚችል አሳሰብን። በዚሀ ተቃውሞዬ የተነሳ ከመንግሥት ባለሥልጣናት ጋር የነበረኝ የሻከረ ግንኙነት ሙሉ ለሙሉ ተበጠሰ። የቃላት እና የተግባር ማስፈራሪያዎች አና ትንኮሳዎች ተባባሱ። ከመኖሪያ ቤቴ ግራ እና ቀኝ ያሉ ሁለት ቤቶችም ድንገት ፈረሱ። ለምን አንደፈረሱ ስንመረምር በባለሀብቶች በከፍተኛ ገንዘብ ተገዝተው እንዲፈርሱ መደረጉን ለማወቅ ቻልን። ከዚህ ቀደም የጥቃት ሙከራ ሲደረግብኝ ጠባቂዎቼ ቢቶቹን እንደ ሽፋን በመጠቀም ወደ ግቢዬ

ለመግባት የተደረገውን ሙከራ ስላከሸፉት፡ የቤቶቹ መፍረስ ቤቴን ነጥሎ ለማጥቃት እንደሆነ በመጠርጠር በንቃት መጠባበቅ ጀመርን።

አንድ ቀን የኦሕዴድ ጉምቱ ባለሥልጣን የሆነ ግለሰብ ቀጥሮኝ ስናወራ ዕድሉን ካገኘሁ ከሀገር እንድወጣ መከረኝ። «ካልሆነ ግን ዕድለኛ ከሆንክ ትታሰራለህ ወይም የባሰ ነገር ሊከተልህ ይችላል» ሲለኝ፤ ከዚህ በኋላ የፈለገው ይመጣል "እኔ ሀገሪሬን ለቅቄ የትም አልሄድም" በማለት መለሰኩለት። «እኔ ከራሴ አውርጃለሁ›› ብሎኝ ሄደ። እኔም ሊያስሩኝ ወይም ሊገድሉኝ ዝግጅት እንደጨረሱ በመረዳት ለሁለቱም ራሴን አዘጋጀሁ። በአንድ በርሳ የምቀበርበትን ነጭ አቡጀዲ፣ በሌላኛው ለአስር ቤት የሚሆን ቱታ እና ጫማ መኝታ ቤቴ ውስጥ አስቀመጥኩ። የደረሰኩበትን ድምዳሜ ቤተሰብ እና ጓደኛቼ አውቀውብኝ እንዳይሸበሩ ሳቅ እና ጨዋታዬ ከመቼውም ጊዜ በላይ ጨመረ። በዚህ መሀል በአንዲት የተረገመች ምሽት ሀጫሉ ሁንዴሳ ተገደለ፡ እኔም ታሰርኩ፡ የኦሮሞ እና የኢትዮጵያ ፖለቲባም ከባድ ውጥንቅጥ ውስጥ ገባ።

## ትውስታ በምስል #4





በሚሊኒዬም አዳራሽ በተዘጋጀልኝ አቀባበል ላይ ለአራት ዓመታት ስታበልባት የነበረችዉን ኮምፒዩተር ለለማ ሳበረክት።



ፕሬዝዳንት ሙላቱ ተሾመ በብሔራዊ ቤተ መንግሥት ግብዣ ባነጋገሩን ወቅት።



አምቦ ስንደርስ በትግሉ ወቅት ቃል እንደገባሁት ባዶ እግሬን በጎዳናው ላይ ስሄድ።



ወደ አምቦ እየሄድን ኖቬምበር 12/2014 የቄሮ ትግል በተለኮሰባት ጊንጪ ስተማ ሰንደርሰ ምስጋና ለማቅረብ ጎራ ባልንበት ወቅት።



አምቦ አቀባበል ላይ ስኮሚሽነር ደቻሳ ቢቲማ፣ ደረጃ ሀዋዝ እና ዝግጅቱን በመሪነት ካሰናዳው የአምቦ ዩኒቨርሲቲ ፕሬዝዳንት ዶ/ር ታደሰ ቀነዓ ጋር።



ሀገር እንደተመለስኩ የረዳኝን ፈጣሪ ለማመስንን ሃጅ ባደረኩብት ጋ ተ የድምጻችን
ይሰማ እመራር አንዱ ከነበረው ከኡስታዝ ካሚል ሾምሱ



ወደ ሀገር ተመልሼ ከአባገዳዎች ጋር ኢሬቻን በመታደም ፈጣሪን ለማመስንን ስንሄድ።



ወደ አደኩባት ጴሙጋ ተመልሼ ከሀገር ሽማግሌዎች ጋር ስንጫወት አደርን።



ወደ ሀገር ከተመለስኩ በኋላ ከእናቴ ጋር።



በልጅነቴ በጀግንነቱ ስሙ ሲጠራ በመሰማት ሳድግ የሱን ፈለግ ለመከትል ሰመኝ የነበረውን የኦነግ ጦር ኮማንደር ባባሳ ገዳን ስዊድን ሀገረ አገኘሁት።



በልጅነቴ ስማቸው ገኖ ሲነገረን ከነበሩት የኦነግ ሠራዊት ኮማንደሮች አንዱ የሆነውን አብደታ ሃጂ ቡናን ወደ ሀገር ተመልሼ ዱሙጋን ሰጎበኝ የእኔን ጥበቃ ሲያቀኖጅ አኘሁት



ከሃይማኖት መሪዎች ጋር ስለ ሰላም እና መቻቻል ስንሰብክ




OMN በናይሮቢ የከፈትን እለት የኬንያ ኦሮሞ ማህበረሰብ የመንግሰት ተመራጮ አመራሮች ጋር ።



የሐረሪ ክልልን ሲመራ በነበረው ፕሬዝዳንት አቶ ሙራድ
አብዱልሃዲ ጋር ስተማዋን ወደሰለም ላመመለስ
በሚያሰፈልጉ ሥራዎች ላይ በእኔ ቤት ሰንወያይ።



ሙራድ አብዱልሃዲን ተክተው አዲሰ ከተሾሙት የሀረሪ ክልል
ፕሬዝዳንት ኦርዲን በድሪ ጋር ከተማዋን ወደ ዘላቂ ሰላም
ለማሸጋገር በተወያየንበት ወቅት።



ሙስጠፋ ሙሐመድ የሶማሌ ክልል ፕሬዝዳንት ሆኖ ከተሾመ በኋላ ከምክትሉ ኢብራሂም ኡሰማን ጋር የድሬ ደዋን ሕዝብ
ለማነጋገር በሄድንበት ወቅት።



በምዕራብ ኦሮሚያ የነበረውን ግጭት ለመረዳት በተጓዝንበት ወቅት ለፌዴሬሽን ምክርቤት ስብሰባ በአሶሳ ለማካሄድ ወደዛው
ተጉዘው የነበሩትን አፈጉባዔ ኬሪያ ኢብራሂም እና በወቅቱ የጠቅላይ ሚኒሰትር ቃል አቀባይ ንጉሱ ታምራትን ባወያየንበት ወቅት።





ከሃላባ ዞን አመራሮች ጋር በቋንቋቸው የሚተላለፍ ሚዲያ ለመንንባት በተወያየንበት ወቅት።

የአፋርን ሕዝብ ለማነጋገር ሰመራ በሄድኩበት ወቅት።



የሲዳማ አመራሮች በሐዋሳ አውሮፕላን ማረፊያ አቀባበል ሲያደርጉልኝ። በወቅቱ የደቡብ ክልል ፕሬዝዳንት ሚሊዮን ማቲዎስ እና የሲዳማ ዞን አስተዳዳሪ ቀሬ ቀዊቻ ይገኙበታል።



ወሎን በጎበኘሁበት ጊዜ ከመከላከያ ሠራዊት አባላት ጋር።



ከለውጡ በፊት በሰብዓዊ መብት ጥሰት የሚታወቀው የክልሉ ልዩ ኃይል ከረፎርም በኋላ ጅግጅጋ ሄጄ ሳገኛቸው።



የኦሮሚያ ፖሊሶች በትግሉ ወቅት ለሕዝብ በመወገናቸው በተገኘሁባቸው መድረኮች ምስጋናዬን አገልጽ ነበር። ሕዝብ በስጦታ የሚያበረክትልኝን ሰንጋዎችም ለፖሊሶች እሰጥ ነበር። እነሱም በእጀባ እየተንከባከቡ ተቋማቸውን የሚያስፈልገውን ለውጥ ይነግሩኛል።



በቄሮ ትግል ወቅት በሕዝብ ላይ ሲተኩሱ የነበሩ የአጋዚ ወታደሮች ላይ መሣሪያውን አዞሮ የተሰዋው ኮንስታብል ሙስጠፋ ሁሴን።



ከቀድሞ የኦነግ ሊቀመንበር፣ ገላሳ ዲልቦ እና ምክትላቸው ሌንጮ ለታ ጋር።



የጨለንቆ ሰማዕታት ሀውልትን ከኘ/ር መረራ ጉዲናጋር ሰንጎበኝ።



ከአባገዳ በየነ ሰንበቶ እና አቦ ሌንጮ ለታ ጋር የአኖሌ ሰማዕታት መታሰቢያ ሀውልትን ስንጎበኝ።



ከአንጋፋው ታጋይ፣ የኦነግ አመራር እና የጅማው ንጉስ ልጅ ከሆኑት አባቢያ አባጆቢር እና ከዕውቁ የገዳ ሥርዓት ተመራማሪ ፕ/ር አሰመሮም ለገሰ ጋር።



በ1991 የሽግግር ወቅት የኢትዮጵያ ትምህርት ሚኒስቴር ሆነው ውስጥ ትምህርት በአፋን ኦሮሞ እንዲሰጥ ካደረጉት አቶ ኢብሳ ጉተማ እና የቀድሞው የኦነግ ሊቀመንበር ገላሳ ዲልቦን በቤቴ ምሳ በጋበዝኩበት ወቅት።



አንጋፋ የኦሮሞ ታጋይ እና ምሁር የመሬት ላራሹን እዋጅ ኦሮሚያ ካረቀቁቱት አቶ ዘገየ አስፋ እና ፕ/ር እዝቃኤል ንቢሳ ጋር የኦነግ አመራር ከእሰመራ ወደ ሀገር ሲገቡ ሰንቀበል።



ከሃጂ ሁሴን ሱራ ጋር ደማስከስ ውስጥ የኦሮሞን ትግል ቢሮ ሲያደራጁ ከነበሩት አባ እናጂና ጋር።



አልጀዚራ ላይ ቀርቤ Oromo First ባልኩበት ወቅት



ኦሮሞ ፈርስትን ያሰተጋባሁበትን አልጄዚራ ከድሉ በኋላ ስጎበኝ።



ወለጋ በሄድንበት ወቅት ቄሮ የዘጋብንን መንገድ ስንከፍት ፖሊሶች "ያስተማርካቸውን አንተው ላይ ተጠቀሙት" ብለው ቀለዱ።



የወለጋን ሕዝብ ለማነጋገር በሄድንበት ወቅት ከበቀለ ገርባ እና ከኦነጉ ወጣት አመራር ለሚ ቤኛ ጋር።





የኦነግ ሠራዊት ወደ ሰላም እንዲመለስ በግንባር ቀደምነት ሲጥሩ የነበሩት አቶ ኃይሌ ገብሬ የአባገዳን ጥሪ ተቀብለው የመጡ ወታደሮችን ሲረከቡ።



የኦነግ ሠራዊት ጦርነት አቁሞ ወደ ሰላማዊ መንገድ        በየዱሩ ገደሉ ሲዋጉ የነበሩ የኦሮሚያ ፖሊስ እና የኦነግ ጦር አባላት  እንዲመለስ
ለማግባባት ወደ ደቡብ ኦሮሚያ በታኃዝኩ        በአባገዳዎች የእርቅ ሰላም ጥረት ወቅት ተገናኝተዉ ሲተቃቀፉ።        ወቅት የጉጂዉን

አባገዳ ጂሎ ማንዶ ቀልድ ቀላቅለዉ
ሲመርቁኝ።



በቤቴ ጥቃት ከተሞከረብኝተ በኃላ ሁሉም የኦሮሞ ፖለቲካ መሪዎች መጥተዉ ድርጊቱን በጋራ ባወገዙት ወቅት



የኦሮሞ አመራር መማክርት መግልጫ ሲሰሰጡ።



ለምርጫ 2020 የኦሮሞ ድርጅቶችን ጥምረት ለመመሥረት ዉይይት ላይ (ፕ/ሮ መረራ፣ ጄ/ል ከማል፣ አቶ ዳዉድ እና ቀጄላ መርዳሳ)











የኦፌኮን የምርጫ ቅስቀሳ በተለያያዩ ዞኖች።

# ክፍል አስር - ረጅሙ እረፍት

## 10.1. የሀጫሉ መገደል

ለአንደኛው የዓለም ጦርነት የኦስትሮ-ሃንጋሪው ልዑል ፍራንዝ ፈርዲናንድ፣ ጋቭሪሎ ፕሪንሲፕ በተባለ የሰርቢያ አክራሪ መገደሉ ክብሪቱን ሊያቀጣጥል ችሏል። የልዑሉ ደም ቤንዚን ሆኖ አውሮፓን ጨምሮ መላውን ዓለምን ያዳረሰ ፍጅት እና ውድመት አስከተለ። የፈርዲናንድ መገደል ብቻውን ግን ለአንደኛው የዓለም ጦርነት መከሰት በቂ ምክንያት ሊሆን አይችልም። ከዚያ በፊት የአውሮፓ ፖለቲካ በመቃቃር፡ በወታደራዊ ፉክክር እና በድንበር ውዝግብ አብጦ ሊፈንዳ ተቃርቦ ነበር። ግድያው ያበጠውን ፖለቲካ አፈንድቶ በዝግጅት ላይ የነበሩ እና በዓይነ ቁራኛ ሲተያዩ የቆዩ ኃይሎችን ፊት ለፊት አላተማቸው።

የሀጫሉ ሁንዴሳ ግድያም በኦሮሞ አና በኢትዮጵያ ፖለቲካ ውሰጥ አየተባባሰ የነበርውን ውጥረት በማፈንዳት አሁንም ድረስ ሀገሪቱን በየአቅጣጫው አየናጠ ወዳለው የአርስሰ በእርሰ ግጭት የከተተ አሳዛኝ ክስተት ነው። ከአንደኛው የዓለም ጦርነት በፊት አንደነበረው የአውሮፓ ፖለቲካ፣ ከሀጫሉ ሁንደሳ ግድያ በፊት በኦሮሞ እና በኢትዮጵያ ፖለቲካ ውሰጥ በተለያዩ ወገኖች መካከል ያለው መቃቃር፡ዛቻ እና ቅራኔ ከቀን ወደ ቀን እየተጠራቀመ እና እየተባባሰ ሄዶ አብጦ ነበር። የሀጫሉ ግድያ ያበጠውን የፓለቲካ ቀዉስ አፈነዳው።

የሀጫሉ ሁንዴሳን ግድያ ተከትሎ መንግሥት በኦሮሞ ላይ የከፈተው እሥራት እና ግድያ በሺዎች የሚቆጠሩ ወጣቶች የትጥቅ ትግል ለማድረግ ወደ ጫካ እንዲያመሩ ምክንያት ሆነ። በኦሮሞ ልሂቃን እና በሕዝቡ መካከል ከፍተኛ መሰንጠቅ ፈጠረ። በአጠቃላይ የሀጫሉ ግድያ የኦሮሞን ሕዝብ ለጥልቅ የልብ ስብራት ያጋለጠ ክስተት ነው ማለት ይቻላል። በዚህ ሕዝብ የቅርብ ጊዜ ታሪክ ውስጥ እንደዚያች ዕለት የጋራ ድንጋጤ እና ሀዘን አጋጥሞ አያውቅም። ኦሮሞ በዚያ ቀን ከተፈጠረበት ድንጋጤ እና ቁጣ ዛሬም ድረሰ ያገገመ አይመስለኝም።

እኔንም በሀጫሉ ግድያ አመካኝተው አሰሩኝ፤ ከአስሩ በላይ የጎዳኝ ግን የረጅም ጊዜ ወዳጄን እና የክፉ ቀን የትግል ጓዴን ሀጫሉን መነጠቄ። ሀጫሉን በሙዚቃው ያወቅኩት ኮሎምቢያ ዩኒቨርሲቲ ተማሪ ሳለሁ ነበር። በወቅቱ በቤቴ እና በዩኒቨርሲቲዬ መካከል በባቡር ስመላለሰ ዘፈኑን ደጋግሜ በማዳመጥ እመሰጣለሁ። ቤተ-መጻሕፍት ውሰጥ ሳጠና እና ስጽፍ በሀጫሉ ዘፈኖች እራሴን አነቃቃለሁ።

የሰላማዊ ትግል ስትራቴጂ ለመንደፍ ብዙ እያብሰለሰልኩ እና እራሴን እያዘጋጀሁ የነበረበት ወቅት ስለነበር፡ "ኦሮሚያ ቲያ" እና "ማሳን ገማ" የተሰኙ ዘፈኖቹ መነቃቃት እና ብርታትን

አጎናጽፈውኛል። አወዛጋቢውን "Oromo First" አባባል የተጠቀምኩበትን የአልጀዚራ ቃለ-ምልልሰ ለመስጠት ከኒው ዮርክ ወደ ዋሸንግቶን ዲሲ በባቡር ሰጓዝ "ማሳን ገማ" የሚለውን ዘፈን ደጋግሜ እየሰማሁ ነበር። ወደኋላ መለሰ ብዬ ሳስበው በቃለ-ምልልሱ ላይ ያንጸባረኩት ስሜት ውሰጥ የከተተኝ ዘፈኑ ይመሰለኛል።

የOromo First ዘመቻ ወቅት ከኤሊያሰ ኢብሳ ጋር ስንወያይ ሀጫሉን ወደ አሜሪካ አያመጡት መሆኑን ነገሮኝ፣ ያቀዱት ኮንሰርት ሕዝቡን ለማነቃቃት እያደርግን ላለነው ጥረት ጠቃሚ እንደሚሆን ተግባባን። ከሀጫሉ በተጨማሪ ጃምቦ ጆቴ፣ አቡሽ ዘለቀ እና ንጉሥ

ታምራት መጥተው በተለያዩ የሰሜን አሜሪካ ከተሞች በመዞር "ኦሮሚያ ቲያ" የተሰኘ ኮንሰርት ማካሄድ ጀመሩ።

ብሔራዊ ስሜትን በሚቀሰቅሱ ዘፈኖች የደመቀው የኦሮሚያ ቲያ ኮንሰርት መጀመሩ የሕዝቡን ስሜት የበለጠ ስላጋጋለው፡ የ"Oromo First" ዘመቻ ላይ በውጪ ያለውን የኦሮሞ ማኅበረሰብ በራስ መተማመን (collective self-esteem) ከፍ ለማድረግ ለምናደርገው ሥራ ትልቅ አስተዋጽዖ አበርክቷል። በብዙ ከተሞች ውስጥ ቀን ላይ የኦሮሞ ፈርስት ስብሰባ፣ ማታ ላይ ደግሞ የኦሮሚያ ቲያ ኮንሰርት ይካሄዳል። አርቲስቶቹ ወደ ሀገር ሲመለሱ ችግር እንዳይፈጠርባቸው፤ እነሱ ስብሰባችን ላይ እንዳይታዩ፣ እኛም ኮንሰርታቸው ላይ ላለመታየት እንጠነቀቃለን።

እነዚያ አርቲስቶች እኔ እና አርፋሴን ሊጠይቁን ወደ ኒውዮርክ ሲመጡ ብዙ ተጨዋወተን በቅርበት ለመተዋወቅ በቃን። ሀጫሉ ተጫዋች፣ ብልጥ፣በሳል እና ቆራጥ ብሔርተኛ እንደነበር ከረዥሙ ውይይታችን ተረዳሁ። እሱ ባለበት ቦታ ድብርት የለም። አንድ ቀን በከተማው ካለ ረጅም ሕንፃ እራት ልንጋብዛቸው ወጣን። የነበርንበት ምግብ ቤት ክፍል የሚሽከረከር ነበር። ሀጫሉ ወሬ ይዞ ስለነበረ መጀመሪያ ልብ አላለም። ድንገት ጨዋታውን በመሀል ገታ አድርጎ በዓይኖቹ ወደ መሰኮቱ ትኩር ብሎ ሲያይ ቆየና፣ «እናንተ እኔ ነኝ የዞረብኝ ወይስ ቤቱ ነው የሚዞረው?» ብሎ አሳቀን። አሜሪካ በነበሩበት ወቅት ስለ ኦሮሞ ትግል ሁኔታ በተደጋጋሚ ሰፊ ውይይት አድርገናል። ኮንሰርቱን እንዳጠቃለለ ሀገር ቤት ከተመለሰ አደጋ ላይ ሊወድቅ ይችላል ብዬ ስለሠጋሁ ውጪ እንዲቆይ ስመክረው «ሞቴም ሕይወቴም ከሕዝቤ ጋር ነው! እንኳን እኔ ልቀር አንተም በቅርቡ ትመጣለህ፣ ብሉ በቆራጥነት ተናገረኝ። ወደ ሀገር ቤት ከገባ በኋላም ተቃውሞው እየተቀጣጠለ በነበረበት ወቅት በየጊዜው በስልክ ስንገናኝ ቆይተናል። ወገኖቻችን ከሶማሌ ክልል ሲፈናቀሉ ከፍተኛ ንዴት እና ጭንቀት ውስጥ ገብቶ እርዳታ ይዞ ወደ ሐረርጌ ለመሄድ መዘጋጀቱን ደውሎ ሲነግረኝ በመንገድ ላይ እንዳይጎዱት ሰግቼ እንዲቀር ብለምነውም አምቢ ብሉኝ ሄደ።

በለውጡ ዋዜማ በሚሊኒየም አዳራሽ በተዘጋጀ ኮንሰርት ላይ እንደተጋበዘ ደውሎ ነገሮኝ፣ ምን ዓይነት ዘፈን ቢዘፍን ለትግሉ እንደሚጠቅም በጠየቀኝ ጊዜ ትግሉ በወቅቱ የደረሰበትን ደረጃ እንዲሁም ቀጣዩን ምዕራፍ ሰፋ አድርገን ተወያየን። ከዚያም ብዙ ሳይቆይ በኮንሰርቱ ላይ ለማቅረብ ያዘጋጀውን የሽለላ ግጥም ላከልኝ።

አንብቤው ሰጨርስሰ «ይህን ከሽለልክ ያጠፉሃል» አልኩት። «የፈለገው ነገር ይምጣ፣ እሱን ለእኔተወውና የሽለላው ይዘት ላይ ሐሳብህን ስጠኝ› አለኝ። ጥቂት ነጥቦችን ጨምሬ በውይይት አዳበርነው። እንዳቀደውም መድረክ ላይ ሽለላውን ሲያፈነዳው ጠላትን አስበርግጎ፣ የኦሮሞን አንጀት አራሰው።

የዚያን ቀን የሀጫሉ ሽለላ በመድረኩ የታደመውን ሕዝብ ሞራል ከፍ ከማድረግ ያለፈ ትርጉም ነበረው። ሽለላው የኦሮሞ ትግል ታሪክ መቀየሩን በይፋ አወጀ። የኦሮሞ ትግል ታሪክ ለረጅም ዘመናት አራት ኪሎ ላይ የሰፈነውን የኢትዮጵያ ሀገር መንግሥት በማውገዝ ላይ ያተኩራል። በሌላ አነጋገር ኦሮሞ ራሱን ከአራት ኪሎ ውጪ በመመልከት አንድም ያለው መንግሥት ጭቆና እንዲያቆምለት፡ አሊያም ራሱን ከአገዛዙ አላቆ ሌላ ሀገረ መንግሥት መገንባትን ያለመ ነው። ባለፈው ምዕራፍ ውሰጥ እንደተገለጸው በቄሮ ትግል ጊዜ የትግሉን ታሪክ ኢትዮጵያን ከውጪ ከመውቀስ ወደ መቆጣጠር አሸጋገርነው። ከአራት ኪሎ መልስ ከመጠበቅ ይልቅ

በታውን ተቆጣጥሮ በደልን በማስቀረት ተጠቃሚ መሆን ያስፈልጋል ወደሚለው አደገ። ይህን በስውር ሲካሄድ የነበረ የታሪክ ሽግግር ሀጫሉ በገሃድ «አራት ኪሎ ላንተ ነው የምትገባው» ብሎ በሽለላው አፈረጠው።

የሽለላው ጭብጥ ለኦሮሞ የሚበጀው ኢትዮጵያን እንደ ባዕድ ከማየት ይልቅ ባለቤትነትን ማረጋገጥ ይሻላል የሚል ነው። ለዚህ የባለቤትነት ማረጋገጫ ደግሞ በአድዋ ጦርነት ታሪክ ላይ የኦሮሞ ጀግኖችን ሚና ዘርዝሮ ያቀርባል። ስለዚህም የኢትዮጵያ መንግሥታት ቢጎዱኝም በአባቶቼ ምድር ላይ በአጥንታቸው የሠሩትን ሀገር እወርሳለሁ እንጂ ጥዬ አልሄድም፣ አላፈርሰውም ይላል። በወቅቱ የታሪክ ሽግግር የማድረግ አስፈላጊነትን የተረዳ ሰው በጣም ውሰን እንደነበር ሳስታውስ፡ የሀጫሉ ብስለት እና አርቆ አሳቢነት ይገርመኛል።

ዐቢይ አሕመድ ጠቅላይ ሚኒስትር መሆኑን የተቃወምኩ ሰሞን ሀጫሉ ደውሎልኝ ለረጅም ስዓት ተከራክረናል። «ማንም ይሁን ኦሮሞ ከሆነ መደገፍ አለብን› የሚል ሐሳብ ነበረው። ዐቢይን አግኝቶ እንዳነጋገረው በመጥቀስ ሊያሳምነኝ ሞከረ። ጠ/ሚስተር ዐቢይ አሜሪካ በመጣ ጊዜ እንዳነጋገርኩትና የሽግግር አመራር መሆን እንደማይችል መገንዘቤን ነገርኩት። ከረጅም ክርክር በኋላ እሱ በድጋፉ እኔም በተቃውሞዬ ለመቀጠል ተሰማማን።

«ባትደግፈውም ለኦሮሞ አንድነት ስትል በሚዲያ እሱ ላይ የምታደርገውን ተቃውሞ ቀንስ» በማለት ሲማጸነኝ፡ «ችግር የለውም፤ እንዲያውም አቆማለሁ አልኩት። በመጨረሻም «ግምገማህ ትክክል ከሆነ አወዳይ ላይ በማስቃም ትቀጣኛለህ፣ የእኔ ትክክል ከሆነ ደግሞ አምቦ በጠጅ አስክሬ እቀጣሃለሁ›› ብሎኝ በቀልድ ተሰናበተኝ።

ወደ ሀገር ቤት በገባሁ ማግሰት አምቦ ስሄድ ሀጫሉ ከእኔ ቀድሞ በመድረስ ሁኔታዎችን አመቻችቶ ጠበቀኝ። አስቀድሜ እንደገለጽኩት ከመኪና ወርጄ በባዶ እግሬ መሄድ ስጀምር እየሮጠ መጥቶ እጅ ለእጅ ተያይዘን ጓደኛው ጃገማ በዳኔ በተሰዋበት ቦታ ለማስታወሻ የዋርካ (ኦዳ) ዛፍ ተከልን። ከዚያ በኋላ በተለያዩ ጊዜያት በአካልም በስልክም እንወያይ ነበር። ከመገደሉ ጥቂት ወራት በፊት ከተማ ውስጥ መኪና ሲነዳ በጣም ይተናኮሉት ስለነበር፤ አንድ ቀን ደውሎ በመኪና እየተከታተሉት እንደሆነ ነገረኝ። ከደህንነት ኃላፊዎች ለአንዱ ደውዬ እንዲያስቆሙለት ስጠይቅ፡ ሀጫሉም የሚከታተሉት ሰዎች ወዲያው መሰወራቸውን አረጋገጠልኝ።

በሀጫሉ ላይ የሚደረገው ዛቻ እና ትንኮሳ በዚህ ብቻ አልቆመም። ከአካላዊ ትንኮሳ በተጨማሪ የስም ማጥፋት ዘመቻ በተለያዩ ሚዲያዎች ተከፈተበት። ለሚካሄድበት የስም ማጥፋት ፕሮፓጋንዳ መልስ ለመስጠት ቃለ-መጠይቅ ሊሰጥ እንደሆነ ከOMN ጋዜጠኞች ሰማሁ። ደውዬለት፣ ቤቴ ጋበዝኩትና በዚህ ሰዓት ሚዲያ ላይ ባይታይ እንደሚሻል ነገርኩት። እሱም

ብሰጭት በተሞላበት ድምፅ «ለምን ሁልጊዜ ከሚዲያ ልትከለክለኝ ትፈልጋለህ?› በማለት ወደ ሚኒሶታ በመጣ ጊዜ የተከሰተን አንድ ጉዳይ አስታወሰኝ።

በ2016 አንድ ቀን የOMN ጋዜጠኛ ሀጫሉን በሚዲያው ማቅረብ እንደሚፈልግ ሲነገረኝ ተቃወምኩት። ጊዜው በሀገር ውሰጥ አመጽ በእጅጉ የተባባሰበት እና መንግሥትም የከፋ የኃይል እርምጃዎችን የሚወሰደበት እንዲሁም OMN በአሸባሪነት የተከሰሰበት ነበር። ሀጫሉ ደግሞ ወደ ሀገር ቤት ለመግባት ወሰኗል። ሀጫሉ ወደ ሚዲያ ከቀረበ ያለ ምንም መሸፋፈን

የልቡን እንደሚናገር አውቃለሁ። በተለይ ሕዝቡ እንደዛ እየተጨፈጨፈ ባለበት ሁኔታ በሰሜት ተሞልቶ መናገሩ ሰለማይቀር፣ በዚያ መልኩ ተናግሮ ወደ ሀገር ቤት ከገባ ይገሉታል በማለት OMN ላይ መቅረቡን ፈራሁለት። ሊያናግረው ያሰበው ጋዜጠኛ ግን ያቀረብኩትን ምክንያት ሳይገልጽለት ለክፋት እንደከለከልኩት አድርጎ ነገረው። በዚህ ምክንያት ሀጫሉ ለተወሰነ ጊዜ ከተቀየመኝ በኋላ ተገናኝተን ሲጠይቀኝ ምክንያቴን ተረዳ።

አሁን OMN ላይ መናገር ስለመፈለጉ ስንወያይ አካላዊ ጉዳት ሳይሆን የፖለቲካ ውዝግቡን ያባብስበታል ብዬ ስለፈራሁ እንዳይናገር ላሳምነው ሞከርኩ። እሱግን የስም ማጥፋት ዘመቻው እንዳበሳጨው፣ በተጨማሪም በፖለቲካ ፓርቲዎች በተለይም በብልጽግና እና በኦነግ መካከል የሚደረገው አተካሮ ስላሳሰብው ሐሳቡን መግለጽ እንደሚፈልግ ነገረኝ። የሚካሄድበትን የስም ማጥፋት ዘመቻ አስፈላጊ ከሆነ ተናግሬ እንደምከላከልለት ቃል ገባሁለት። አስቀድሜ ሥራ መጀመሬን ጠቁሜ በወቅቱ የተከሰተ አንድ ነገር አወጋሁት።

አንዲት የአማርኛ ሬዲዮ ጋዜጠኛ ደውላልኝ «የመሬት ዝርፊያ ለማስቆም ታግላችሁ እናንተም ዘረፋ ውሰጥ ገባችሁ አለችኝ። «ማነው የዘረፈው?» ብዬ ስጠይቃት፡ «ከአንተ ጋር ሲታገሉ የነበሩትን አለችኝ። «ስማቸውን ጥቀሺ, ብዬ ንግግሬን ሳልጨርሰ ከአፌ ላይ ነጥቃ «ሀጫሉ እና ፈይሳ ሌሊሳ› አለች። ምን ያህል መሬት እንደወሰዱ ስጠይቃት እያንዳንዳቸው አምስት ሺ ካሬ እንደሆነ ነገረችኝ።

«ሲደመር ሀጫሉ እና ፈይሳ የፊንፊኔን መሬት ዘረፉ አይባልም፡ ከአባታቸው የተዘረፈውን ንብረት አስመለሱ ነው እንጂ። ሀጫሉ የአያቱን የቱፋ ሙናን መሬት ከወሰደ ዘረፈ ሳይሆን የተዘረፈውን ርስት አስመለሰ መባል አለበት። ጥፋታቸው አምሰት ሺ ካሬ ብቻ መውሰዳቸው ነው፡ የሚገባቸው አምሰት ሺ ሔክታር ነው› አልኳት።

ጋዜጠኛዋም ከእኔ ያልጠበቀችውን መልስ በመስማቷ ተደናግጣ «እውነት አሁን ያልከውን እንዳስተላልፍ ትፈልጋለህ?» ስትል ጠየቀች። «አንድም ቃል ሳትቆርጪ» አልኳት ፈርጠም ብዩ። እሷ ግን ሙሉ በሙሉ ሳታስተላልፈው ቀረች። አነጋገሬ የልጆቹን መሬት መውሰድ መደገፌ ሳይሆን፣ እነዚህን በትግሉ ወቅት ትልቅ ሚና የነበራቸውን ወጣቶች ቅስም ለመሰበር ሲደረግ የነበረውን የስም ማጥፈታ ዘመቻ ለማጣጣል አስቤ ነበር።

ከጋዜጠኛዋ ጋር ሰለነበረኝ የቃላት ልውውጥ ለሀጫሉ ነገርኩትና «እንዲህ ዓይነት ሁነኛ ጠበቃ እያለህ አንተ እራስህን ለመከላከል መናገር አያስፈልግህም› አልኩት። ሀጫሉም እየቀለደ «ካልክ ይሁን፡ ወያኔን ካሸነፈ ምላስ ጋር ተሟግቼ አልችልም። አንተ እንደሆንክ ነጬን ጥቁር ነው ብለህ ሰው ታሳምናለህ› አለኝ።

ብዙም ሳይቆይ ወደ OMN ቢሮ ሄደ ቃለ-ምልልሰ እንደሰጠ ሰማሁ። ቃለ ምልልሱን ከሰጠ በኋላ

እኔ ጋር መጥቶ መታገስ አቅቶት እንደተናገረ ነገረኝ። ብቻችንን ለሰዓታት አወራን። ኦሮሞ የትላንቱን አገዛዝ በአንድነት ገርሰሶ ዛሬ ግን ተከፋፍሎ እርስ በእርስ መዋጋቱ እንዳስከፋው እና በኦሮሞ አመራር በጣም ማዘኑን አወጋኝ። «እንኳንም በሕይወት ያለን ሰው አወድሽ አልዘፈንኩ። በሕይወት ያለ ሰው አንድ ቀን ያኮራህና በሌላ ቀን ደግሞ ያሳፍርሃል። የሞተ ሰው ግን የሠራውን ጥሩ ታሪክ ለማጉደፍ ዕድል ስለሌለው አሱን ብታሞግሰውም ሪስክ የለውም»

አለኝ። ንዴቱን ለማስረሳት በማሰብ «በቃ አታስብ የምትዘፍንለት ሰው አታጣም፣ በቅርቡ እኔን መግደላቸው ስለማይቀር ትዘፍንልኛለህ›› ብዬ ቀለድኩ።

«አንተ የምትሞት ቢሆን ኖሮ ገና ድሮ ነበር የምትሞተው። እንደ ድመት ሰባት ነብስ ነው ያለህ። ቶሎ አትሞትም፤ እንዲያውም ከማርጀት ብዛት ትጃጃለህ፣ እኔ ነኝ ቀድሜህ የምሞተው ሲለኝ፤ «እኔ ቀድሜህ እሞታለሁ፣ ሌላው ባይገድለኝ እንኳን ይህ ውፍረት ልቤን ሳያፈነዳው አይቀርም› አልኩት። እንዲህ እየተቀላለድን እያለ ቁጭ ብላ ቡና ስታፈላልን የነበረችው አህቴ ምንድነው እንዲህ በሞት ላይ ማሚረት?›› ብላ ሰትቆጣን፣ በቁጣዋ ተደናግጠን ወሬያችንን ቀየርን።
ሀጫሉ ሊሄድ ሲነሳ የእሱ ደኅንነት ስላሳሰበኝ ሁለት ጠባቂዎቼን እንዲወስድ ተማጸንኩት። የእኔ ሥጋት እሱ ይገደላል የሚል አልነበረም። ይልቁንም መንገድ ላይ አዋክበው ስሜት ውስጥ በማስገባት ሌላ ሰው ላይ ጉዳት እንዲደርስ አድርገው ለእስር ይዳርጉታል የሚል ነበር። ጠባቂዎቼን እንዲወስድ የፈለኩትም ለዚሀ ነው። ጠባቂዎቹ በአጥቂዎቹ ላይ እርምጃ ቢወስዱም ሥራቸው ስለሆነ ነገሩ የከፋ አይሆንም። እሱ ግን ቴኳንዶ የተማረ ወንድሙ አብሮት ስላለ ችግር የለውም በማለት እምቢ አለ። ሀጫሉን ከዚያ ቀን በኃላ በአካል አላገኘሁትም። ከጥቂት ቀናት በኋላ በአሳዛኝ ሁኔታ ገደሉት።

በተገደለበት ምሽት አንድ የመንግሥት ባለሥልጣን ደውሎ «ሀጫሉ ተጎድቷል አሉ፤ ሰምተሃል?» ሲለኝ በጣም ደነገጥኩ። በጭንቅላቴ በረዶ የተደፋ ይመስል መላ ሰውነቴ ቅዝቅዝ አለ። በዚያ ድንጋጤ ውስጥ ሆኘ «ምን ሆነ አልከኝ› ብዬ ስጠይቀው «ሰው ነው የመታው አሉ አልታወቀም። አንዲት ልጅ ናት ደውላ ለኋደኛው የነገረችው፡ የት አንዳለም አልታወቀም።

እስቲ ቄሮዎች እንዲፈልጉት በፌሰቡክ ላይ ለጥፍ›› አለኝ። የባለሥልጣኑ ንግግር የበለጠ ረበሸኝ። «የተመታ ሰው በፖሊሽ አንጂ በቄሮ እንዴት ይፈለጋል? በያዘው ተንቀሳቃሽ ስልክ በጂፒኤስ በሰከንዶች ውስጥ ማግኘት እየተቻለ ለምን ለቄሮ እናሳውቃለን?›› አልኩት።

ሀጫሉ መሞቱ ከተረጋገጠና አስከሬኑ ወደ ሆስፒታል ከተወሰደ በኋላ ሌላ የመንግሥት ባለሥልጣን በድጋሜ ደውሉ «ሀጫሉ የተገደለው በሸኔ እና በወያኔ ነው አለኝ። እኔም «በዚሀ አጭር ጊዜ ማን እንደገደለው እንዴት ማወቅ ተቻለ? አጥቂው ተለይቶ ታስሯል እንዴ?» ስለው መልስ ሳይሰጠኝ ዝም አለ። «ጥቃት አድራሹ ቢያዝ እንኳን ከጀርባው ያለውን የፖለቲካ ቡድን ለመለየት ጊዜ ይወስዳል። ፖሊስ ትክክለኛ ምርመራ ያድርግ። ለአሁኑ ያለ ማስረጃ ወደ የትኛውም ቡድን ጣት መቀሰር ከፍተኛ ግጭት ውስጥ ስለሚያስገባን በግምት ከማውራት መቆጠብ ያሰፈልጋል›» አልኩት።

ከባለሥልጣኑ የሰማሁትን ወዲያው በፌሰቡክ ተለጥፎ አየሁት። የመንግሥት ባለሥልጣናት ገና ሬሳው እንኳን ሳይመረመር ያለምንም ማሰረጃ ግድያውን በፖለቲካ ቡድኖች ላይ ለማላከክ መሞከራቸው፣ በኦሮሞ መካከል እንዲሁም ከሌሎች ብሔር ብሔረሰቦች ጋር ግጭት ሊፈጥር

እንደሚችል ሠጋሁ። የተወሰኑ የቄሮ አስተባባሪዎች እና ውጭ ሀገር ያሉ ምሁራንን አነጋግሬ ሕዝቡን በኀሳ እና በብሔር የማጣላት ሴራ ሊኖር ስለሚችል በንቃት ተከታትለን ማክሸፍ እንዳለብን ተስማማን።

ሌላ ባለሥልጣን በእኩለ ሌሊት ደውሎ መንግሥት ለሀጫሉ መንግሥታዊ የቀብር ሥነ-ሥርዓት (state Funeral ) ለማድረግ ኮሚቴ እንዳቋቋመ እና ፊንፊኔ እንዲቀብር መወሰኑን ነገረኝ። ገና በማለዳ ቴሌቪዥን ስከፍት ግን ባለሥልጣኑ ከነገረኝ በተቃራኒ እየተፈጸመ ነበር። አስከሬኑ ከሆስፒታል ወጥቶ ሕዝቡ ወደ አምቦ ይዞት ሲሄድ ተመለከትኩ። መንግሥት የጀግና አሸኛኘት አደርጋለሁ ብሎ አሁን አስከሬኑን እንዴት ለሕዝብ አሳልፎ ሰጠ? በተጨማሪም ስለ ግድያው ሁኔታ የአስከሬን ምርመራ (autopsy) በእነዚህ ጥቂት ሰዓታት ውስጥ ተጠናቆ ለቀብር እንዴት ተዘጋጀ? የሚሉ ጥያቄዎች ጭንቅላቴ ውስጥ ተመላለሱ። ስልኬን አንስቼ ማታ መንግሥታዊ የቀብር ሥነ-ሥርዓት እንደሚደርግ ለነገረኝ ባለሥልጣን ሰደውል፡ መንግሥት ሐሳቡን ቀይሮ አምቦ እንዲቀበር መወሰኑን ነገረኝ። ምክንያቱን ሰጠይቀው በአጭሩ «አላውቅም» አለ፤ በተበሳጨ ድምፅ። አሰከሬኑን አጅበው ወደ አምቦ የሚሄዱ የመንግሥት ባለሥልጣናት አነማን እንደሆኑ ሰጠይቅ «ማንም የለም፣ ሕዝቡ ነው እየወሰደው ያለው» አለኝ።

የኦሮሞ የዓይን ብሌን የሆነ፣ ለሕዝብ እና ለሀገር ትልቅ አስተዋጽዖ ያደረገ እንደ ሀጫሉ ያለ ሰው አስከሬኑ እንዲሁ ይጣላል? ብዬ በጣም ተናደድኩ፡ ውስጤ ተቃጠለ። ማታ ከጠባቂዎቹ ጋር ስናወራ አስከሬኑ ወዳለበት ሆሰፒታልም ሆነ ወደ ቀብር ሥን-ሥርዓት መሄድ አደጋ አለው ብለው ስለተማጸኑኝ ላለመሄድ ተስማምቼ ነበር። ከባለሥልጣኑ የሰማሁት ነገር ግን አሳበደኝ፤ ደሜን አፈላው፡ "የሞትኩት እኔ ብሆን እና አስከረኔ ተመሳሳይ ሁኔታ ቢያጋጥመው ሀጫሉ ቤቱ ተቀምጦ ይመለከት ነበር?" ብዬ ራሴን ጠየኩ።

አእምሮዬ የሰጠኝ መልስ ሀጫሉ ለእኔ ይቅርና ዛሬ ቀብሩን ያሳነሱ የመንግሥት ባለሥልጣናት ቢሞቱ፣ ታሞ አልጋ ላይ ቢውል እንኳን አይቀርም፡ በቃሬዛም ቢሆን ታዝሎ ሁላችንንም በመጥራት አነሳስቶ ይወስደናል የሚል ነበር። ወዲያው በቀብር ሥነ-ሥርአቱ ላይ መገኘት አለብኝ ብዬ ወሰንኩ። ጠባቂዎቹ የሚያውቁት ማታ አውርተን እንደተስማማነው ወደ ቀብር እንደማልሄድ ነው። ለመሄድ እንደወሰንኩ ሲሰሙ በድንጋጤ መጥተው በሩን ዘጉብኝ። ከተቀመጥኩበት እንዳልነሳም ከለከሉኝ። የቤት እቃዎችን ሰባብሬ ተነስቼ በጉልበት ወጣሁ። እንደወጣሁም ባለሀብቶች እና ሽማግሌዎችን ግቢ ውሰጥ አየሁ። ከእኔ ጋር ሄደው ጉዳት እንዳይደርስባቸው በማሰብ «ቤቴ ውስጥ ባለው ቢሮዬ ላናግራችሁ እፈልጋለሁ›› ብዩ ካስገባኋቸው በኋላ በጀርባ በመውጣት መኪና ውሰጥ ገብቼ አመለጥኳቸው።

ለፕሮፌሰር መረራ ጉዲና፣ አቶ በቀለ ገርባ እና ለሌሎች ደውዬ እንሂድ አልኳቸው። ሁሉም ተስማምተው ፕሮፌሰር መረራ ግን እንዳልሄድ ሲለምነኝ ቢያንስ ሸኝቼ እመለሳለሁ ብዬ አሳመንኩት። እኛ ስንደርሰ አሰከሬኑ ከአንድ ሰዓት በፊት ቢወጣም ከሆስፒታሉ አንድ ኪሎ ሜትርም ፈቅ አላለም። በጣም ብዙ ሕዝብ ስለነበር የመኪና መንገዱ ከመጨናነቁም በላይ ፊንፊኔ እንጂ አምቦ መቀበር የለበትም በሚል ተቃውሞ የአስከሬን መኪናው እንዳይንቀሳቀሰ አግደውታል። ከእኔ ጋር ያሉ ሰዎች ብዙ መኪኖች ይዘው ስለነበር፡ አስከሬኑን አጅበው ከነበሩት ውሰጥ ድምጻዊ ገላና ጋሮምሰ መጥቶ አስከሬኑ ሳይበላሽ በፍጥነት ወደ ቀብር ቦታ እንዲደርሰ መንገድ በማስከፈት እንድንረዳቸው ጠየቁን። አስከሬኑ ማቀዝቀዣ ባለው ተሽከርካሪ

መጓጓዝ ሲኖርበት በአንድ የግል መኪና ውስጥ እንደተጫነ እና ፀሐዩ እየበረታ ሲሄድ ሊበላሽ

እንደሚችል ነገረን። ያሉንን መኪኖች በሁለት ከፍለን አስከሬን የጫነውን መኪና ከፊት እና ከኋላ አጅበን መንቀሳቀስ ጀመርን።

ሕዝቡ ግን የአስከሬን መኪናው ከከተማ እንዳይወጣ ይቃወም ስለነበረ በፈለግነው ፍጥነት ሊያስኬዱን አልቻሉም። መንገድ ሲዘጉብን ከመኪና ወርደን እየለመን መጓዝ ቀጠልን። ከከተማ በራቅን ቁጥር እንቅስቃሴው የበለጠ አስቸጋሪ ሆነ። ከቡራዩ አለፍ ስንል ከአምቦ አቅጣጫ የሚመጣ ሕዝብ በከባድ መኪና (ሲኖትራክ) መንገድ ይዘጋብን ጀመር። አንድ ሰው ቢላ አውጥቶ አንገቱ ላይ በማሳረፍ «ራሴን ከምገድል አስከሬኑን መልሱት አለኝ። ተለማምጬ አረጋጋሁት። አንድ መስቀለኛ መንገድ ላይ ስንደርሰ ሲኖትራክ ተደርድሮ መንገድ በመዝጋቱ ማለፍ እንደማንችል ስናይ ገላና ለኦሮሚያ ፕሬዘዳንት ሽመልሰ አብዲሳ ደውሎ ችግራችንን ነገረው። መመለስም «አላስኬድ ካላችሁ ወደ ከተማ ተመለሱና ፖሊሰ ይላክላችኋል አለው።

ወደኋላ ተመልሰን ቡራዩ ውስጥ አንድ ትንሽ ፓሊስ ጣቢያ ጋር ቆመን ብንጠብቅም ይመጣላችኋል የተባለው ፖሊስ የውኃ ሽታ ሆነ። እዚያ በቆየን ቁጥር የሰዎች ቁጥር እየጨመረ ከባድ አደጋ የመከሰት ዕድሉ እየሰፋ መምጣቱን አየን። ቦታው መሀል ከተማ በመሆኑ ግጭት ይፈጠራል ብለን ፈራን። ይህን በመረዳት ለታከለ ኡማ (በወቅቱ የአዲስ አበባ ከንቲባ) ደውዬ ምን ማድረግ እንዳለብኝ ጠየቅኩት። ከሽመልስ ጋር እንደተነጋገሩ እና አስከሬኑን ወደ ፊንፊኔ እንድንመልሰው ነገረን።

ወደ ፊንፊኔ ከተመለስን አሰከሬኑን ወዴት መውሰድ አለብን በሚለው ላይ ስንወያይ ሦስት አማራጮች ቀረቡ፤ የከንቲባ ቢሮ፣ ሰታዲየም እና የኦሮሞ ባሕል ማዕከል። የኦሮሞ ባሕል ማዕከል የሚጠበቀው በኦሮሚያ ፖሊስ በመሆኑ ችግሮችን ለመቀነስ የተሻለ እንደሆነ ተሰማማን። ከቡራዩ ተነስተን በፍጥነት መንገድ እያስከፈትን፣ ከአግረኛው ሕዝብ አምልጠን ወደ ኦሮሞ ባሕል ማዕከል አመራን። በዚህ ጊዜ የደረሰንበትን ቦታ ሁሉ ለመንግሥት ባለሥልጣናት በስልክ እያሳወቅን ነበር። የኦሮሞ ባሕል ማዕከል ግቢ በር ስንደርሰ ፖሊሶች እንዳንገባ ከለከሉን። እየመጣን መሆኑን የመንግሥት ባለሥልጣናቱ ስላልነገሯቸው፤ ከጠባቂዎቻችን ጋር ተፋጠጡ። ለታከለ ደወልኩለትና ስልኩን በሩ ላይ ለነበረው የፖሊስ አዛዥ ሰጥቼ ካናገረው በኋላ አስገቡን።

ብዙም ሳይቆይ ታከለ መጣ፡ኮሚሽነር ደቻሳ ቢቲማም ተከተለው። «ሕዝቡ መንገዱን ሰለዘጋው እና አስከሬኑን ዛሬ ወደ አምቦ መውሰድ ስለማይቻል፣ ለዛሬ እዚሁ አድሮ ነገ ወይም ከነገ ወዲያ የሽኝት ፕሮግራም አዘጋጅታችሁ ቢቀበር ይሻላል» ስለው ታከለ መስማማቱን ገለፀ። የፀሐዩ ግለት አስከሬኑን እየጎዳው ስለሆነ ማቀዝቀዣ ያለው መኪና እንዲያመጡም ተግባባን። በመሀል ለታከለ የሆነ ስልክ ተደውሎለት ካናገረ በኃላ ፊቱ በድንጋጤ ክፉኛ ሲለወጥ አየሁ። «እና በመኪኖዬ አብረን ሄደን ፍሪጅ እናምጣ›› አለኝ። ለእኔም የሆነ ባለሥልጣን ነገሮች ወዴት እያመሩ እንደሆነ የሚጠቁም መልዕክት ልኮልኝ ስለነበር ታከለን ያስደነገጠው ጉዳይ ገባኝ። እኔን ከዚያ ግቢ አስወጥቶ ሕይወቴን ለማዳን አንዳሰበ ብረዳም አብረው መውጣቱ እኔንም እሱንም ለአደጋ እንደሚያጋልጥ ስለጠረጠርኩ «አይ አንተ ራስህ ሂድና አምጣ›› አልኩት።

ታከለ በወጣ በደቂቃዎች ውስጥ የሀገር መከላከያ ሠራዊት ወታደሮች መጥተው አስከሬኑን አምጡ አሉን። «ይኸው ውሰዱ› አልኳቸው። ሲደርሱ መሬት ላይ ተቀምጬ ነበር። ሲላኩ

የጠበቁት ሁኔታና በዓይናቸው ያዩት ነገር የተለያየ ሆኖ ስላገኙት ግር እንዳላቸው ከፊታቸው ገጽታ ይነበባል።

አስከሬኑን አንሰጥም የምንል መሰሏቸዋል። እዚያ የነበረው አዛዥ በያዘው ሬዲዮ «እንደተባለው አይደለም» ብሎ በአማርኛ ሲያወራ ሰማሁ። አዛዡን በእጄ ጠራሁትና «ምነው ችግር አለ እንዴ?» ብዬ ስጠይቀው፡ «ያገታችኋቸው የመንግሥት ባለሥልጣናት የት ናቸው?» አለኝ። «ያገትነው ባለሥልጣን የለም።

ከንቲባ ታከለ እዚህ ነበር፡ እሱም አሁን ወጣ›› አልኩት። አዛዡ አሁንም ከፊቱ ላይ ግራ መጋባት ይታያል። በሬዲዮ ተናግሮ ተመለሰ። ይህ በእንዲህ እንዳለ ተጨማሪ የኦሮሚያ ፖሊስ ልዩ ኃይል መጥቶ የመከላከያ ወታደሮችን ስለከበበ የከፋ ውጥረት ተፈጠረ።

ሦስት የታጠቁ ኃይሎች ተፋጠጡ፣ የሀገር መከላከያ ሰራዊት፣ የኦሮሚያ ፖሊስ እና የእኔ ጠባቂዎች። ሦስቱም መሣሪያቸውን ባቀባበሉበት፡ ድንገት ሊታኮሱ ስለሚችሉ፣ የሠራዊቱን አዛዥ ጠርቼ፣ «ይህ ፍጥጫ አስፈሪ ነው። ድንገት አንድ ጥይት ከተተኮሰ ሁላችንም ማለቃችን ነው። ስለዚህ አንተ ወታደሮችህን አስወጣ።

እኔም የሚጠብቁኝን ልጆች ትጥቅ አስፈታለሁ። ከዚያም የኦሮሚያ ፖሊስ ሁኔታውን እንዲቆጣጠር እናደርጋለን›› አልኩት። እሱም ተስማምቶ ሄዶ በሬዲዮ ከተነጋገረ በኋላ ኃይሉን ከአኛ አራቀ። የኦሮሚያ ፖሊስም ከቦ ይጠብቀን ገባ።

ቀጥሎ አንድ የኦሮሚያ ፖሊስ አዛዥ መጥቶ «በቁጥጥር ሥር አውሏቸው ተብለናል› አለ። «ምንም ችግር የለውም፣ ወዲህ ተጠጋና እንነጋገር› ብዬው ፈራ ተባ እያለ ወደ መኪና ይዤው ገባሁ። «አታስብ የሚጠብቁኝን ልጆች አስፈታለሁ፤ አንተ ተረጋግተሀ ፖሊሶቹን አረጋጋ› አልኩት። ወዲያው የጥበቃዎቹ አዛዥ የሆነውን ጌቱ ተረፈን ጠርቼ የታጠቀውን መሣሪያ ለፖሊስ አዛዡ እንዲያስረክብ አደረኩ። እሱም በስሜት እያለቀሰ ሰጠው። «የሌሎቹንም ልጆች መሣሪያ ተቀብለህ ለፖሊስ ስጥ› አልኩት። ከዚያ እኔ እና በቀለ ከፖሊስ አዛዡ ጋር በእኔ መኪና መሄድ ስንጀምር ሃምዛ በረና «ከጀዋር እና ከበቀለ አልነጠልም›› በማለት ፖሊሶቹን ለምኖ ተቀላቀለንና እዚያው ግቢ ውስጥ ወዳለው የኦዴፓ ቢሮ አመራን። እዚያም በረንዳ ላይ ከሦስት ሰዓት በላይ ቆየን። መታሰራችን ግልጽ ስለነበር በቀለ እስር ቤት ውስጥ ምን እንደሚጠብቀን ከልምዱ በመነሳት እየነገረን የሥነ ልቦና ዝግጅት እንድናደርግ ማስረዳት ጀመረ።

አመሻሹ ላይ የፌደራል ፖሊሶች ሊውስዱን መጡ። የኦሮሚያ ፖሊሶች እኛን ላለማስረከብ ቢያንገራግሩም አረጋግተናቸው ብረት ለበሰ በሆነው የፌደራል ፖሊሰ መኪና ውስጥ ገባን።

# 10.2. እስር

ከኦሮሞ ባሕል ማዕከል ተወስደን ሦስተኛ ተብሎ በሚጠራውና ከቀድሞው ማዕከላዊ አጠገብ ወደሚገኘው የአዲስ አበባ ፖሊስ ኮሚሽን አስር ቤት ስንደርሰ የመሥሪያ ቤቱ ሠራተኞች በብዛት መግቢያው ላይ ጠበቁን። ብዙዎቹ ፊት ላይ ደሰታ ይነበባል፣ ያዘኑም ነበሩ። ወደ ውሰጥ ገብተን ከተመዘገብን በኋላ የጤና ምርመራ ለማድረግ አንድ ቢሮ ስገባ ዕድሜው ጠና ያለ ሐኪም እንዳየኝ ዓይኑ እንባ ስላቀረረ ፊቱን አዙሮ ጠረገ። ጀርባውን መታ አድርጌ «አይዞህ!› አልኩት። «አንተን በዓይኔ ለማየት ትልቅ ምኞት ነበረኝ። በእንዲህ ዓይነት ሁኔታ አይሃለሁ ብዬ ግን አስቤ አላውቅም ነበር›› አለ። «አይዞህ ይሄም የትግሉ አካል ነው ብዬ ተሰናበትኩት።

እኔን እና በቀለን ወደ አንድ ክፍል አስገብተው፣ ትንሽዬ ፍራሽ እና ብርድልብስ ሰጥተው ከውጪ ከረቸሙብን። በጣም ደክሞኝ ስለነበር ወዲያው እንቅልፍ ይዞኝ ጭልጥ አለ። እኩለ ሌሊት ሲከፍቱ የበሩ መቀርቀሪያ ጩኸት ቀሰቀሰኝ። በሩም መቀርቀሪያውም ብረት ሰለነበር ጩኸቱ ይረብሻል። ከአስር ቤት ኑሮ አንዱ አሠቃቂ ነገር በእንቅልፍ ልብ እያለህ ድንገት በር ሲከፈት የሚፈጠረው መረበሽ እንደሆነ የታሰረ ሁሉ የሚስማማበት ጉዳይ ይመስለኛል። በሩን ከፍተው ሸንት ቤት ካደረሱን በኋላ ስንመለሰ እኔና በቀለን ለያይተው የተለያየ ክፍል ውሰጥ አስገቡን። አሁንም ወዲያው እንቅልፍ ይዞኝ ሄደና ጠዋት ለሽንት ሲቀሰቅሱኝ ነቃሁ።

የነበርኩበት ክፍል ካሜራ እንዳለው ስላየሁ፣ መሥራቱን ለማረጋገጥ ፈለኩና ግድግዳው ላይ በጠጠር የሆነ ነገር ጻፍኩ። ፖሊሶች መጥተው እንዳልጽፍ ነገሩኝ። ይሄም ካሜራው እንደሚሠራ አረጋገጠልኝ። ቀጥሎ ድምጹ ይሠራ እንደሆነ ለማየት ፊቴን ከካሜራው አዙሬ ፖሊስ ጠራሁ። ማንም አልመጣም። ወደ ካሜራው ዞሬ አጄን ሰውለበልብ ግን መጡ። በዚህም ድምጹ እንደሚሠራ ማረጋገጥ ቻልኩ።

ለቁርስ ዳቦ እና ሻይ ሲያቀርቡልኝ አልበላም አልኳቸው። ሌሊት ሳይለዩን በፊት፣ በቀለ «በመርዝ ሊጎዱህ ስለሚችሉ የሚሰጡህን ምግብ እንዳትበላ፣ ዉኃም እንዳትጠጣ» ብሎ መክሮኝ ስለነበር፡ ለደህንነቴ ስለምሠጋ መንግሥት የሚያቀርበውን ምግብ እንደማልጠቀም ነገርኳቸው። ፖሊሶቹም ሊያሳምኑኝ ሞክረው ሲያቅታቸው አለቆቻቸውን እንደሚያማክሩ ነግረውኝ ሄዱ።

ከሰዓት ቤተሰብ አናግረው ምግብ ከቤት አስመጡልኝ። ቤተሰቤን ውጪ አስቀርተው ምግቡን ተቀብለው ሲያመጡ «ያመጣውን ሰው ሳላይ ከቤት መምጣቱን ማረጋገጥ ስለማልችል አልበላም» አልኳቸው። ይህን ያደረኩት ለደህንነቴ ካለኝ ሥጋት ብቻ ሳይሆን ቤተሰቤ በሕይወት መኖሬን በዓይናቸው አይተው እንዲረጋጉ ነበር። ፖሊሶቹም ቤተሰቦቼን አስገብተው ምግቡን እንዲያቀብሉን ፈቀዱ፡ እንዳላወራቸው በማሰብ ርቀው እንዲቆሙ አደረጉ።

በተያዝን በሦስተኛው ቀን ፍርድ ቤት አቀረቡን። መርማሪ ፖሊሶቹ «የሀጫሉን አስከሬን በኃይል መመለስ እና በአንድ ፖሊስ ሞት» እንደሚጠረጥሩኝ ለዳኛው አስረዱ። በኦሮሞ

ባሕል ማዕከል ውስጥ ፖሊስ መሞቱን ለመጀመሪያ ጊዜ መስማቴ ነበር። የሀጫሉን አስከሬን ከመንግሥት ባለሥልጣናት ተነጋግሬ መመለሴ እውነት ቢሆንም ስለሞተው ፖሊስ ግን የማውቀው ነገር እንደሌለ ለዳኛው ነገርኩት። ከፍርድ ቤት ከተመለስኩ በኋላ ጠባቂዎቼን በበሩ ቀዳዳ ስጠይቃቸው አንድ የኦሮሚያ ፖሊስ አባል ከፖሊሶች መሀል በተተኮሰ ጥይት መሞቱን አረጋገጡልኝ። ፍርድ ቤቱ ፖሊስ ለምርመራ ያስፈልገኛል ብሎ የጠየቀውን የአሥራ አራት ቀን ቀጠሮ ከፈቀደ በኋላ ቤቴን ለመፈተሽ ይዘውን ሄዱ። ያጀቡኝ ቀይ ቦኔት ለባሾች ኮማንዶዎች በብዙ ብረት ለበሽ መኪኖች ተጭነው መትረየስ እና ሰናይፐር ደግነው ስለነበር፣ አንድ እስረኛ ይዘው በከተማ ውስጥ የሚጓዙ ሳይሆን ወደ ጦር ሜዳ የሚያቀኑ ይመስላሉ።

ቤቴ ስንደርስ እያንዳንዱን ክፍል ለሰዓታት አመሰቃቅለው ፈትሸው ያገኙትን ወረቀት፣ ኮምፒዩተር እና ስልክ ሰበሰቡ። «ዶላሩ የት ነው ያለው?» ሲሉኝ፡ «የለኝም፡ ካገኛችሁ ፈልጉ›› ብዬ አፌዝኩባቸው። ከአሜሪካ መጥተው እኔ ጋር ከከረሙ ልጆች ኪስ ውስጥ ሀያ ዶለር ($20) ብቻ አገኙ። ልንወጣ ስንል ፓሊሶች መኝታ ክፍሌ የነበረ አንድ ካዝና ቤተሰብ በጥርጣሬ ከደበቀበት ማገዶ ውስጥ አገኙ። ፖሊሶች እና ሰላዮች አንድ ትልቅ ነገር ያገኙ መስሏቸው ተደሰቱ። ምንም እንደሌለበት ባውቅም የደነገጥኩ መሰልኩ። ቁልፉ ስላልተገኘ ጭነው ወደ ፖሊስ ጣቢያ ሄድን።

በማግስቱ ብዙ ሚዲያዎችን እና ምስክሮችን ወደ ፓሊስ ጣቢያው ጠርተው ካዝና ሰባሪም አምጥተው ወደ መስበሩ ገቡ። ሰውዬው ካዝናውን ለመስበር መቀጥቀጥ ሲጀምር ወደኋላ ሳፈገፍግ ሁሉም ሰው በድንጋጤ ወደኃላ "። እኔ ስስቅ እየቀለድኩ እንደሆነ አውቀው ቆሙ። ከበርካታ ሙከራዎች በኋላ ካዝናው ተሰብሮ ሲከፈት አነስተኛ መጠን ያላቸው ወረቀቶች አና ትንሽ የኢትዮጵያ ብር ውስጡ ተገኘ። እዚያ የነበረው መርማሪ ሰላላመነ ምናልባት ድብቅ አካል ካለ ፈልጉ ብሎ ካዝናውን ብዙ ቦታ ቢሰባብሩትም ምንም ነገር አላገኙም።

ለተጨማሪ ሁለት ቀናት ቤት እያመላለሱኝ ፈተሹ። ጣሪያው ላይ ያለውን አንቴና ሲያዩ “ሳተላይቱ ይሄ ነው?" ብለው ጠየቁኝ።

ዝም ስላልኩኝ የካድኩ መስሏቸው አንቴናውን ነቅለው ማምሻውን የጀዋር ቤት ሳተላይት ተያዘ ብለው በቴሌቪዥን እንደዘገቡ ሰማሁ። ያገኙት መሣሪያ ግን የኢንተርኔት ማከፋፈያ (WiFi amplifier) እንጂ ሳተላይት አልነበረም። ቤቱ ባለ አራት ወለል ፎቅ ስለነበረ የኢንተርኔት ሰርጭት አቅምን በመጨመር ሁሉንም ክፍሎች እንዲያዳርሱ ያሰገባነው ነው።

የአዲሰ አበባ ፖሊሰ ጣቢያ በነበርንበት ወቅት ብዙ ሰዎች ተይዘው መምጣት ጀመሩ። ከፖለቲከኞኛች እስክንድር ነጋ፣ ይልቃል ጌትነት እና ሌሎችም ተይዘው መጡ። እስክንድርን ያመጡት እኛ ታስረን ከሁለት ወይም ሦስት ቀን በኋላ ነበር። አንድ የደህንነት መሥሪያ ቤት ሹም ወደ ምርመራ ክፍል አስጠርቶን ”ማን ታስሮ ማን ይቀራል” በማለት እስክንድርን በእኔ መታሰር የእሱ ወገኖች በመደሰታቸው እንዳሰሩት ነገረኝ። «ለአኔ ብላችሁ ከሆነ ያሰራችሁት እባካችሁ አሁኑኑ ፍቱት። እንዲያውም እንደ እስክንድር እና በቀለ ገርባ ያሉ ሰዎች ባለፈው አገዛዝም ለረጅም ዓመታት በእሰር ቤት ስለማቀቁ፣ እኔን አስቀሩና ልቀቋቸው›› በማለት ተማጸንኩት። ሰውዬው ከእኔ ያልጠበቀውን መልስ ሲሰማ ‹‹ያንን አንተ አትወስንም!» ብሎ ወደ መታሰሪያ ክፍሌ እንዲመልሱን አዘዘ።

በንቱ በቀለ ገርባ እና ጫልቱ ታከለን ከእኛ ማዶ ባለ ክፍል ውስጥ አሰሯቸው። ጫልቱ

በኢሕአዴግ ዘመን ለዘጠኝ ዓመታት የፓለቲካ እሰረኛ ነበረች። አሁን ደግሞ ወልዳ አራስ ሳለች ከህጻኗ ነጥለው አመጧት። ታሪኳን ስለማውቅ አንድ ጠዋት የአራስ ጡቷ አስቸግሯት ውጪ ስትዞር አይቻት በጣም አዘንኩ። እሷግን የራሷ ዳግም መታሰር ምንም ሳይመስላት እኔን ለማበረታታት ትሞክር ነበር።

የሀጫሉ ግድያ ላይ ምርመራ የሚካሄደው እዚያው ጣቢያ ስለነበር፡ ከተጠርጣሪዎች እና ከመርማሪዎች መረጃ አገኛለሁ። በንቱ እና ጫልቱም ሀጫሉ ሲገደል አብራ ከነበረችው ሴት ጋር አንድ ክፍል ስለታሰሩ፥ ሳያስወጧት በፊት የነገረቻቸውን መረጃ አካፈሉን። በጥቂት ቀናት ውስጥ ግልጽ የሆነልኝ ነገር ቢኖር፡ ሀጫሉን የገደለውን አካል ፈልጎ ከመያዝ ይልቅ ለመደበቅ እየሞከሩ መሆኑ ነበር። ወንጀሉን በትክክለኛ ምርመራ ከማጋለጥ እና ፍትሕ ከማስፈን ይልቅ ተቃዋሚዎችን በመወንጀል ፖለቲካዊ ጥቅም ማግኘት ላይ አተኮሩ።

ለምሳሌ ከፍተኛ የመንግሥት ባለሥልጣናት በሀጫሉ ግድያ ተጠርጥረው የተያዙ ሰዎች ጋር በአካል በመምጣት፣ ግድያውን ያዘዝነው እኔ (ጀዋር ሙሐመድ) ፣ ኮ/ል ገመቹ አያና እና በቀለ ገርባ እንደሆንን እንዲናገሩ የተለያዩ ጥቅማ ጥቅሞችን ቃል በመግባት ለማሳመን ሞክረዋል። በጥቅማ ጥቅም ለመታለል ፈቃደኛ ያልሆኑት ላይ ከባድ ድብደባ ፈጽመዋል። ከዚያ ባለፈም ወንጀሉን በፍትኃዊነት ለመመርመር የሞከሩ ፖሊሶች ወደ ሌላ ቦታ እንዲዛወሩ ተደርገዋል። ያገኘነው መረጃ እንደሚያሳየው፣ በሀጫሉ አስከሬን ላይ የረባ ምርመራ አልተካሄደም። ከዚህ በመነሳት ሀጫሉን ማን እንደገደለው ባላውቅም፣ ከፍተኛ የመንግሥት አካላት እውነቱ እንዳይወጣ ለመደበቅ ሰፊ ጥረት ሲያደርጉ እንደነበር በሚገባ አውቃለሁ።

ከአንድ ሳምንት በኋላ ከአዲስ አበባ ፖሊስ ኮሚሽን አንስተው ሜክሲኮ ወደሚገኘው የፌደራል ፖሊስ ዋና ምርመራ ቢሮ አዛወሩን። በጊዜው ከእኔ ጋር የነበሩት በቀለ፣ ሃምዛ እና ሸምሰዲን ጠሃ ነበሩ። ቦታው ቀደም ሲል አባይ ፀሐዬ የሚመራው የፌደራል ጉዳዮች ሚኒስቴር መሥሪያ ቤት እንደሆነ፣ ፌደራል ፖሊስ ገና መረከቡን እና እዚያ ለመታሰር የመጀመሪያዎቹ እንደሆንን ተነገረን። በመጀመሪያ ቀን እኔና በቀለን አንድ ክፍል አስገብተውን የነበረ ቢሆንም በማግሰቱ የተለያያ ክፍል ውስጥ ለየብቻ አሰሩን። የታሰርንበት ክፍሎች ከፎቁ ጀርባ ዝቅ ብሎ ምድር ውሰጥ (basement ) ስለነበር በጣም ከመቀዘቅዙ የተነሳ ከቤት የሚመጣልን ምግብ ለቀናት አይበላሽም።

በቀን ሁለቴ ለሽንት እንዲሁም ሠላሳ ደቂቃ (ጠዋት 15፣ ከሰዓት 15) ፀሐይ እንድንሞቅ ያወጡናል። ወቅቱ ክረምት ስለነበረ ፀሐዩዋ ብዙም ስለማትገኝ ግቢው ውሰጥ በእግራችን ዞር ዞር ብለን እንገባለን። ለፀሐይም ሆነ ለሽንት በተለያየ ጊዜ እንጂ በአንድ አያስወጡንም። ይህን ያደረጉት በምንገናኝበት ጊዜ የምንለዋወጠውን መረጃ ለማገድ እና በእኛ ላይ የሥነ ልቦና ጫና ለማሳደር እንዲመቻቸው ይመስላል። ወደኛ ቀርበው በር የሚከፍቱልን እና ሽንት ቤት የሚያደርሱን አፋን ኦሮሞ የማይናገሩ ፖሊሶች ነበሩ። ኦሮሞ የሆኑ ፓሊሶች ታጥቀው ከእኛ ርቀው ዘብ ይጠብቃሉ እንጂ እንዲቀርቡን አይደረግም።

መጀመሪያ አካባቢ ፖሊሶች በጣም እንደሚፈሩን አንዳንዶቹም እንደሚጠሉን ገጽታቸው ይናገራል። ሸንት ቤት ሲወስዱን እንኳን መሳሪያቸውን አቀባብለውና በብዛት አጅበውን ነው። ጠዋት በርሜል ውስጥ ባደረና ቅዝቃዜው አጥንት ድረስ በሚሰማ ውኃ እንታጠባለን።

ታዲያ በር መዝጋት ስለማይፈቀድ ፖሊሶቹ መሣሪያ ይዘው አጠገባችን ይቆማሉ። አንድ ሰሞን

ሴት ፖሊሶች ተመድበው ነበርና አጠገቤ መቆም ግዴታ ሆኖባቸው ወደ መሬት አቀርቅረው ሲቆሙ አሳዝነውን ኋላ ላይ አለቃቸውን አናግሬ እንዳይመድቧቸው አሳመንኩት።

ፖሊሶቹ በሂደት ሲቀርቡን እና እያወቁን ሲመጡ እንደ ቤተሰብ ሆንን። የፖሊሶችን ፍርሀት እና ጥላቻ የመቀየር ምሥጢሩ እነርሱን እና ራስን ማክበር ነው። እስር ቤት ሙሉ ሥልጣን ያለው ፖሊሰ መሆኑን በመገንዘብ ሥልጣናቸውን ማክብር አስፈላጊ ነው። በተለይ ታዋቂ ሰው ከሆንክ ይንቀናል ብለው ስለሚያስቡ፣ ጉልበታቸውን እና የበላይነታቸውን ሊያሳዩህ ይፈልጋሉ። ስለዚህ ለስብዕናቸው እና ለሞያቸው አክብሮት በማሳየት፣ አመለካከታቸውን እንዲያለዝቡ እና በራሰ መተማመናቸውን እንዲያዳብሩ ማድረግ አሰፈላጊ ነው። በራሱ የሚተማመን ፖሊስ ያምንሃል፤ ስታከብረው ያከብርሃል።

ብዙ ሰዎች በተለይ በፖለቲካ ጉዳይ ሲታሰሩ በመንግሥት ድርጊት ተናደው በስሜት ወደ አስር ቤት ስለሚመጡ አጠገባቸው የሚያዩት የመንግሥት አካል ደግሞ ፖሊስ ስለሆነ ቁጣቸውን በፖሊስ ላይ ያወጣሉ። የፖለቲካ እስረኛ ማወቅ ያለበት እስር ቤቱን የሚጠብቁ ፖሊሶች በማሰሩ ውሳኔ ውሰጥ ተሳትፎ እንደሌላቸው ነው። የመንግሥት አካል ስለሆነ ብቻ እንደ ጠላት መመልከት የአስር ቤቱን ቆይታ ለታሳሪውም ሆነ ለፖሊሱ ከባድ ያደርገዋል።

በሌላ በኩል የፖሊስን ሥልጣን ማክበር እንዳለባቸሁ ሁሉ ሰብዓዊ መብቶቻችሁንም ማስከበር አለባችሁ። ከሕግ ወሰን አልፈው በድርጊት ከመጡባችሁ በሥን-ምግባር በታጀበ ጠንካራ አቋም መፋለም ግድ ነው። የማረሚያ ቤቱን አሥተዳደር ሕጎች እና ደንቦች በማጥናት ፖሊሶች መብታችሁን ሲጋፉ በትዕግሥት መታገል ያስፈልጋል። በቀለ ገርባ ከዚያ በፊት በተለያየ ዙር እና ቦታ ታስሮ ስለነበር፡ ፖሊስን እንዴት መያዝ እንዳለብን ትልቅ ትምህርት ስለሰጠን እኛም ምክሩን ተከትለን የፌደራል ፖሊሰ እስር ቤት ቆይታችንን ማለዘብ ችለናል።

የፌደራል ፖሊስ እስር ቤት የተወሰድን ሰሞን ከሰዎች ጋር መገናኘት አስቸጋሪ ነበር። ምግብ እና ልብስ የሚያመጡልን ቤተሰቦቻችን ከሃምሳ ሜትር በላይ ርቀው እንዲቆሙ ይገደዳሉ።

አንድ ቀን እናቴ ልትጠይቀኝ መጥታ ተጠርቼ ስወጣ ዝናብ እየወረደባት ራቅ ብላ ቆማ አየሁ። በጣም ተናድጄ ሳላናግራት ወደ ክፍሌ ተመለሰኩ።

ከዚህ በኋላ በዚህ ሁኔታ ቤተሰብ ማናገር እንደማልፈልግ ለፖሊሶቹ ነገርኳቸው። የእስር ቤቱ አሥተዳደርም ከከፍተኛ አመራሮች ጋር ተወያይቶ ቤተሰብ የምናናግርበት ቦታ ተዘጋጅቶ በሁለት ሜትር ርቀት ማነጋገር ቻልን። ምግብ አምጥተው ሊያናግሩን የሚችሉት ግን ቀድመን ያስመዘገብናቸው ሦስት የቤተሰብ አባላት ብቻ ነበሩ።

ይህንን ክልከላ የምንወጣበትን ዘዴ ስንፈልግ በሕገ-መንግሥቱ መሠረት አንድ አስረኛ በሦስት አካላት የመጠየቅ መብት እንዳለው ተረዳን፡ እነሱም ጠበቃ፣ ሐኪም እና የሀይማኖት

አባት ናቸው። ከሦስቱ አካላት መካከል ጠበቃ የሚገባ ቢሆንም በሕጉ መሠረት በምሥጢር እንዳናወራ እና ብቻችንን እንዳያዩን ፖሊስ ከነናችን ይቆማሉ። ለፍርድ ቤት አቤት ብለን ብቻችንን እንድናናግር ተፈቀደልን፡ ፖሊሶችን ከእኛ ራቅ ቢያደርጉም ጠበቆቻችንን ካሜራ በተገጠመለት ክፍል ውስጥ እንድናማክር አደረጉ። ይህንንም ለፍርድ ቤት አመልክተን ለሌላ ክፍል ተቀይሮ በምሥጢር ማውራት ቻልን። የጤናም ጉዳይ በተመሳሳይ መንገድ በፍርድ ቤት ተከራክረን ተፈቀደልን። ፌደራል ፖሊሰ እንደተወሰድን በጣም አሞኝ ወደ ፖሊስ ሆሰፒታል

## 10.3. **ቃሊቲ**

ቃሊቲ ጠባቂዎቹ እና አብረውን የተያዙ ቄሮዎች ዞን ስምንት ተብሎ ወደሚጠራውና የቀድሞ የመንግሥት ደኅንነት ሰዎች የታሰሩበት ግቢ ሲወስዱ፤ እኔ፣ በቀለ፣ ሃምዛ እና ሸምሰዲን ስድስተኛ ቤት የምትባል ትንሽ ግቢ ውስጥ ለብቻችን አስገቡን። እኔ እና በቀለ አንድ ክፍል፤ ሃምዛ እና ሸምሰዲንን ሌላኛው ክፍል ተመደብን። ፖሊስ የማደሪያ ክፍላችንን በር ሲከፍተው በረሮ ቤቱን ሞልቶ እየተርመሰመሰ ተቀበለን። የተቻለንን ያህል ጠርገን አውጥተን እቃችንን አስገባን። በፖሊስ ጣቢያ ቆይታችን መሬት ላይ በተነጠፈ ፍራሽ ላይ ስንተኛ ነበር። ቃሊቲ ስንዛወር ከብረት የተሠራ አልጋ ከነፍራሹ አገኘን። የመኝታ ክፍሉ ውስጥ ሽንት ቤት ስላለው እንደ ፖሊስ ጣቢያው ጠዋት ፖሊስ መጥቶ እስኪከፍት መጠበቅ ቀረልን።

የመንግሥት እና የተወሰኑ የመዝናኛ ቻናሎች ብቻ የሚያስተላልፍ ቢሆንም ቴሌቪዥንም አለ። ያኔ ብዙ ጊዜ በሚዲያ እየቀረቡ የመንግሥት ተቃዋሚዎችን የሚወርፉት ሁለት ታዬዎች ስለነበሩ፤ ዋልታን ታየ ቦጋለ፣ ፋናን ደግሞ ታዬ ደንደዓ ብለን ሰ! ናቸው። ከግል ጣቢያ ቃና ስለነበር የመንስግትን ፕሮፓጋንዳ ለማምለጥ ስንቸከልበት የአማርኛ የፍቅር ቃላትን ተማርንበት። " የገባን ዕለት አንዱን ጦር አ ጠፍት - ቃሊቲ ገና አሁን ትክክለኛውን እስረኛ and wrin C ፊልም ለማስተዋወቅ። በቀለም "ላንተ በልዩ ትዕዛዝ የተዘጋጀ 31 ኣንኳ ድሮም እዚህ ነበርኩ" ብሎ ተረበኝ። ከጥቂት ቀናት በኋላ ሌላ ማስታወቂያ ለ- -ደግሞ በቀለን ብሎ እንግሊዝኛ ተናጋሪ" የሚል መጣና በቁም የእጁን አገኘ።

በነጋታው የፌደራል ማረሚያ ቤት ኮሚሽነሮች ሊያነጋግሩን መጡ። ለደኅንነታችን እንደሚጨነቁ በመጥቀስ፣ ቆይታችንን በትብብር ጥሩ እንድናደርግ አደራ አሉን። እኛም ማረሚያ ቤቱን ማሥተዳደር ሥራቸው መሆኑን እና በመታሰራችን ከእነሱ ጋር የሚያገናኘን ነገር እንደሌለ አረጋገጥንላቸው። የማረሚያ ቤቱን ሕግ እንደምናውቅ እና እንደምናከብር ቃል ገብተንላቸው፣ መብታችን እንዲነካ ግን እንደማንፈቅድ አሳወቅናቸው። ማንኛውም ችግር ከገጠመን እንድናስጠራቸው ነግረውን ተለያየን።

ወደ ቃሊቲ ከተዘዋወርን በኋላ ሕዝቡ እንደልቡ ሊጠይቀን የሚችልበትን ዕድል አገኘ። ፍርድ ቤቱ ምግብ ከቤተሰብ እንዲመጣ ብሎ በማዘዙ ቤተሰብም ሌላውም ጠዋት እና ማታ ሊጠይቀን መጉረፍ ጀመረ። ብዙ ሰዎች እንደ አርሲ፣ ባሌ፣ ሐረርጌ፣ ወለጋ፣ ቦረና፣ ጉጂ፣ ወሎ ከመሳሰሉ ሩቅ ቦታዎች በመምጣት ይጠይቁናል። ከባሌ የመጡ አንዷት አሮጊት ዱቄት እና ቅቤ አዘጋጅተው በመምጣት አዳማ ሰው ጋር አድረው በጠዋቱ ገንፎ ሠርተው አመጡልን።ብዙ እናቶች ከድሬደዋ በአውሮፕላን መጥተው ጠይቀውን ይመለሳሉ። በተለይ ከአወዳይ እና ሻሸመኔ ቢያንስ በወር አንዴ ይመጣሉ። ከሐሳሳ በየወሩ ሁለት አውቶብስ ሞልተው ይመላለሱ ስለነበር፤ በር ላይ ያሉ ፖሊሶች አውቶቡስ በመጣ ቁጥር "ሐሳሳዎች መጡ" ይሉ ነበር። አንድ ቀን ዕድሜያቸው ከመቶ ዓመት በላይ የሆናቸውና መራመድ የማይችሉ አዛውንት ከባሌ ሊጠይቁን መጥተው ፖሊሶች ከጎን እና ከጎን ተሸክመው አስገቧቸው። ያመጡልን ገንዘብ ላይ

እንትፍ ብለውበት፣ መርቀውን ሄዱ። አካል ጉዳተኞች በተሰባበረው እና በአስቸጋሪው የአበር ቤት ግቢ መንገድ በዊልቸር እያለፉ ይመጡ ነበር። መንገድ ላይ የምትኖር አንዲት የአእምሮ ሕመምተኛ ዘወትር ልትጠይቀን ትመጣለች ።

ታዋቂ ነጋዴዎች እኛንለመጠየቅ እንዳይመጡ ባልነው መሠረት በልጆቻቸው እና በሚስቶቻቸው በኩል ልብስ እና ሌላ ቁሳቁስ ይልኩልናል። ማንም ሰው ከሦስት መቶ ብር በላይ ይዞ እንዲገባ አይፈቀድም። እንደዛም ሆኖ በየቀኑ ለእስር ቤት ብዙ ሊባል የሚችል ገንዘብ እንሰበስባለን። በዚህ ገንዘብ በተለያዩ እስር ቤቶች ውስጥ ላሉ የፖለቲካ እስረኞች ልብስ፣ መድኃኒት እና ምግብ እንዲገዛላቸው እንልካለን።

በሂደትም የእስር ቤቱ አሥተዳደር እና ፖሊሶች በእኛ ላይ ሙሉ እምነት እያሳደሩ መጡ። በየሀይማኖት በዓላት ወቅት ሕዝቡ መጥቶ አብሮን ያከብራል። በተለይ ኢድ፣ ጥምቀት፤ ኢሬቻ እና መስቀል እኛ ጋር ለማሳለፍ የሚመጣው ሰው ከመብዛቱ የተነሳ እስር ቤቱ እየተቸገረ መጣ። ተማሪዎች በምርቃታቸው ስለት ጋዋናቸውን እንደለበሱ መጥተው በቀለን መርቀን ሀታሙ

ዓርብ ሰው ሊጠይቀን ሲመጣ ሁላችንም ጀለቢያ (ሙደወር) ለብሰን እንጠብቃቸዋለን። አንድ ቀን ታላላቅ ሼኾች እያናገሩን እያለ በቀለ ሙደወር ለብሶ ብቅ አለና "ሰላም- አሌይኩም" አላቸው። ሼኾቹ እሱን እንዳናገሩት ተደስተው መጥተው «በቀለን አሰለምከው እንዴ?» አሉኝ። «ተያይዤዋለሁ ትንሽ ነው የሚቀረኝ» ስል ቀለድኩ። «ምን ቀረህ?» ብለው በጉጉት ሲጠይቁኝ «ማሻ አላህ፣ ቢስሚላህ እና አልህምዱሊላህን አስተምሬዋለሁ። እሽ ሀዱ አን-ላኢላህ ኢለላህን ብቻ ምላሱ መያዝ አቃተው። እስኪ እናንተ ሞክሩ።› ብዬ ቀልዴን እከልኩበት። ሼኾቹ እውነት መስሏቸው በቀለን ሄደው ማነጋገር ጀመሩ። በኋላ አንድ ላይ ሆነን እየቀለድን እንደሆነና ማንም ሀይማኖቱን እንዳልቀየረ፣ በቀለም የለበሰው ለሚጠይቁን ሰዎች ክብር እና አንድነታችንን ለማሳየት እንደሆነ ነገርናቸው። በቀለ የረመዳን ወር አብሮን ይጾም ስለነበር የገና በዓል ከረመዳን ወር ጋር በመገጣጠሙ፣ በዓሉን አብረነው ለማድመቅ ብለን ለሁለት ቀን ጾም አስፈታን። እሱ ሀያ ስምንት ቀን ከእኛ ጋር ከጾመ፤ ሁለቱን ቀን በኋላ በማካካሻ (ቀዳ) እንጾማለን ብለን ከእርሱ ጋር በላን።

ሊጠይቀን የሚመጣ ሕዝብ ለረጅም ዓመታት በመታሰር የሚታወቁትን የነብዩ የሱፍ ታሪክ Aየነገረ ተስፋ እንዳንቆርጥ ሊያበረታታን ይሞክራል። ይህንን ታሪክ ሁል ጊዜ ሰለምንሰማ የሆነ ሼኽ በመጣ ቁጥር ከእኛ የተሻለ ስለሀይማኖት ማውራት ወደሚችለው በቀለ እንመራዋለን። ሌሎች ደግሞ የኔልሰን ማንዴላን ታሪክ በማውሳት ሊያበረታቱን ሲሞክሩ፣ «እንዴ ሀያ ሰባት ዓመት ትታስራላችሁ ብላችሁ እያሟረታችሁ ብን ነው?» እያልን እንተልዳለን። በአጠቃላይ ኦሮሞ ብቻ ሳይሆን ብዙ ብሔር ብሔረሰቦች እየጠየቁን እና እያዝናኑን የእስር ቤት ስቃይ እንዳይሰማን አበረታቱን። ይህም ለዚህ ሕዝብ ምንም ዓይነት መሥዋዕትነት ብንከፍል እንደሚገባው አረጋገጠልን።

ከሀጫሉ ግድያ በኋላ በግፍ የታሰሩ እና ብዙ ስታይ ደርሶባቸው የተፈቱ ወጣቶች ቃሊቲ ሊጠይቁን ሲመጡ ወደ ኦሮሞ ነጻነት ሠራዊት ለመቀላቀል እንደወሰኑ ነግረውን ይሰናበቱናል። እነዚህ ትላንት በቄሮ ትግል ወቅት ትልቅ መሥዋዕትነት ከፍለው ለውጥ ያመጡ ወጣቶች ምስጋናቸው በእስር እና በከፍተኛ ድብደባ መስታየት ሆነ። ከተፈቱ በኋላ ወደ ቤተሰቦቻቸው ቀዬ ሲመለሱም የመንደር ማሊሻዎች ስቃያቸውን በማብዛት መኖር ከለከሏቸው። ስለዚህ

«በቀዬኣችን ከመሞት ለትግሉ መሥዋዕት መሆን አለብን» ብለው እንደወሰኑ ይነግሩናል። በወያኔ ዘመን ለረጅም ጊዜ ታስሮ የነበረ አንድ ልጅ ከሀጫሉ ግድያ በኋላ በድጋሚ ታሰሮ ሲፈታ ወደ ቃሊቲ መጣና «ጀዋር፣ እኔ ካሁን በኋላ ሰልችቶኛል። ከእንግዲህ እንደ እኔ ያለ ወንድ እንደ ከብት በፈለገው ቀን እያሰረኝ፣ እንደ አህያ እየገረፈኝ መኖር አንገሽግሾኛል። በሰላማዊ ትግል ባምንም ከዚህ በላይ መታገሥ አልችልም። መሮ ጋር እሄዳለሁ» አለኝ። ይህ ከወጣቶች ስንሰማ የነበረው ነገር የፖለቲካው ሜዳ ሙሉ በሙሉ እንደተዘጋ እና ስቃዩ ተባብሶ ቁሮን ወደ ጫካ እየገፋ እንደሆነ አመላካች ነው።

## 10.4.የፍርድ ቤት ሂደት

የፍርድ ሂደታችን ከጅምሩ አስቂኝ ነበር። መጀመሪያ ፍረድ ቤት የወሰዱን ዕለት ምንም ዓይነት ተጨባጭ ወንጀል ስላጡብን ዋስትና ከልክለው እስር ቤት ሊያቆዩን ስለፈለጉ የኦሮሞ ባሕል ማዕከል በሞተው ፖሊስ ግድያ ከሰሱን። በሚቀጥለው የፍርድ ቤት ቀጠሮ ደግሞ መቶ ሰባ ስምንት ሰው አስገድላችኋል የሚል ውንጀላ ለፍርድ ቤቱ አቀረቡ። ቀጥሎ የሚኞችን ቁጥር ወደ መቶ ሀያ ሦስት ዝቅ አደረጉት። ችሎቱን እንድናገር አስፈቅጄ «ቀሪዎቹ ሃምሳ አምስት ሰዎች ከሞት ተነስተው ነው እንዴ ቁጥሩ የቀነሰው» በማለት ጠየኩ። ዳኛው መርማሪ ፖሊሱን እንዲመልስ ሲጠይቀው «አላውቅም» ብሎ አቀረቀረ። ገና ከጅምሩ እየሆነ ያለው የሐሰት ተውኔት መሆኑን እኛ ተከሳሾች ብቻ ሳንሆን ፖሊስ፣ አቃቤ ሕግ እና ዳኞችም ያውቃሉ። እኛን ከምርጫ ለማስወጣት የተቀነባበረ የሐሰት ድራማ መሆኑን እያወቅን በፍርድ ሂደቱ ስንሳተፍ ነበር።

ከተያዝኩበት ዕለት አንስቶ እንደሌላ ተጠርጣሪ ምርመራ ተካሂዶብኝ አያውቅም። በሚዲያ ያለ የሌለ ወንጀል ቆልለውብኝ ቢያወሩም አንድም ሰው "ይሄን ወንጀል ፈጽመሃል ወይ?" ብሎ የጠየቀኝ አልነበረም። አንድ ቀን ልንከሰስ ጥቂት ቀናት ሲቀሩት የፌደራል ምክትል አቃቤ ሕግ የሆኑት ፍቃዱ ጸጋዬ ከመርማሪ ፖሊሶች ጋር መጥተው ቃሌን መቀበል እንደሚፈልጉ ነገሩኝ። እኔም «በሚዲያ ስትለፍፉ የምትውሉትን ወንጀል እንዳልሠራሁ ሁላችሁም ታውቃላችሁ። ባለፉት ሁለት ዓመታት የተፈጸሙ ነገሮችን እንድናገር ከፈለጋችሁ፣ ጠበቆቼ እና ሚዲያ ባለበት ዘርዝሬ ለመናገር ዝግጁ ነኝ። አለቆቻችሁ ይህ እንዲሆን ከፈቀዱላችሁ ጠይቁና በድጋሜ እንገናኝ» አልኳቸው፤ በዚያው ቀሩ። በቀለን ከእኔ ቀጥሎ ሲጠሩት ለጠየቁት ጥያቄዎች በሙሉ መልስ ቢሰጣቸውም በኋላ ከመሠረቱት ክስ ጋር አላያያዙትም። ይህም የሚያሳየው ለይስሙላ እንጂ በእውነት ስለተባለው ወንጀል የእኛን መልስ እንዳልፈለጉ ነው።

ፖሊስ ምርመራውን ማጠናቀቁን ለፍርድ ቤት እንዳሳወቀ ክስ ሊመሠርትብን ሲገባው፣ አቃቤ ሕግ ግን ቅድመ ምርመራ በሚባል አሠራር በችሎት ምስክርሊያሰማብን እንደሚፈልግ አሳወቀ። ለዚህ ያቀረበው ምክንያት ምስክሮቹ በተጠርጣሪዎቹ ጫና ሊጠፉ ወይም ሊገደሉ ስለሚችሉ ፍርድ ቤቱ ቃላቸውን እንዲመዘግብ እፈልጋለሁ የሚል ነበር። በተጨማሪም የምስክሮቹ ማንነት እንዳይታወቅ ከመጋረጃ ጀርባ ሆነው እንዲመስክሩለት ጠየቀ። የሚመሰከሩብንን ሰዎች ማንነት ማወቅ ሕገ መንግሥታዊ መብታችን መሆኑን በመጥቀስ ብንከራከርም ሰሚ አጣን። አቃቤ ሕግ አሥራ ስድስት ምስክሮች ከመጋረጃ ጀርባ ማቅረብ እንደሚፈልግ ገልጾ ማሰማት ጀመረ።

የውሸት ምስክሮችን እያዘጋጁ እንደሆነ ስለምናውቅ ከጠበቆቹ ጋር መስቀለኛ ጥያቄ እየጠየቅን ውሸታቸውን ማጋለጥ ጀመርን። ለምሳሌ ከምስክሮች አንዱ «ጀዋር አይሪስ በሚባል መኪና ጳውሎስ ሆስፒታል ውስጥ ገብቶ የምኒሊክን ሃውልት አፍርሱ፣ መንግሥትን ገልብጡ ብሎ አዘዘን» በማለት መስከረብኝ። እውነታው ግን እኔ ጳውሎስ ሆስፒታልን አይቼው አላውቅም።

የታሰርን ዕለትም የሀጫሉን አስከሬን ከሆስፒታል ከወጣ በኋላ ነበር መንገድ ላይ የደረስንበት። አይሪስ የሚባል የመኪና ስም ስለመኖሩም ከምስክሩ መስማቴ ነበር።

ሌላ የአቃቤ ሕግ ምስክር ቡራዩ እንዳየኝና ፖሊስ ላይ ተኩስ እንዲከፈት ማዘዜን ተናገረ። የዚያ ምስክር እና የጠበቃችን አሥቂኝ ምልልስ በጥቂቱ ይህን ይመስላል።

ጠበቃ፡ «አቶ ምስክር እስቲ ምን አየህ?»

ምስክር፡ «ጀዋር ጥቁር መኪና ውስጥ ሆኖ መስኮቱን ከፈተና "ቄሮ እዚህ ምን ትጠብቃላችሁ ጠመንጃ ከፖሊስ ውሰዱ" ብሎ ሲያዝ ሰማሁ።»

ጠበቃ፡ «ከዚያ በኋላ ምን ተፈጠረ?»

ምስክር “ቄሮ ፖሊስ ላይ ድንጋይ መወርወር ጀመረ። የጀዋር ጠባቂዎች ተኩስ ከፍተው የአሥተዳደር ቢሮውን በአሥራ ሦስት ጥይት ደበደቡ።»

ጠበቃ፡ «ድንጋይ ሲወረወር እና ጥይት ሲተኮስ አንተ እንዴት ሆንክ?»

ምስክር፡ «ወደኩኝ። ከሚወረወረው ድንጋይ እና ከጥይት ተኩስ የሚሸሸው ሕዝብ ረጋግጦ ጣለኝ።”

ጠበቃ፡ «አንተ ወድቀሃል። ሌለ ሰውም አንተ ላይ ተደርቦ ወድቆ ነበር። ስንት ሰው ይሆናል አንተ ላይ የወደቀው?»

ምስክር: «ስድስት ሰዎች ይሆናሉ።»

ጠበቃ፡ «አንተ ወድቀሃል፣ ስድስት ሰዎች በላይህ ላይ ተደርበው ወድቀው እያሉ ማን እንደተኮሰ፣ ወዴት እንደተተኮሰ እና አሥራ ሦስት ጥይት ቢሮ ሲመታ እንዴት አየህ?»

ምስክር፣ «እግሬ እንጂ ዓይኖቼ አልወደቁም»

ጠበቃ፡ «አግርህ ዓይንህን በቁሙ ትቶ ነው የወደቀው?»

ምስክር፣ «አዎ»

ይሄን ሲሰሙ ዳኛው እና አቃቤ ሕጉን ጨምሮ በፍርድ ቤቱ የታደሙ ሁሉ ሳቁ። በዚህ መልኩ ከቀረቡት ምስክሮች መካከል ብዙዎቹ በመስቀለኛ ጥያቄ ውሸታቸው ተጋለጠ። እኛ ላይ ለመመስከር የመጡት በኦሮሚያ ባሕል ማዕከል ውስጥ የነበሩ ፖሊሶች ደግሞ እኛን የሚጠቅም ምስክርነት ሰጡ። ነገሩ እንደማያዋጣ በመረዳት፣ አቃቤ ሕግ መጀመሪያ ካስመዘገባቸው አሥራ ስድት ምስክሮች ውስጥ ዘጠኙን ብቻ አቅርቦ ለመተው ተገደደ። የቅድመ ምርመራው ሂደት በዚሁ አብቅቶ ክስ መሠረቱብን።

ክሱ ሊመሠረትብን አንድ ቀን ሲቀረው፣ አንድ መርማሪ ፖሊስ እና አቃቤ ሕግ መጥተው ክሱ እንዲመሠረትብን መታዘዛቸውን መሬት መሬት እያዩ ነገሩኝ። እኔም «ይህ የፖለቲካ ውሳኔ ነው። እናንተ ልታስሩኝም ሆነ ልትፈቱኝ ሥልጣን የላችሁም። እትሸማቀቁ፣ ካስፈለገም ከሚነግሯችሁ በላይ ከፍ አድርጋችሁ ክሰሱኝ ሥልጣን

*ሊጨምሩላችሁ ይችላሉ እንጂ በእኔ ዕጣ ፈንታ ላይ የሚጨምረውም የሚቀንሰውም ነገር የለም» በማለት በቀልድ አዋዝቼ ነገርኳቸው። እነርሱም «አይ፣ እኛም ተቸግረን ነው እንጂ ወንጀል እንዳልሠራችሁ እናውቃለን»*

ሲሉ መለሱልኝ። «አይዟችሁ፣ እናንተ አለሰራችሁኝም። የእናንተ ክስ ምርጫው አስኪያልፍ እንዲያቆየን ተፈልጎ እንጂ ሌላ ዓላማ የለውም። እኔ በእናንተ አልናደድም። እንኳን በእናንተ በነ ጠ/ሚኒስትር ዐቢይም ቂም አልያዝኩም» በማለት አጽናናኋቸው።

በማግስቱ የፌደራል ከፍተኛ ፍርድ ቤት ተወስደን የከሱ ግልባጭ ተሰጠን። የተከሰሰንበት መዝገብ በስሜ ስለተከፈተ አንደኛ ተከሳሽ ነበርኩ። እንደ ግለስብ ሀያ ሦስት ሰዎች እንዲሁም ኦሮሚያ ሚዲያ ኔትወርክ (OMN) እንደ ተቋም ተከሰሰን። በእኔ ላይ አራት ክሶች ቀረቡብኝ። ሽብርተኝነት፣ የመፈንቅለ መንግሥት ሙከራ፣ ሕገ ወጥ የጦር መሣሪያ እና ሕገ ወጥ የመገናኛ መሣሪያ ይዞ መገኘት የሚሉ ናቸው። ክሶቹ ውስጥ አስገራሚ ነገርም ነበር። ለምሳሌ ሕገ ወጥ የጦር መሣሪያ የተባለው ከፌደራል ፖሊስ በገንዘቤ ገዝቼ ፈቃድም አራሳቸው አውጥተውልኝ ጠባቂዎቼ የታጠቁት ነበር። እንዲሁም በሽብርተኝነት ከተከሰስኩባቸው ጉዳዮች አንዱ፡ አሥራ ሁለት ሰዎችን በውጫሌ (ሶማሌለንድ) በኩል ወደ ግብጽ ለወታደራዊ ሥልጠና ልኳል የሚል ነው። እነርሱ እንዳሉት ወታደር ለማሰልጠን ልኬያለሁ እንበልና፣ ወደ ግብጽ ለመለክ የሚቀርበው ሱዳን ሆኖ ሳለ ለምን በውጫሌ በኩል እንዲሆን እመርጣለሁ?

በጣም አጳያፊው ክስ አምስት የኦርቶዶክስ እምነት ጳጳሳት እንዲገደሉ ትዕዛዝ ለመሰጠት ሞክረሃል የሚለው ነው። አምስት ጳጳሳት ይባል እንጂ ስማቸው ስላልተጠቀሰ ፖሊስ ስለማንነታቸው እንዲገልጽ ፍርድ ቤቱን ስንጠይቅ “አላውቅም ፋይሉ ውስጥ የለም ብሎ መለሰ። የውሸት ስም እንኳን ጨምረው እውነት ለማስመስል አለመጨነቃቸው፣ በዚህ ጉዳይ ሊከሱኝ የፈለጉት ከዚያ በፊት ከሀይማኖት ጋር ተያይዞ ሲነዛብኝ የነበረውን ፕሮፓጋንዳ ለማጠናከር ብቻ እንደሆነ መገንዘብ አያዳግትም።

ከዚሁ ጋር ተያይዞ ሌላው አስቀያሚ ውንጀላ በኦሮሚያ ውስጥ የሚኖሩ የአማራ እና የኦርቶዶክስ ማኅበረሰቦችን አስገድለዋል የሚል ነው። ለረጅም ጊዜ የሚጠሉኝ ቡድኖች እና ሚዲያዎች የሚነዙብኝን ፕሮፓጋንዳ መንግሥት በክስ መልክ ማቅረቡ በጣም አሳዘነኝ። ድርጊቱ እኔን እንደ ግለሰብ ስም ከማጥፋት አልፎ በኦሮሞ ትግል እና ታጋዮች ላይ እየተካሄደ የነበረውን የውሸት ፕሮፓጋንዳ ሕጋዊ ሽፋን ያላበሰ ነው። ያኔ አቃቤ ሕግ እኔን ለመክሰስ የተጠቀመውን ትርክት ውሎ አድሮ መንግሥትን እራሱ ለመወንጀል ጥቅም ላይ መዋሉን ስመለከት፣ መሰል ሀይማኖት ነክ ክስ እንዲቀርብበኝ ያዘዙ ባለሥልጣናት እንዲህ ያለው ትርክት ወደፊት ሊያመጣ የሚችለውን ችግር እንዳላሰቡበት ጠቋሚ ነው። ነገሩ “ሰውን ለመጉዳት ጉድጓድ አትቆፍር፣ ክቆፈርክም ወደ ታች አታርቅ፣ ምክንያቱም አንተው ልትወድቅበት ትችላለህና” የሚለውን ተረት ያስታውሳል።

ለክሱ ምላሽ የምንሰጥበት ቀን ሲደርስ የተወነጀልኩበት ክስ ውሸት ብቻ ሳይሆን፣ በሕዝቦች መካከል መርዝ የሚረጭ እና ሀገርን የሚያፈርስ ፕሮፓጋንዳ መሆኑን የሚገልጽ ረጅም ጽሑፍ አዘጋጀሁ። በምላሽ ካነሳኋቸው ነጥቦች መካከል፣ የቄሮን ትግል በመምራት ከሳሾቼ ሥልጣን የያዙበትን ለውጥ ከማምጣት እልፎ፣ ወደ ሀገር ከተመለስኩ በኋላም፣ ሀገሪቱን ለማረጋጋት እና ወደ ዴሞክራሲ የሚደረገውን ሽግግር ለማሳካት ያደረኳቸውን ጥረቶች በመዘርዘር፣ ምስጋና እንጂ መታሰርም ሆነ በውሸት ከስ ሰሜን ማጥፋት እንደማይገባ ገለጽኩ። እንደኔ ምኞት እና ልፋት ቢሆን ኖሮ ይህቺ ሀገር አሁን ወዳጋጠማት ቀውስ እንደማትገባ ጠቆምኩ። ያን ረጅም ጽሑፍ ያዘጋጀሁት ለታሪክ ተመዝግቦ እንዲቀመጥ እና መጪው ትውልድ እንዲማርበት

እንጂ ከተከፈተብኝ ክስ ነጻ ያወጣኛል ወይም በእኔ ላይ የሚነዛውን ፕሮፓጋንዳ ያከሽፋል ብዬ በማሰብ አልነበረም።

በፍርድ ቤት ሂደቱ ውስጥ የጠበቆቻችን ሚና ታሪክ የማይረሳው ነው። የመጀመሪያ ቀን ፍርድ ቤት ሲወስዱኝ ጠበቃ አልነበረኝም። በሚቀጥለው ቀጠሮ ግን አሥራ አምስት ጠበቆች መጡ። በፍርድ ቤት ውስጥ ለጠበቆች የተዘጋጀ መቀመጫ አልዳረስ ብሎ ቆመው ነበር። የታሰርነው በፖለቲካዊ ውሳኔ ስለሆነ ጠበቆቹ የቱንም ያህል ጠንካራ ቢሆኑ ፍትሕ እንደማያስፍኑ እናውቃለን።

ሆኖም ሀገሪቷ የምትመካባቸው ጠንካራ ጠበቆች እንደዚያ ተሰልፈው መምጣታቸው ለእኛ ትልቅ ማበረታቻ፣ መጥፎ ለሚያስቡልን ደግሞ አስደንጋጭ ነበር። በተጨማሪም ጠበቆቹ ከተለያዩ የኦሮሚያ አካባቢዎች የመጡ መሆናቸው ኦሮሞ በአንድነት ከመሪዎቹ ጎን እንደቆመ መልዕክት አስተላልፏል። በእኛ ላይ ሲለጠፍ የነበረውን ውሸት በማጋለጥ ረገድም ጠበቆቻችን በጣም ጠቅመውናል። በየደረጃው ያለውን የክርክር ሂደት በመውያየት እና በአግባቡ በመዘጋጀት ወደ ፍርድ ቤት እንቀርብ ስለነበር፣ በችሎት በተደረጉ ክርክሮች ላይ መንግሥትን ከወከለው የዐቃቢ ሕግ ቡድን መብለጥ ቻልን።

የታሰርን ሰሞን ጉዳያችንን ሲመለከት የነበረው የፌደራል የመጀመሪያ ደረጃ ፍርድ ቤት ዳኛ ለእኛ ያለውን ጥላቻ መደበቅ አልቻለም። መጀመሪያ ተይዤ እርሱ ጋር ሲወስዱኝ ንቀት እና ጥላቻ በተቀላቀለበት አስተያየት ይመለከተኝ ነበር። በምናደርገው ክርክር ሁሉ አድሉ ያደርግብን ስለነበር እንዲነሳልን ጠየቅን። ሌሎች ዳኞች ክሳችንን ሰምተው ሊያነሱት ፈቃደኛ ባይሆኑም በራሱ ጊዜ ራሱን አገለለ። “ለሕይወቴ እፈራለሁ” በማለት ጠባቂ እንደተመደበለትና ሥልጣንም እንደተጨመረለት ሰማን። ጉዳያችንን የሚመለከቱ የከፍተኛ ፍርድ ቤት ዳኞችም መጀመሪያ እነርሱ ችሎት ስንቀርብ ፊታቸውን ያኮሳትሩ ነበር። በተለይ አንዷ ዳኛ በግልጽ ብታመናጭቀንም እኛ ግን ታግሰን አክብሮት ማሳየትን መረጥን።

አንድ ቀን እንዳልናገር ለመከልከል ስትሞክር «የተከበራችሁ ዳኞች አንድ ማወቅ የሚገባችሁ ነገር የምንታገለው ለራሳችን መብት ብቻ ሳይሆን እናንተም ሕገ-መንግሥቱ የሰጣችሁን ክብር እና ሥልጣን ሙሉ በሙሉ እንድትጠቀሙ ለማስቻል ነው» በማለት ተናገርኩ። በሂደት ዳኞቹ ከውጪ እንደሚወራብን ጽንፈኛ እና ተሳዳቢ አለመሆናችንን እየተረዱ ስለመጡ፣ ማመናጨቁ እየቀረ በክብር ያስተናግዱን ጀመር። ከእስር ከተፈታሁ በኋላ ከዳኞቹ መካከል አንዱን ሳገኘው መጀመሪያ ሰው እንደምትሰድቡ እና እንደምትንቁ ተነግሮን ስለነበር በረታንባችሁ። በኋላ ግን ችሎት ላይ ያሳያችሁት አክብሮት እና ሥነ ምግባር እጅ አስሰጠን” አለኝ።

የፍርድ ሂደቱ ሲጓተት ቆይቶ በክሱ ላይ ምንም ብያኔ ሳይሰጥ አንድ ዓመት ተኩል ታስረን ምርጫው ካለፈ በኋላ ከእስር ተፈታን። ምንም እንኳን በፖለቲካ ውሳኔ እንጂ በፍርድ ቤት ክርክር ነጻ ተብለን ከእስር እንደማንለቀቅ ብናውቅም በፍርድ ሂደቱ ውስጥ በሕገ-መንግሥቱ እና በሌሎች ሕጎች የሰፈሩ መብቶች እንዲከበሩ ተከራክረናል። በችሎት የሚታዩ ግድፈቶችን፣ የታሳሪዎችን አያያዝ፣ በእስረኞች ላይ የሚደረገውን ፕሮፓጋንዳ እና የመሳሰሉትን ጉዳዮች በመቃወም እስከ ሰበር ሰሚ ችሎት ድረስ በመከራከር ስንረታ ነበር። በችሎት ስንታገል የነበረውም የግል መብታችንን ለማስከበር ብቻ ሳይሆን የሀገሪቱን የፍትሕ ሥርዓት ለማሻሻል ይጠቅማል ብለን ስላሰብንም ጭምር ነው።

## 10.5.**የረሃብ አድማ**

ከተያዝንበት ጊዜ ጀምሮ መብታችን ሲጣስ የረሃብ አድማ በማድረግ እንታገል ነበር። መጀመሪያ ሦስተኛ ፖሊስ ጣቢያ በነበርንበት ወቅት፣ አንድ ጠዋት በቀለን ለሽንት ሳይከፍቱለት ስለረሱ ተናዶ ምግብ አቆመ። ፖሊሶቹ እንዳሳምነው ጠይቀውኝ ሳናግረው ምክንያቱን ስላስረዳኝ እኔም አድማውን ተቀላቀልኩ። በማግስቱ የጣቢያው አዛዥ መጥቶ ለተፈጸመው ስህተት ይቅርታ ጠይቆ ምግብ ወደ መመገብ ተመለስን። ከዚያ በኋላ በፌደራል ፖሊስም ሆነ ወደ ቃሊቲ ከተዛወርን ወዲህ የረሃብ አድማን መብታችንን ለማስከበር ስንጠቀምበት ነበር።

ረጅሙን የረሃብ አድማ የጀመርነው የኦነግ አባል የሆኑት ኮሎኔል ገመቹ እያና ላይ እየደረሰ የነበረውን በደል በመቃወም ነው። ኮሎኔል ገመቹ በ2006 የኢትዮጵያን መከላከያ ሠራዊት ትተው ወደ ኦነግ ለመቀላቀል ኤርትራ ከሄዱ የኦሮሞ ተወላጅ የጦር መኮንኖች አንዱ ነው። በ2010 ዓ.ም ለውጥ ሲመጣ ከኦነግ ጋር ወደ ሀገር ቤት ገብቶ ብዙም ሳይቆይ ተይዞ ታሰረ። የኦሮሞ አመራር መማክርት ላይ በተደረገ ውይይት ከስምንት ወራት ቆይታ በኋላ ተፈታ። የሀጫሉን ግድያ ተከትሎ በድጋሚ ከታሰረ በኋላ ፍርድ ቤት በተደጋጋሚ በነጻ ቢለቀውም ከአንዱ አስር ቤት ወደ ሌላ ከማዘዋወር በቀር ሊፈቱት ፈቃደኛ አልነበሩም። አዋሽ ካምፕ በታሰረበት ወቅት ለአርባ ቀናት ሰውነቱን ሳይታጠብ በቀን አንድ ዳቦ እየሰጡ እንዳቆዩት ሰማን።36 በኋላም በፌደራል ፍርድ ቤት ተከስሶ እኛ ወደነበርንበት የቃሊቲ እስር ቤት አመጡት።

መጀመሪያ ወደ ፖለቲካ እስረኞች ማቆያ ግቢ የወሰዱት ቢሆንም ከጥቂት ቀናት በኋላ እስር ቤት ውስጥ ጥቃት ካደረሱ አደገኛ ወንጀለኞች ጋር አሰሩት። ይህ ድርጊት ሕይወቱን አደጋ ላይ ለመጣል ያለመ በመሆኑ እኛ ባለንበት አስር ቤት ለዚህ ሕዝብ ትልቅ መሥዋዕትነት የከፈለ የኦሮሞ አመራር ሕይወቱ አደጋ ላይ ሲወድቅ በዝምታ አናይም በማለት ምግብ መብላት በማቆም ተቃውሞ ጀመርን። አምስት ቀናት እንደቆየ ኮሎኔል ገመቹን ከቦታው አስወጥተው ወደ ቂሊንጦ እስር ቤት አዛወሩት። እኛ ግን ሌላ ጥያቄ ጨምረን አድማውን ቀጠልን። በወቅቱ ተራዝሞ የነበረው ምርጫ እየተቃረበ ስለነበረና ሁለቱ የኦሮሞ ፓርቲዎች (ኦነግ እና ኦፌኮ) ከዚህ ምርጫ ተገፍተው እየወጡ በመሆናቸው ሕዝቡ እና ዓለም አቀፉ ማኅበረሰብ ለዚህ ጉዳይ ትኩረት እንዲሰጠው ፈለግን።

ከዚያ በፊት ለአጭር ጊዜ የረሃብ አድማ እናደርግ ስለነበር የኋለኛውን አድማ ስንጀምር በተወሰነ መልኩ ረሃብን ተለማምደናል። በቀለ ከዚያ በፊት በታሰረበት ወቅት ለዘጠኝ ቀናት የረሃብ አድማ አድርጎ መቆየቱን ስለነገርን፤ በዚህኛው ዙር ቢያንስ ለአስር ቀናትም ቢሆን እናደርጋለን ብለን ቀጠልን።[37]

የረሃብ አድማ ማለት ከውኃ በስተቀር ከምግብ ሙሉ በሙሉ መታቀብ ነው። የመጀመሪያዎቹን አምስት ቀናት በጣም ይርባል፣ እንቅልፍ ይከለክላል። ከዚያ በኋላ ግን ድካም እንጂ የረሃብ ስሜት ይጠፋል። ከዶክተሮቻችን እንደተረዳነው የሰው አካል የሚፈልገውን ኃይል ለማመንጨት በሁለት መንገድ ይሠራል። የተለመደው መንገድ የምንመገበውን ምግብ በቀጥታ

ወደ ኃይል በመቀየር መጠቀም ነው። ከምንበላው ምግብ የተወሰነውን ለጊዜው ለሚፈልገው ኃይል ተጠቅሞበት ቀሪውን በአብዛኛው በስብ (ጮማ) መልክ ያከማቻል። ለተወሰኑ ቀናት ያለ ምግብ ስንቆይ፣ ሰውነታችን የተከማቸውን ሰብ ወደ ኃይል በመቀየር መጠቀም ይጀምራል። የረሃብ ስሜት የሚሰማን ሰውነታችን ከውጭ የሚገባን ምግብ በሚጠባበቅበት ወቅት ስለሆነ፣ ከውጭ የሚገባ ምግብ መጠበቅ ሲያቆምና የተከማቸ ስብ መቀየር ሲጀምር የረሃብ ስሜት ይቆማል።

ያለ ምግብ ለሳምንታት መቆየት ቢቻልም ያለ ውኃ መቆየት የሚቻለው ጥቂት ቀን ብቻ እንደሆነ በተጨባጭ እየነው። አድማውን ስንጀምር ምግብ ብቻ ሳይሆን ውኃም መጠጣት አቁመን ነበር። ከተወሰኑ ቀናት በኋላ ሐኪሞቻችን የደም እና የሽንት ምርመራ ሲያደርጉ ኩላሊታችን ላይ ጉዳት እየደረሰ መሆኑን ተረዱ። ረዘም ላለ ጊዜ የረሃብ አድማውን መቀጠል የምንፈልግ ከሆነ ውኃ መጠጣት እንዳለብን መክረው አሳመኑን።

በተጨማሪም፣ የዓለም አቀፍ ቀይ መስቀል ማኅበር ሐኪሞች በጎበኙን ወቅት፣ ለረጅም ጊዜ የሚቆይ የረሃብ አድማ በአንጎል ውí. ነዜሚካል መዛባት በማስከተል ለአካለዊ እና NዕምርVE ጉዳት እንደሚያመጣ ነገሩን።የኬሚካል መዛባቱ ረሃብ አድማውን እያካሄድን ሳሌም ራስን እስከመሳት ሊያደርስ እንደሚችል አስረዱን። ራሳችንን ከሳትን ደግሞ በእስርቤቱ ባለስልጣናት ያለፍቃዳችን እንድንመገብ ልንደረግና አድማውን ለማቋረጥ እንደምንገደድ ስለስጋን፣ የኬሚካል ማዛባቱን አደጋ ለመቀነስ የሚያችሉ ኤሌክትሮላይቶች ለመውሰድ ወሰንን። ሐኪሞቻችንም እነዚህን ኤሌክትሮላይቶች ከውጭ እና ከሀገር ውስጥ እያስመጡልን መጠተም ጀመርን።

ከታሰርንበት ወቅት ወቅት ጀምሮ በዶክተር ኢሊሊ ጀማል አስተባባሪነት የተለያዩ ዶክተሮች በነጻ ጤናችንን ይከታተላሉ። የረሃብ አድማውን ስንጀምርም ሌሎች ሐኪሞች ተጨምረው እና የበለጠ ተደራጅተው ከጎናችን ቆሙ። በየቀኑ ቃሊቲ እስር ቤት እየመጡ የደምና የሽንት ናሙና በመውሰድ ሰውነታችን የደረሰበትን ጉዳት እየመረመሩ አስፈላጊውን መድኃኒት ያመጡልናል።

የማረሚያ ቤቱ አሥተዳደር መጀመሪያ ላይ ልክ እንደ ባለፉት የረሃብ አድማዎች ለተወሰኑ ቀናት ምግብ አቁመን የምናቋርጥ መስሏቸው ነበር። ቀናቱ እየረዘሙ ሲመጡ እና ሰውነታችን መዳከም ሲጀምር ጉዳዩን ወደ መንግሥት ባለሥልጣናት አስተላለፉ። መጀመሪያ ላይ የመንግሥት ምላሽ "በድብቅ ጭኮ እየበሉ ነው" በሚል ፕሮፓጋንዳ አድማችንን ማጣጣል ነበር። እውነቱ ግን አድማውን እንደጀመርን ከቤት የሚመጣ ምግብ እንዲቆም ከማድረግ አልፎ በታሰርንበት ግቢ የነበረ ማንኛውንም ምግብ ጥለናል። ሌላው ይቅርና በፊት በግቢው የምንመገባቸውን ድመቶች እንኳን አድማውን እንደጀመርን ፖሊሶች ከግቢ ውጪ እንዲመግቧቸው አድርገናል። ምግብ ከግቢ ያራቅነው የሚበላ ነገር መኖሩን ቀልባችን ካወቀ የሚፈጠረው መዳዳት አድማችንን ሊፈታተን ስለሚችል ነው።

የመንግሥትን ፕሮፓጋንዳ ተለማምደነው ስለነበር ያን ያህል አላስጨነቀንም። ቤተሰብ፣ ሽማግሌዎች እና ሕዝቡ የሚያደርገው ተማጽኖ ጫና ፈጠረብን። በየቀኑ በመቶዎች የሚቆጠር ሕዝብ መጥቶ ያለቅስብናል። ሽማግሌዎች ልብሳቸውን አውልቀው መሬት ላይ ተንከባለው አድማውን እንድናቆም ይማጸኑን ስለነበር ትልቅ ጭንቀት ውስጥ ከተተን። የበቀለ እናት በዚያ

ዕድሚያቸው ከምዕራብ ወለጋ መጥተው ለመኑን፤ እኛ ግን በአቋማችን ጸናን። አንድ ቀን እናቴ መጥታ «በዚህ ጭንቀት ብሞትብህስ?» ሰትለኝ፤ ተናድጄ «ከፈልግሽ አሁን እዚሁ ክንብል በይ; ሰንት የኦሮሞ እናቶች እየሞቱ አይደል?!» አልኳት። ይህን ስናገራት በደራርቱ ቱሉ የሚመራ የአትሌቶች ቡድን ሊለምኑን መጥተው ነበርና ለእናቴ የሰጠሁትን መልስ ሲመለከቱ ምንም ሳይናገሩ ተሰፋ ቆርጠው ተመለሱ።

በኣድማው ወቅት ብዙ አሰቂኝ ነገሮችም ነበሩ። አሥራ አንድ ቀናት እንደቆየን ሸምሰዲን ጠሃ እየደከመ መጣ። ሃኪሞች ባደረጉት ምርመራ በሰውነቱ ያለው ሰኳር በጣም መቀነሱን እና ሕይወቱ አደጋ ላይ መሆኑን ነገሩት። በሌላኛው ግቢ ያሉ ልጆችም ደክመው ሐኪም ቤት ከገቡ በኋላ ምግብ እንዲጀምሩ ሰለተደረገ፣ ሸምሱም ሄዶ። አድማውን አንዲያቆም ፈለግን። እሱ ግን ከእኛ ተለይቶ አድማውን ማቆም ሰለከበደው፣ በቀለን ለብቻው ጠራና «በቄ አድማውን የምንቀጥለው አሰከ መቼ ነው?» ሲለው፡ በቀለም «ጥያቄዎቻችን አሰኪመለሱ ወይም አስክንሞት ድረሰ» ብሎ መለሰለት። ሸምሱም «በቄ፣ እኔ ለመሞት ዝግጁ አይደለሁም ይህን አንኳን ሳልጠቀም ልሞት ነው?» አለው፡ ቃሊቲ ከሄድን ጀምሮ ሊጠይቁን የሚመጡ ሴቶችን ስልክ ቁጥር ወደመዘገበበት ማሰታወሻ እየጠቆመ። በቀለም «እንደዚያ ከሆነ ችግር የለውም፤ አንተ አድማውን አቁም› ብሎ አሰቆመው።

ከመጀመሪያዎቹ አምሰት ቀናት በኋላ ርሀብ አልተሰማንም፣ ጉልበታችን ግን እየተዳከመ መጣ። ከአንድ ሳምንት በኋላ ሊጠይቀን የሚመጣውን ሕዝብ እንደድሮው ወጥተን ማነጋገር ተሳነን። ጥላ ሥር ተኝተን እንውል ሰለነበር የተወሰኑ የቤተሰብ አባላት እና ሽማግሌዎች ወደ ውስጥ ዘልቀው በተኛንበት እንዲያዩን ተፈቀደ። አድማውን ከመጀመራችን በፊት ጸጉራችንን አሳድገን ነበር። ገላችንን በምንታጠብበት ጊዜ ሳሙናው ከጸጉራችን ላይ አሰኪጸዳ መቆም ስላቃተን ተላጨነው። ከሁሉም በላይ ያሰቸገረን ግን የቆዳችን ማሳከክ ነበር።

ምክንያቱ ደግሞ በሰውነታችን ውሰጥ ያሉ ንጥረ-ነገሮች እየተመናመኑ እንደሆነ ዶክተሮች ነገሩን። ቤተሰብ ሲመጣ ቫዝሊን እና ሎሽን አቀብለውን ብንቀባም በዓይናችን እያየነው ሰውነታችን ወዲያው ምጥጥ ይደርገዋል። ከውጪ የተለያዩ መድኃኒቶችን ቢያሰመጡልንም ምንም አልጠቀመንም«። እኔ እና በቀለ ሌሊት ማሳከኩ አላሰተኛ ሲለን ጀርባችንን እርሰ በእርስ አያክከክን አናድራለን።

የአድማው ቀናት እየረዘሙ በሄዱ ቁጥር የሕክምና ባለሙያዎች ለሕይወታችን መጨነቃቸው ጨመረ።ፍርድቤትሄደንመቀመጥ አቅቶንወንበርላይ አንተኛሰለነበር፡አድማውንአሰክናቆም ድረሰ ፍርድ ቤት አንዳንቀርብ ተወሰነ። እየተዳከምን ሰለመጣን ሆሰፒታል መተኛት አሰፈላጊ ሆን። የደረሰብን የአካል ጉዳት መጠን፣ የልብ ምት፣ የሳንባ አተነፋፈስ እና ሌሎች ነገሮች በማሽን ለሀያ አራት ሰዓታት ክትትል ሊደረግበት አንደሚገባ ሐኪሞቹ ወሰኑ። መንግሥት ግን ወደ ግለ ሐኪም ቤት እንዳንሄድ ከለከለን። ከተያዝንበት ጊዜ ጀምሮ በፍርድ ቤት ትዕዛዝ በግል ዶክተሮች ስንታከም ብንቆይም፣ በወቅቱ ግን በአድማ የተጎዳው አካላችንን ሕዝቡ አንዲያይ ሰላልፈለጉ ወደ ግል ሆስፒታል እንዳንሄድ አገዱ።

ጠበቆቻችን ጉዳዩን ዳግም ወደ ፍርድ ቤት ወሰዱት። የፌደራል ከፍተኛ ፍርድ ቤት ወደ ግል ሆስፒታል መሄድ መብታችን እንደሆነ ወሰነ። መንግሥት ግን ውሳኔውን ለማሰፈጸም ፈቃደኛ

አልሆነም። በድጋሚ ጠቅላይ ፍርድ ቤት ይግባኝ ሰንጠይቅ፡ አሰፈላጊው መሣሪያ ገብቶ

በቃሊቲ ማረሚያ ቤት ይታከሙ ተባለ። ይህ ማለት በእሰር ቤቱ ውሰጥ በሆስፒታል ደረጃ ብቻ የሚቻለው የጽኑ ሕሙማን ክፍል (ICU) ይሥራ አንደ ማለት ነው። ይህ እንደማይቻል የማረሚያ ቤቱ አሥተዳደር እና ሐኪሞቻችን ለፍርድ ቤቱ ቢያሰረዱም መፍትሔ ሰላልተገኘ፣ ጉዳዩ ለሰበር ሰሚ ችሎት ቀረበ።

ይህ በእንዲህ እንዳለ በቀለ በጣም ተዳክሞ ሰለነበር ለአሰቸኳይ ሕክምና ወደ መረጥነው ላንድማርክ ሆሰፒታል በእስር ቤቱ አምቡላንሰ ወሰዱት። ዶክተር ኢሊሊም አብረው ሄደች። ነገር ግን ወደ ሆስፒታሉ ሲቃረቡ መንገዱ በድንገት ሰለተዘጋጋ ወደ ጦር ኃይሎች ሆስፒታል ለመሄድ ተገደዱ። እዚያ ሲደርሱ በቀለ በመንግሥት ሆሰፒታል አልታከምም በማለት ከአምቡላንሱ አልወርድም አለ። ሐኪሞቹም፣ «ታካሚው ፈቃደኛ ካልሆነ አሰገድደን ለማከም ሙያችን አይፈቅድልንም› አሉ።

ከረጅም ሰዓታት ጭቅጭቅ በኋላ ሳይታከም ወደ እሰር ቤት መለሱት። ከዚያም የሰበር ሰሚ ችሎት በግል ሆስፒታል መታከም ‹መብታችን እንደሆነ አረጋግጦ ወሰነ። ከዚህ ውሳኔ በኋላ አድማውን ጀምረን በሠላሳ ስድሰተኛው (36ኛው) ቀን፣ ወደ ላንድማርክ ሆዕፒታል ተወሰድን። እዚያ ሰንደርስ በጣም ደክመን ስለነበር፡ በቃሬዛ ላይ አሰቀምጠው የጽኑ ሕሙማን ክፍል (፲፪) አሰገብተው አሰተኙን። ወታደሮች ከትንሽ አሰከ ትልቅ ጠብመንጃ ወድረው፣ ታማሚዎች እና ዶክተሮች ብቻ ሊገቡበት በሚገባ ክፍል ውሰጥ ቆመዋል። በመሰኮቱ አሻግረን ሰንመለከት መትረየስ ተጠምዷል። እኛ ያለንበት ወለል (floor) ሌላ ሰው መግባት አይችልም። የሆሰፒታሉ ዙሪያም በብዙ ወታደሮች ተከቦ ሰለነበር፡ ታካሚዎች መግባት እና መውጣት ቸግሯቸው ነበር።

የጽኑ ሕሙማን ክፍል እንደገባን ልብሳችንን አውልቀው ገላችንን ሲያጥዮቡን የነበሩ ነርሶች እጃቸው ይንቀጠቀጣል።እኛን በማየታቸው ከመደንገጣቸው በተጨማሪ፣ ቁመናቸው ግዙፍ የሆኑ ወታደሮች ጠመንጃቸውን ይዘው እዚያው ክፍል ውሰጥ ቆመው ሰለነበር ተረበሹ። ነርሶቹ ሰውነታችንን ለማጠብ የለበሰነው በሙሉ መውለቅ እንዳለበት ሲነግሩን፣ ቀድሞኝ ገብቶ የነበረው በቀለ አፍሮ እምቢ አላቸው። እኔ ግን አሜሪካ በነበርኩበት ጊዜ የትርፍ አንጀት ቀዶ ሕክምና በተደረገልኝ ወቅት ልብሴን አውልቀው ያጥቡን ሰለነበር አዲሰ አልሆነብኝም። በቀለ እኔ ያለማንገራገር ለማውለቅ ስስማማ አይቶ ተገረመ። ሃምዛም ከሁለታችን ኋላ ደርሶ ነበርና ነርሶቹ ልብሱን ለማውለቅ ሲሞክሩ ተከሳከላቸው። በኋላ ሁለቱም በጽኑ ሕሙማን ክፍል ውስጥ ከሆስፒታል ልብስ በስተቀር ሌላ ነገር መልበሰ እንደማይቻል አምነው አወለቁ።

ላንድማርክ ሆሰፒታልን የመረጡልን ሐኪሞቻችን ነበሩ። ሆስፒታሉ የተመረጠው በጥሩ መሣሪያዎች፡ በጠንካራ ባለሙያዎች የሚታወቅ ሰለሆነና ለደኅንነታችንም አሰተማማኝ ተብሎ ነው። የሆስፒታሉ ባለቤት ፕሮፌሰር ከበደ ኦሊ ይባላል። በዚያ ሆስፒታል መታከም እንደምንፈለግ ካሳወቅን ጀምሮ “ሽኔ" በሚል የውሸት ውንጀላ አሰፈራርተው እዚያ እንዳንታከም ሚና ሲደረግበት ነበር።

ፕሮፌሰር ከበደ ግን በአቋሙ ጸንቶ ፈቀደልን። በሆስፒታሉ በቆየንባቸው ሁለት ሳምንታት ወታደሮች ግቢውን እና አካባቢውን በመውረር ወጪ ወራጁን ሰለሚያዋክቡ ገበያውን

ዘግተውበት ነበር።ፕሮፌሰር ከበደ ወደ ሆስፒታሉ ከገባንበት ቀንጀጀምሮ ራሱ የሚያምንባቸውን ባለሙያዎች ብቻ መርጦ መደበልን።

እሱም ቢሆን እስከ ወጣንበት ጊዜ ድረስ እኛው ጋር ጠቅልሎ ገብቶ ነበር ማለት ይቻላል። ለሕይወታችን በመሥጋት ውኃ ሳይቀር ራሱ ገዝቶ ቢሮው ውስጥ ቆልፎበት ሰንፈልግ ያመጣልናል። ዶ/ር ሰንበታ እና ዶ/ር ዱፌራም ተራ በተራ እኛ ጋር እያደሩ ይከታተሉናል።

ከግል ሐኪሞቻችን መካከል ዶ/ር ኢሊሊ ጀማል እና ዶ/ር አብዲ ባቲ ቀን እኛ ጋር ይውላሉ። ከተወሰኑ የጤና ባለሙያዎች እና ሁለት ጠበቆች በስተቀር ቤተሰብ መግባት ስለማይችል፣ ይክተርኢሊሊ ከሙያዊ ሥራዋ ጎንለጎን ለቤተሰቦቻችን መረጃ ታደርሰልናለች። ሕክምናችንን ከማስተባበር በተጨማሪ ሰላለንበት ሁኔታ በየጊዜው ለሚዲያ ገለፃ ስለመታድረግ፣ ከእኛ አንድትርቅ ብዙ ዛቻዎች ይደርሱባት ነበር። እሷ ግን ሁሉንም ጫና በመቋቋም እና በሥራዋ ጸንታ በመቀጠል ሕይወታችንን በመታደግ ረንድ ባለውለታችን ናት።

ሆስፒታል ከገባን በኋላ አድማውን እንድናቆም የሚደረግብን ጫና የቀጠለ ቢሆንም፣ ቤተሰብ እና ሕዝቡ ሰለማያዩን የበፊቱ ጭንቀት አልነበረም። ሰውነታችን ከቀን ወደ ቀን አየደከመ ቢመጣም ሞራላችን ጠንካራ ነበር። በሠላሳ ዘጠነኛው ቀን ፕሮፌሰር ከበደ ወደ እኛ መጥተው ከዚህ በላይ እዚህ ከቆያችሁ መሞታቹ እርግጥ ነው። ሆሰፒታል ሕይወትን የምናድንበት እንጂ ዓይናችን እያየ ነፍሰ የምትጠፋበት ቦታ ሰላልሆነ አድማውን ካላቆማችሁ ሆሰፒታሌ ውሰጥ መቆየት ጥቅም የለውምና መውጣት አለባችሁን አለ። እኛ ግን አድማውን የማቋረጥ ፍላጎት ሰለሌለን ለመውጣት ወሰንን። ተሰክቶብን የነበረውን ማሽን መንቀል ሰንጀምር በቦታው የነበሩ ሁሉም ነርሶች እና ወታደሮች ያለቅሱ ነበር።

ወደ እስር ቤት ለመሄድ ተዘጋጅተን የሚያደርሰንን መኪና እየጠበቅን ሳለ፣ ድንገት አንዲት የገጠር ልብሰ የለበሰች ሴት መጥታ እግሬ ሥር ወደቀች። ምናልባት አድማው ሰላደከመኝ ሊሆን ይችላል፡ የወደቀችብኝ ሰው አክሰቴ በቀሉ ቶላ መሰለችኝ። እትዬ በራሷ በሬ ጠምዳ የምታርሰበት ማሳ ያላት፣ ቁጡ በመሆኗ ከአብዛኛው ቤተሰብ የማትስማማ ሲሆን፣ እኔን ግን በጣም ታቀርበኝ ነበር። በተገናኘን ቁጥር ለወትሮው ኮሰታራ የሆነውን ፊቷ ተቀይሮ ድምጿን ከፍ አድርጋ ሰትስቅ ሰዉ ይገረም ነበር። እናም ከላንድማርክ ሆሰፒታል ለቀን ወደ ቃሊቲ እስርቤ ለመለስ እየተዘጋጀን ሳለን መጥታ እግሬ ላይ የወደቀችው ሰው አክስቴ ሁሌ ለብሳው ቤተ-ክርሰቲያን የምትሄደውን የሚመስል ነጭ ልብሰ ለብሳ ነበርና ሁለመናዋ አሷኑ መሰለኝ። እግሬን አልለቅ ብላ ማልቀሷን ሰትቀጥል፣ እሺ ብዬ ከእግሬ ላይ ቀና አድርጌ ሳያት ደራርቱ ቱሉ ናት። አክሰቴን መስላኝ እሺ ብላትም፣ ደራርቱም በጣም የምወዳት እና የማከብራት ሰው ሰለሆነች ቃሌን ማጠፍ አቃተኝ። ከደራርቱ ጋር ታዋቂው የአትሌቲክሰ አሠልጣኝ ኮሚሽነር ሁሴን ሽቦ ነበር። አድማውን ለማቆም መስማማታችን ሲታወቅ በሆስፒታሉ ያሉ ነርሶች እና ፖሊሶች የደሰታ እንባ አነቡ።

ደራርቱ ፕሮፌሰር ከበደ ጋር ሄዳ መሰማማታችንን ሰትነግረው፡ እኛ ጋር መጥቶ ምግብ የምንጀምርበትን እቅድ እና መመገብ ሰንጀምር ሊያጋጥሙን ሰለሚችሉ ክሰተቶች አሰረዳን። ፕሮፌሰር ከበደ ሰውነታችን የተከማቸ ሰብ ለረጅም ጊዜ ሲጠቀም ከቆየ በኋላ ድንገት ከውጪ የሚገባ ምግብ ወደመጠቀም ሲመለሰ እሰከሞት ሊያደርሰ ለሚችል አደጋ (refeeding syndrome) እንደሚያጋልጥ ነግሮን፡ ሰውነታችንን ቀሰ በቀሰ ምግብ መቀበል እንድናላምድ መከረን። በወሎ ድርቅ ጊዜ ለብዙ ቀናት ያለምግብ የቆዩ ሰዎች፣ ድንገት ምግብ ሲሰጣቸው መሞታቸውን እንደምሳሌ ነገረን።

በዚሀም መሠረት አድማው በተደመረ በአርባኛው (40ኛው) ቀን ጠዋት በአንድ ትንሽ ብርጭቆ ሾርባ መጣልን። ለሰሙ ሾርባ ቢባልም የፈላ ውኃ ነበር። ሁለት ፍሬ የዶሮ ሥጋ ቁራጭ እና አንድ የብሮክሊ እንጨት ነበረው። ለረጅም ጊዜ የረሃብ ሰሜታችን ጠፍቶ ቢቆይም ለመብላት ከወሰንን በኋላ ትዕግሥት አጣን። በብርጭቆ የቀረበውን ሾርባ ከፍቼ በማንኪያ ልጠጣው ስል ከሁለቱ የዶሮ ሥጋ ቁራጭ አንዱ መሬት ላይ ወደቀ። ማንም ሳያይ አንሰቼ ልበላው እያሰብኩ፣ አንዲት ነርሰ መጥታ ረገጠችው። መሬት ለወደቀው ሥጋ እያዘንኩ ሾርባውን እንደጠጣሁ ወዲያው ሆዴ መጮህ ጀመረ። ትንሽ ቆይቶ ተቅማጥ ተከተለ። በቀለ እና ሃምዛ ወደ መጸዳጃ ቤት ስሮጥ ይስቁብኛል።

በዚህ ሁኔታ ለሦስት ቀናት በትንሽ በትንሹ ሾርባ እየወሰድን ሰውነታችንን ካለማመድን በኋላ በአራተኛው ቀን የምትፈልጉትን ምግብ እዘዙ ተባልን። እኔ ፓስታ አዘዝኩ፣ በቀለ የክክ ወጥ ስላ/// «ያትላንቱ የአሰተማሪነት ዘመን ድሀነት ናፈቀሀ እንዴ?» ብለን አሾፍንበት። ከሰዓት በኋላ የበቀለ ክክ ጣጣ አመጣ። ከቀናት በፊት እንደሳቀብኝ እሱንም ተራው ደረሰው። በሆድ ቁርጠት ጀምሮት፣ ቀስ በቀሰ ተባብሶ ከላይ እና ከታች ያራውጠው ገባ። ራሱን ሲስት በጣም ተደናገጥን፤ የሚሞት መሰለን። ሐኪሞቹ ምን ማድረግ እንዳለባቸው ፕሮፌሰር ከበደን ጠይቀው የነገራቸውን መድኃኒት ሲወጉት እንቅልፍ ይዞት ሄደ። ከአንድ ሰዓት በኋላ ሲነቃ «ሞቹ የገነት በር ላይ ስደርስ "ጀዋርን ለምን ትተኸው መጣሀ?" ብለው መለሱኝ› አለና አሳቀን።
መብላት በጀምረን ከአምስት ቀናት በኋላ ወደ እስር ቤት ለመመለስ ወሰንን። ሆሰፒታል ብንቆይ ፍላጎታችን ቢሆንም በእኛ ምክንያት ሥራቸው ስለተስተጓጎለ ከዚሀ በላይ ልንጎዳቸው አልፈለግንም። በዚህ ሁኔታ ከሁለት ሳምንት ቆይታ በኋላ ከላንድማርክ ሆሰፒታል ወጥተን ወደ ቃሊቲ ማረሚያ ቤት ተመለስሰን።

ከአድማችሁ ምን የፖለቲካ ትርፍ አገኛችሁን የሚለው ጥያቄ ብዙ ጊዜ ይነሳል። በአድማው ላይ ሳለን ሰዎች ይመጡና «ይህ አፍሪካ ነው በአድማ ተቃውሞ ማን ይሰማቹሃል?» ይሉናል። ለእኛ ግን በሥልጣን ላይ ያሉት ሰዎች መስማት አለመስማታቸው ትልቅ ጉዳይ አልነበረም። አድማውን ያደረግነው በዋናነት ለጎሊናችን ነው። ሕዝባችን እንደ ቅጠል እየረገፈ ባለበት፣ ሺዎች እስር ቤት እየበሰበሱ፣ የኦሮሞ ድምጽ ከሀገሪቱ የፖለቲካ ተዋስያ (political discourse) ተገፍቶ ወደ ምርጫ ሲገባ ዝም ብለን ማየት አልቻልንም።

ወቅቱ የትግራይ ጦርነት ሰለነበር ሁሉም የሀገሪቷ ሚዲያዎች፣ ቴሌቪዥኖች እና ኤፍ ኤም ሬዲዮኖች በኦሮሞ ሕዝብ እና በትግራይ ላይ "ሸኔ" እና "ጁንታ የሚል ሰም በመለጠፍ ፕሮፓጋንዳ ያሰራጫሉ። የኦሮሞን ትግል እውነቶች በማንቋሸሽ የታሪክ ተወቃሽ የሆኑ የትላንት ነገሰታትን በማወደስ ተጠመዱ። በኃይለሥላሴ እና በደርግ ዘመን ሕዝብን ሲጨፈጨፉ የነበሩ ወታደራዊ እና የፖለቲካ ባለሥልጣናት፣ በመንግሥት ሚዲያ በመቅረብ በደም የተጨማለቀ እጃቸውን እያወራጩ በሕዝባችን ላይ ይፎክሩ ነበር። የኦሮሞ ተቃዋሚ ፓርቲ አመራር በእሥራት እና በግድያ ከጨዋታ ውጪ ሰለተደረገ፡ በሕዝባችን ላይ የጥላቻ እና የስም ማጥፋት ዘመቻ ሲያቀጣጥሉ ከልካይ አልነበረም። ይህን ዝም ብለን ከማየት ይልቅ በረሃብ አድማ አካላችን ላይ እርምጃ ወስደን በሕዝባችን ላይ እየደረሰ ያለው ችግር ትኩረት እንዲያገኝ የተቻለንን ሞክረናል። አድማችን እየተራዘመ በሄደ ቁጥር ሰፊ የዓለም አቀፍ ሚዲያ ሽፋን ማግኘቱ ለዓላማጫችን መሰካት ማሳያ ነው። በተጨማሪም በአድማው ለሕዝባችን ልናስተላልፍ የፈለገነው ዋናው መልዕክት በአሰረኛች

እና በኦሮሞ መሪዎች መካከል ያለውን አንድነት እንዲገነዘቡ ማድረግ ነው። መንግሥት አንዳንድ መሪዎችን በማሰር፡ሌሎችን በመግደል እና የኦሮሞ ፖለቲካ ፓርቲዎችን ከምርጫው በማግለል ሕዝቡን ተስፋ ለማስቆረጥ ፈልጎ ነበር። እቅዳቸው እንዳይሳካ ለማክሸፍ አድማውን አንደ መልካም አጋጣሚ በመጠቀም በኦነግ እና በኦፌኮ ፓርቲዎች እንዲሁም በአመራራቸው መካከል ያለውን አንድነት በማጠናከር ረገድ ውጤት አሰገኝቷል።

አድማውን የጀመርን ዕለት ኮሎኔል ገመቹ አያና የኦነግ ከፍተኛ ባለሥልጣን ሲሆን፣ እኛ አድማ አድራጊዎቹ ደግሞ ኦፌኮ ስለሆንን በሁለቱ ፓርቲ መሪዎች መካከል ያለው አጋርነት ጠንካራ መሆኑንም መልዕክት አስተላልፏል። የኦሮሞ ታጋዮች በየትኛውም ጊዜ እና ቦታ ቢኖሩም እርስ በእርሳቸው እንደሚተዛዘኑማሳየት ችለናል። የሁለቱ ድርጅቶች ሊቀመንበሮች አቶ ዳውድ እና ፕሮፌሰር መረራ እኛን መጥተው መጠየቃቸው ይህንን የአጋርነት መልዕክት አጠናክሮታል።

አድማው ሌላ ጥቅምም አስገኝቶልናል። ውፍረት መቀነስ የአድማው እቅድ አካል ባይሆንም ረሃቡ ከልክ በላይ እየወፈረ የነበረውን ሰውነታችንን ቀንሶታል። ከመታሰረ በፊት በጣም ወፍራም ነበርኩ። በቁሮ ትግል ወቅት ከቢሮ ሳልወጣ ለአራት ዓመታት ከኮምፒዩተር ጋር ተቆራኝቼ መቆየቴ ከልክ በላይ አወፍሮኛል። ወደ ሀገር ቤት ከገባሁ በኋላም ለደኅንነት ሲባል ከቤት ብዙም አልወጣም። በዚህ የተነሳ በታሰርኩበት ጊዜ የሰውነቴ ክብደት ከመቶ አሥር ኪሎ በላይ ነበር። እስር ቤትም ክብደቴ ጨምሮ ምናልባትም ወደ መቶ ሀያ ኪሎ ሳይጠጋ አይቀርም። አድማውን አቁመን መብላት ሰንጀምር ሰባ ስድሰት ኪሎ ነበርኩ። ከዚያ በኋላ አንደገና ላለመወፈር በየቀኑ የአካል ብቃት እንቅሰቃሴ መሥራት ጀመርኩ። ጠባቂዎቼ የነበሩ ሁለት ወታደሮች ከእኔ ጋር መሆናቸው የበለጠ እንድገፋበት አድርጎኛል። ከዚያን ጊዜ ጀምሮ ስፖርት ሱሰ ሆኖብኝ በመደበኛነት ቀጥዬበት እየሰራሁ አገኛለሁ።

የረሃብ አድማው ሌላ ትውፊት ከዶ/ር ኢሊሊ ጀማል ጋር የበለጠ እንድንቀራረብ ዕድል መፍጠሩ ነው። ከዶ/ር ኢሊሊ ጋር ከተዋወቅን ቆየት ብሏል። መጀመሪያ የተገናኘነው በ2016 ዘመድ ጥየቃ ወደ አሜሪካ አቅንታ፡ በዚያውም በሰሜን አሜሪካ የኦሮሞዎች እግር ኳሰ ውድድር (OSFNA) ለመታደም ወደ ሚኒሶታ በመጣችበት ወቅት ነበር። የአሜሪካ ግብኝቷን አጠናቃ ወደ ሀገር ቤት ከተመለሰች በኋላም በቁሮ ትግል ውሰጥ ጉዳት የሚደርሰባቸው ሰዎች የሕክምና እርዳታ እንዲያገኙ በማሰተባባር ሰትረዳ ሰለነበር ብዙ ጊዜ አብረን እንሠራ ነበር።

ከለውጡ በኋል ወደ ሀገር ቤት ሰመጣ በደጋሚ በአካል ተገናኝተን የበለጠ ተዋወቅን። በወቅቱ በነበሩ የምሁራን ውይይት መድረኮች ላይ ትሳተፍ ሰለነበር በተደጋጋሚ የመገኛነት አጋጣሚ ነበር። ትውውቃችን በሂደት ተጠናክሮ ልታሰር ጥቂት ጊዜ ሲቀሩት ፍቅር ብንጀምርም፡ ብዙም ሳንገፋበት ለመለያየት ወሰንን።

ከታሰርኩ በኋላ ፍርድቤት በግል ሀኪም የመገልገል መብቴን ቢያረጋግጥም፣ ቀድሞ የነበሩኝ የግል ሐኪሞች እስርቤት ድረስ መጥተው ሊያገለግሉኝ መፍራታቸውን ሰለሰማች፣ ዶ/ር ኢሊሊ ኃላፊነቱን ወሰደች። ሌሎች ሀኪሞችን በመስተባበርም እኔና በቀለን ብቻ ሳይሆን ሌሎች የፖሊቲካ እሰረኞችንም ማገልገል ጀመሩ። የጤናችንን ሁኔታ ለመከታተል ወደ እስርቤት መመላለሷ አቋርጠነው የነበረው ይፍቅር ሰሜት እንዲያንሰራራ አደረገ። እሷን አግኝቼ ለማነጋገር ስል የህክምና ቀጠሯችን እለት ይረዝምብኝ ጀመር። በቀለም ሰሜቴን ከመሸሽግ ይልቅ ፍቅራችንን እንዳድሰው ይገፋፋኝ ነበር።

የበረሃብ አድማው ጊዜ ከመደበኛ ሥራዋ ፈቃድ ወስዳ ሙሉ ጊዜዋን እኛን ለማገልገል ላይ ሰለነበር፡ የኔ በሞት አፋፍ ላይ መሆን እና በሷ ላይ የመንግስት ሰዎች ሲያደርሱ የነበረው ጫና የሰነልቦናትሥራችንን አጠበቀው። የወደፊት ሕልም እና ዓላማችንን በሰፊው ለማውራት ብሉም በጥልቀት ለመተዋወቅ ልባችንን ከፈተው። ከዚህ ቅርርብ አና ትውውቅ በመነሳት እዛው እስርቤት እየላሁ በምግብ ውሰጥ ተደብቆ በመጣ ቀለበት የጋብቻ ጥያቄ አቀረብኩላት። እሷም ተቀበለች። ከአሰር ከተፈታሁ በኋላም ቤተሰቦቿ ጋር ሽማግሌ ላኩኝና ኒካህ አድርገን ትዳር መሰረትን።

# 10.6.የትግራይ ጦርነት

ከለውጡ ማግስት አንስቶ እየሻከረ የሄደው የትግራይ ክልል እና የፌደራል መንግሥት ግንኙነት፣ በምርጫው መራዘም ሰበብ ተባብሶ፣ ፍጥጫው ወደ ወታደራዊ መዛዛት ደረጃ አደገ። በታሰርን በአራት ወራት ጊዜ ውስጥ ጦርነቱ ፈነዳ። ባለፉት ምዕራፎች እንደገለጽኩት፣ ገና ከጅምሩ በጠቅላይ ሚኒስትሩ እና በሕወሓት መካከል የተጀመረው ሽኩቻ ተባብሶ ወደ ግጭት እንዳያመራ፡ በቀጥታ ከሁለቱም ወገን አመራሮች እንዲሁም በመገናኛ ብዙኃን ስማጸን ነበር። ሰሚ ስላልተገኘ የተፈራው ደረሰ።

የትግራይ ጦርነት አስቀድሞ መገመት የሚቻል፣ለማስቀረትም ሰፊ ዕድል የነበረ አሳዛኝ ክስተት ነው። በሕወሓት የበላይነት ሥር የነበረውን የኢሕአዴግ አምባገነናዊ አገዛዝ ሙሉ በሙሉ ከማስወገድ ይልቅ ውስጣዊ ለውጥ ማምጣት ላይ ትኩረት ያደረግነው ይህን መሰል የእርስ በእርሰ ጦርነት እንዳይመጣ ነበር። ምክንያቱም ከሀዳጣን (መፈመሪ2ፈ፡ሃ) ብሔር የወጣ ቡድን ሥልጣኑ ሲናወጥ፣ የሥልጣን ማጣት ብቻ ሳይሆን የኅልውና ሥጋትም ሲለሚያድርበት ሀገርን ወደ እርሰ በእርስ ጦርነት ሊያሰገባ ይችላል።

ስለችግሩ ማሰብ እና መጻፍ የጀመርኩት ለውጡ ከመምጣቱ ከረጅም ጊዜ በፊት ነው። ለምሳሌ በ2010 "Tigrean Nationalism: From Revolutionary Force to Weapon of Repression በሚል ርዕስ በጻፍኩት ረጅም ጽሑፍ በሕወሓት የበላይነት የሚመራውን አምባገነናዊ ሥርዓት ለመጣል የሚደርገው ትግል በጥንቃቄ ካልተመራ አደጋ እንዳለው በመግለጽ ልንከተላቸው የሚገባውን ስልቶች ጠቁሜ ነበር። በ2012 የተቀሰቀሰው የአረብ ሀገራት አብዮት (Arab Spring) ወደ ጦርነር እና የሀገረ-መንግሥት መፍረስ (State Collapse) ካመራ በኋላ፣ ሕወሓትን ከሥልጣን የማውረዱ እና የመተካቱ ሂደት ሊያመጣ ስለሚችለው አደጋ የነበረኝን ሥጋት የበለጠ ጨመረ።

በተለይ የሶሪያ ሁኔታ ከሀገራችን ጋር እጅግ ተመሳሳይ ነበር። ከአለዊይት (Alawite) ህዳጣን የሀይማኖት ቡድን የወጣው እና መጀመሪያ በሃፌዝ አል አሳድ ቀጥሎ በልጁ በሻር አል አሳድ የሚመራው አምባገነናዊ መንግሥት ለአራት አሥርት ዓመታት ሥልጣን ላይ ቆይቷል። በ2011 ሕዝባዊው አመጽ ሲፈነዳ በአገዛዙ ብቻ ሳይሆን በአለዋይት ማኅበረሰብ ላይ የተጋረጠ የኅልውና አደጋ (Existential Threat) እንደሆነ ስለታየ ሥልጣን ላይ ጸንቶ መቆየት ብቸኛው የኅልውና ዋሰትና ተደርጎ ተወስዶ፤ ሀገሪቱን ወደ ከፍተኛ የእርስ በእርስ ግጭት ከተታት። ይህን ሁኔታ በቅርበት ስከታተል ከቆየሁ በኃላ በ2012 “Avoiding Syria and Libya : Lesson for Ethiopia” የሚል ጽሑፍ ጽፌ፣ ሶሪያን እና ሊቢያን ካጋጠማቸው አደጋ ኢትዮጵያን እንዴት መታደግ እንምንችል ምክረ -ሐሳብ አቀረብኩ።

ለኦሮሞ ሰላማዊ ትግል እቅድ ስነድፍም፣ በንድፈ ሐሳብ ጥናት እና በተለያዩ ሀገራት በሚታዩ ተጨባጭ ሁኔታዎች ላይ በመመሥረት፣የእርስ በእርስ ጦርነት እና የሀገር ውድቀት ሳያስከትል

የሕወሓትን መንግሥት ማስወገድ ዋናው ትኩረቴ ነበር። ከላይ እንደጠቀስኩት፣ ከህዳጣን ማኅበረሰብ የወጣ ቡድን ለረጅም ጊዜ ሥልጣን ላይ ቆይቶ አምባገነናዊ አገዛዙን የሚገዳደር

ሁኔታ ሲፈጠር፤ ስልጣኑን ማጣት ብቻ ሳይሆን የጅምላ ዕልቂት ያጋጥመናል የሚለውን ፕሮፓጋንዳ የወጣበትን ማኅበረሰብ ለማነሳሳት ይጠቀምበታል። በዚህም አስከ መጨረሻው ሥልጣን ላይ ሙጭጭ በማለት ሀገሪቱን ለተራዘመ የእርስ በእርስ ግጭት ያጋልጣል።

ሕወሓትም መሰል ማስፈራሪያ በመጠቀም እንደ ሶሪያው የአላውይት ቡድን ልሂቃን ሀገሪቱን ወደከፋ የእርስ በእርስ ጦርነት እንዳያስገባ ቅድመ ጥንቃቄ ያሰፈልግ ነበር። ሥልጣን ላይ ያለን የህዳጣን ቡድን የኀልውና አደጋ ፍራቻ ለመቅረፍ፣ ሥልጣን ቢያጡ እንኳን አካላዊም ሆነ ቁሳዊ ጉዳት እንደማይደርስባቸው ዋስትና ሊሰጣቸው ይገባል። ይህም የህዳጣኑ ልሂቃን በሥልጣን ላይ በነበሩበት ጊዜ ለፈጸሟቸው ወንጀሎች የበቀል እርምጃ እንደማይፈጸምባቸው ማረጋገጥ እና በሥልጣን ዘመናቸው ያፈሩት ሀብት እንደማይነካባቸው አሳማኝ ማረጋግጫ መስጠት ነዉ። በዚህ ስልት በመጠቀም የባሰ ውድመት ሳይመጣ የህዳጣን ቡድንን አምባገነን መቀየር ከቻሉት ውስጥ በኔልሰን ማንደላ የተመራው የደቡብ አፍሪካ ሽግግር ተጠቃሽ ነው።

በዚህም መሠረት የቁሮ ትግል ስልት በአንድ በኩል ሕወሓት በሥልጣን ላይ ለመቆየት ያለውን ጥንካሬ በማዳከም፡ በሌላ በኩል ሥልጣን ከለቀቁ ከላይ የተገለጹት ዋስትናዎች እንደሚጠበቁላቸው ማሳመን ላይ ያነጣጠረ ነበር። እንደገመትነውም ስናደርጋቸው በነበረው ውይይቶች እና ድርድሮች ወደ መጨረሻ አካባቢ ከላይ ከተጠቀሱት የባለሥልጣናት አካላዊ እና ቁሳዊ ዋስትና በተጨማሪ ለሕዝባቸው ደኅንነትም ዋስትና እንደሚያስፈልጋቸው ተናግረናል። የትግራይ ማኅበረሰብ ለጸጥታ ችግር እንዳይጋለጥ ባላንጣቸው የሆኑት የኤርትራ እና የአማራ ኃይሎች እንዳይወጓቸው የፌደራሉን ሥልጣን የሚይዘው ኃይል ማረጋገጥ አለበት የሚል ነበር። በዚህ ጉዳይ መግባበት ላይ ተደርሶ ሽግግሩ መጣ።

ከጅምሩ በለውጡ ሥልጣን የያዘው ቡድን ቃል የተገቡትን ዋስትናዎች ተግባራዊ ማድረጉ ላይ በትግራይ አመራር ዘንድ ሥጋት እና ጥርጣሬ የሚፈጥሩ እርምጃዎችን መውሰድ ጀመረ። ትላንት ለተፈጸሙ ጥፋቶች በይቅርታ እና በእርቅ የማለፍን አስፈላጊነት ከመስበክ ይልቅ አጋንኖ ማውገዝን መረጠ። ይባስ ብሎም ከኤርትራ ጋር በተደረገው የእርቅ ሂደት ውስጥ የትግራይ መሪዎችን አለማሳተፍ፡ እነሱን ለማጥቃት የተወጠነ የወታደራዊ ትብብር ግራ አድርገው እንዲረዱት በር ከፈተ። አንዳንድ የሕወሓት መሪዎችም ትላንት ባጠፉት ጥፋት ተጠያቂ እንዳይሆኑ በግላቸው ካላቸው ሥጋት በመነሳት የትግራይን ሕዝብ አንደ መደበቂያ ዋሻ በመጠቀም፡ አዲሱን የፌደራል አመራር ለማዳከም የወሰዷቸው እርምጃዎች ነገሮችን አባባሱ።

በዚህ መልኩ በትግራይ እና በፌደራል መንግሥት መካከል የነበረው ጥርጣሬ እና እሰጣ ገባ በሂደት አገረሸ። ይህን ሽኩቻ ከጠዋቱ ማብረድ ሲቻል የሁለቱም ወገን አመራርም ሆነ ሦስተኛ ወገኖች እያንዣበበ ያለውን አደጋ አቅልለው በማየታቸው አስፈላጊውን እርምጃ በጊዜ ሳይወስዱ ቀሩ። ወደ ሀገር ቤት እንደገባሁ ሰሞን ወደ ሠላሳ የሚሆኑ የአሜሪካ፣ የአውሮፓ እና የእስያ ሀገራት አምባሳደሮች በጋራ ስብሰባ አዘጋጅተው በጋበዙን ወቅት፡ በትግራይ እና በፌደራል መንግስታት መካከል እየሻከረ ያለውን ግንኙነት ጣልቃ በመግባት እንዲያቀራርቡ በአጽንዖት ተናግሬ ነበር።

በወቅቱ ብዙዎቹ ሥጋቴ የተጋነነ እንደሆነ በማሰብ አጣጣሉት። የአሜሪካ አምባሳደር የነበረው ሰው «ለዓመታት በግጭት ውስጥ ስለቆየሁ፡ አእምሮህ ሁሉም አለመግባባቶች ወደ ግጭት

እንደሚያመሩ ያስባል› በማለት ሥጋቴን አጣጣለው። በተጨማሪም መቀሌም ሆነ አዲስ አበባ ያሉት ባለሥልጣናት ለረጅም ጊዜ የሚተዋወቁ ስለሆኑ ያለማንም ጣልቃገብነት ልዩነታቸውን መፍታት እንደሚችሉ በእርግጠኝነት ተናገረ።

መጀመሪያ አካባቢ ለጠ/ሚኒስትር ዐቢይም ሆነ ለተለያዩ የሕወሓት ባለሰልጣናት ሥጋቴን ገለጬ ወደ እርቅ እንዲሄዱ በተደጋጋሚ ስወተውት፣ አደጋውን በጣም አሳንሰው ሊያሳምኑኝ ይሞክራሉ። ይህ ብቻ ሳይሆን ታረቁ የሚለውን ውትወታይን ወደ ጎን በመተው ሁለቱም ወገኖች ወደራሳቸው ጎራ ሊስቡኝ ይጥሩ ነበር። ከመታሰሬ ከጥቂት ወራት በፊት ከአንድ ከፍተኛ የሕወሓት አመራር ጋር አውሮፓ ውስጥ በተገናኘንበት ወቅት የጦርነት አደጋ ማንዣበቡን ቢያምንም የእኔን የእርቅ ውትወታ ከመቀበል ይልቅ ለማይቀረው ጦርነት አጋርነቴን ለማግኘት ወተወተኝ። ይህ ሰው ለወትሮው ከሌሎቹ የሕወሓት አመራር የተሻለ ለዘብተኛ መሆኑን ስለማውቅ፤ የእርቅ ሐሳቤን አጣጥሎ ጦረኝነትን ሊሰብከኝ መሞከሩ ተሰፋ አስቆረጠኝ።

ከትግራይም ሆነ ከፌደራል መንግሥት በኩል እያንዣበበ የነበረውን ጦርነት ለማስቀረት ጥረት ያደረጉ ግለሰቦች ነበሩ። ከጄኔራል ጻድቃን ገብረ ትንሳኤ እና ከአቶ ስዩ አብረሀ ጋር ባደረኳቸው ውይይቶች ልዩነትን በእርቅ ፈትቶ ጦርነትን ለማስቀረት. ቁርጠኛ አፈቋም እንዳላቸውና ሲተጉ እንደነበር መረዳት ችያለሁ። በዚህኛው ወገንም አቶ ለንጮ ለታአ እና አባዱላ ገመዳ በተመሳሳይ መልኩ ጦርነቱን ለማሰቀርት ጥረት ያደርጉ ነበር። ሆኖም ከሁለቱም ወገን ሰላም ፈላጊ የሆኑ ግለሰቦች ሥልጣን ላይ ስላልነበሩ ፍላጎታቸውን ወደ ፖለቲካዊ ውሳኔ መቀየር አልቻሉም። በሥልጣን ላይ የነበሩት ደግሞ ግማሹ ጦርነት ፈላጊ ሲሆን፣ ሌላው ደግሞ ቁርጠኛ አቋም መውሰድ አልቻለም።

በጦርነቱ ወቅትም ሆነ ከዚያ ወዲህ፣ ለግጭቱ መቀስቀስ ራስን ከደሙ ነጻ በማድረግ፣ በሌላው ላይ ጣት መቀሰር ይታያል። ሆኖም የፖለቲካ አለመግባባቱ ወደ ጦርነት ለማምራቱ፣ እንደ ሀገር መሪ ዋነኛው ተጠያቂነት የጠቅላይ ሚኒሰትሩ ቢሆንም፣ የሕወሓት አመራሮችም ከፍተኛ አስተዋጽኦ ማድረጋቸውን በቀጥታ የታዘብኩት ሀቅ ነው። በሕወሓት እና በፌደራሊዝም ጥላቻ የታወሩ የአማራ ልሂቃን የትግራይ እና የፌደራሉ ሽኩቻ እንዲፋፋም ቤንዚን ሲያርከፈክፉበት ነበር።

ሕወሓትን የመበቀል የረጅም ጊዜ እቅድ የነበረው የኤርትራ መንግሥትም ገና ከጠዋቱ ለፌደራል መንግሥት ወታደራዊ አጋርነት እንደሚሰጥ በመጠቆም የልብ ልብ እንዲሰማው አድርጓል። በሕዳሴው ግድብ ጉዳይ ጠቅላይ ሚኒሰትሩ እንደከዷቸው የተሰማቸው የውጭ ኃይሎችም፡ ለትግራይን አመራሮች አይዞህባይ በመሆን ወደ ጦርነት እንዲገቡገፋፍተዋቸዋል። ይህ ሁሉ ተደማምሮ በውይይት እና በድርድር ሊፈታ ይችል የነበረ ቁርሾ አመርቅዞ ሁሉንም ወገን ለከፋ ሰብዓዊ፣ ፖለቲካዊ እና ኢኮኖሚያዊ ኪሳራ ወደዳረገ ጦርነት አገባ። የኮሮና ወረርሽኝን ተከትሉ የፌደራል መንግሥት ምርጫውን ለማራዘም ሲወስን፤ የትግራይ ክልል ግን ምርጫውን ለማካሄድ በመወሰኑ በሁሉቱም በኩል የሚዲያ ውግዘቱ በይፋ ታወጀ። ለቀጣይ ጦርነት ጦር ማጠናከር እና ጥምረት መፍጠር ተጧጧፈ። የፌደራል ፖሊስ አስር ቤት እያለሁ አንድ የመንግሥት ባለሥልጣን ሊያናግረኝ መጥቶ «በቅርቡ ከትግራይ ጋር ወደ ጦርነት

ትገባላችሁ፤ እኛም የዚያኔ ከምታደርጉብን ፕሮፓጋንዳ ተንፈስ እንላለን» ብዬ ቀለድኩበት። ባለሥልጣኑም «አንተ አሁንም የምታስበው ስለ ጦርነት እና ብጥብጥ ነው። ሀገሪቷ ሰላም ናት። ትግራይ በአፍ እንጂ በተግባር ጦርነት አትጀምርም›› አለኝ። እኔም «ታያለሀ ጠብቅ። በዛ ከተባለ በጥቂት ወራት ውስጥ ጦርነት ይፈነዳል›› አልኩት። ወቅቱ ነሐሴ 2012 ዓ.ም ነበር።
ወደ ቃሊቲ ከተወሰድን በኋላ ነገሮች እየተባባሱ መምጣታቸውን እና ጦርነት ሊፈነዳ ጫፍ ላይ መድረሱን በሁለቱም ወገን በሚዲያ ከሚተላለፈው ፕሮፓጋንዳ እየተረዳን መጣን። ጦርነቱ ከመጀመሩ ጥቂት ቀናት ቀደም ብሎ ወደ ፍርድ ቤት ስንወሰድ በመንገድ ላይ አደጋ ሊደርስብን ስለሚችል እንድንቀር ከጸጥታ አካላት በምስጢር መልዕክት ደረሰን። በእኛ ላይ አደጋ በመጣል ጦርነቱን ለማስጀመር መታሰቡንም ሰማን። በማግሰቱ ፍርድ ቤት እንድንሄድ ሲነገረን ሁኔታው ኣስቀድሞ ካገኘነው መረጃ ጋር ተዳምሮ ጥርጣሬያችን አናረው።

በማረሚያ ቤቱ ውስጥ ያሉት የጸጥታ አካላት ስለታዘዙ እንጂ በመሄዳችን ደስተኛ እንዳልሆኑ ሹክ አሉን። ከዚያ በፊትም ፍርድ ቤት ሲያቀርቡን ሴራ እንዳለ ሲነግሩን ነበር። ከዚህ በመነሳት «በደኅንነት ሥጋት ምክንያት ፍርድ ቤት መሄድ አንፈልግም። አንድ ነገር ቢደርሰብን ጦርነት አፋፍ ላይ ለደረሰች ሀገር ሌላ አደጋ ይፈጥራል» በማለት ለፍርድ ቤት ደብዳቤ ጽፈን ቀረን፣ ዳኞቹም ተረዱን። በማግስቱ በወለጋ የአማራ ተወላጆች በጅምላ መገዳለቸውን ሚዲያዎች እየተቀበሉ ዘገቡ። በፓርላማ ስብሰባ ላይ አባላቱ ቁጣ እና ለቅሶ ሲያሰሙ የሚያሳይ ቪዲዮ በመንግሥት ሚዲያ ሲተላለፍ ስናይ በጦርነት ዋዜማ ላይ መሆናችንን አርግጠኛ ሆንን።

ጥቅምት25 ቀን 2013ዓ.ም ዓ.ም አንድ ምሽት እንቅልፍ እምቢብሎን ከበቀለ ጋር ቴሌቪዥን እያየን እያለ በመሀል ጠ/ሚኒስትር ዐቢይ አሕመድ ብቅ ብሎ መናገር ጀመረ። ከዚያ በፊት በቴሌቪዥን ተደጋግሞ የሚቀርበው ፀረ-ሕወሓት የፕሮፓጋንዳ ፤ዶክመንተሪ ስለነበር የጠ/ ሚኒስትር ዐቢይም ንግግር የዚያው አካል መስሎን ነበር። ነገር ግን ከጥቂት ደቂቃዎች በኃላ እንደገና ደገሙት። በአንክሮ ስናዳምጥ ጠቅላይ ሚኒስትሩ የሀገር መከላከያ ሠራዊት የሰሜን ዕዝ በሕወሓት ኃይል ጥቃት እንደደረሰበት" ገልጸው ጦርነት አወጁ። የዚያን ሌሊት በላያችን ላይ የሚያልፉ የአውሮፕላኖች ድምጽ ስንሰማ አደርን። ልናስቀረው ብዙ ጥረት ያደረግነው ጦርነት በዚሁ ሁኔታ እንደፈነዳ አወቅን።

ጦርንቱ በፈነዳ በጥቂት ቀናት ውሰጥ አንድ በእኔ እና በመንግሥት መካከል መልዕክት ሲያመላልስ የነበረ ግለሰብ መጣ። «ወያኔ ተመልሶ ሥልጣን ለመያዝ ጦርነት ከፍቷል። ትላንት እንዳባረርካቸው አሁንም መንግሥትን አግዝ› አለኝ። «ይህ ጦርነት እንዳይመጣ ምን ያህል እንደለፋሁ ታውቃለህ።

ዛሬም ቢሆን የዚህ ጦርነት አካል መሆን አልፈልግም!» አልኩት። «ሰውዬውም ምን ትመክረናለህ?» ሲለኝ፤ «ወደ ጦርነቱ ከገባችሁ አይቀር የወሰዱትን መሣሪያ በአስቸኳይ አውድማችሁ ከትግራይ ውጡ።

በአንድ ወር ውሰጥ ካልወጣችሁ የሽምቅ ውጊያ ይጀምራሉ፡ ከዚያም እዚያው ያስሯችኋል። ወታደራዊ ኪሳራ ብቻ ሳይሆን ከባድ የዲፕሎማሲ ጫናም ሊያጋጥምችሁ ይችላል። ክልሉ የህዳጣን ስለሆነ የተራዘመ ጦርነት የሚያስከትለውን ቀውስ ዓለም ዝም ብሎ አይመለከትም» አልኩት።

ጦርነቱ በማይታመን ፍጥነት ተጋግሎ በሦስት ሳምንታት ውስጥ የፌደራሉ መንግሥት መቀሌን ተቆጣጥሮ ድሉን አበሰረ። ጠቅላይ ሚኒስትሩ ወደ መቀሌ ሄዶ እንደተመለሰ፡ ፓርላማ ላይ በመቅረብ አንፀባራቂ ድል መቀዳጀታቸውን አሳወቀ። ንግግሩን ስመለከት የቀድሞ የአሜሪካ ፕሬዝዳንት ጆርጅ ቡሽ (65695 ጅሀ5እ) ኢራቅን በወረረበት ወቅት፤ ሠራዊታቸው ሳዳም ሁሴንን አባሮ ባግዳድን ሲይዝ መርከብ ላይ ወጥቶ ግርይይ205 እርርዐመ115ከዳፇ (ተልዕኮው በድል ተጠናቋል) "በማለት ያወጀውንአስታወሰኝ።ፕሬዘዳንቱ ድል ማድረጋቸውን ቢያውጁም የኢራቅ ጦርነት ግን ከዚያ በኋላ ተባብሶ፣ የአሜሪካ ጦር ለስምንት ዓመታት ተዋግቶ ሲያቅተው ጥሎ ወጥቷል።

ከጠ/ሚኒስትር ዐቢይ የድል መግለጫ በፊት አንድ ጽሑፍ ጽፌ በድብቅ በማስወጣት አጋራሁ። በዚህ ጽሑፍ የሽግግር ፖለቲካን በአግባቡ አለመምራት ወደዚኅ ጦርነት እንዴት እንዳመራን በመተንተን፡ በፍጥነት ካልቆመ የተራዘመ ጦርነት እና ብሔራዊ ኪሳራ የሚያደርስ እንደሆነ አስጠንቅቄያለሁ። ጠ/ሚኒስትር ዐቢይ የትግራይን ጦርነት ማሸነፉን ካወጀ ከጥቂት ቀናት በኋላ፡ መልዕክት አመላላሹ ሰው መጥቶ ያሰተምኩትን ጽሑፍ በመተቸት «አየሀ አይደል ወያኔን ያለናንተ እርዳታ አየር ላይ የተበተነ ዱቄት አደረግናት›; በማለት ጠቅላይ ሚኒስትሩ ፓርላማ ላይ የተጠቀሙትን ቃል ተውሶ ተመፃደቀብኝ። ፡-

እንኳን ደስ አለህ፡ እኔ እንደማየው ግን የተጠናቀቀው የመጀመሪያ ምዕራፍ ነው፤ ሁለተኛው ምዕራፍ አሁንመጀመሩ ነው። አኔአናንተንብሆንኖሮከወያኔጋር ድርድር (7292:3520፡) አድርጌ በፍጥነት ከክልሉ-አወጣ ነበር» አልኩት። «እሁንም ወያኔ ከሞት ይነሳል ብለሀ ትፈራለሀ? አልቋል አኮ፡ ሰለሞቱት መሪዎች እና ጀኔራሎች በሚዲያ አትሰማም?" ሲለኝ፤ «አሰማለሁ፣ ግን ጉዳዩ የሕወሓት ሳይሆን የትግራይ ብሔርተኝነት ጉዳይ ነው። አመራሩን መጨረሰ እንዲሁም ድርጅቱን ማፍረሰ ይቻል ይሆናል።

ብሔርተንነትን ግን መሰበር አይቻልም። በተለይ በሁሉም ድንበር በጠላቶች ተከብቤቢያለሁ ብሉ በማሰብ የኅልውና ሥጋት (2ይ :151 ፓአፓጳ3) የሚሰማውን የሀዳጣን ቡድን ብሔርተንንት መሰበር ከባድ ይመሰለኛል። ከዚሀም በተጨማሪ ሕወሓት የአርባ አምስት ዓመት ወታደራዊ ልምድ እና ዲፐሎማሲያዊ ግንኙነት አላቸው። ለጊዜው በቀላሉ ሰለተሸነፉ የሚጠፉ አይመሰለኝም› ብዬው ተለያየን።

ከዚያም ከአዲሰ አበባ የተያዙ እና ከጦር ሜዳ የተማረኩትን የትግራይ የፖለቲካ እና ወታደራዊ ባለሥልጣናትን ወደ ቃሊቲ አሰር ቤት አመጧቸው። ጠባቂዎቹ ወዳሉበት ግቢ ሊወሰዷቸው እንደሆነ አሰቀድመን ሰለሰማን ልጆቹ በአክብሮት እንዲቀበሏቸው መከርናቸው። ይሀንን ያደረግነው በሰብዓዊ ርሀራሄ ብቻ አልነበረም። አነዚሀ የትግራይ አመራሮች ሥልጣን ላይ በነበሩበት ወቅት በሕዝባችን ላይ ከፍተኛ ጉዳት ሲያደርሱ እንደነበር ይታወቃል። ከእኛ ጋር አሰር ቤት ከነበሩት ልጆች መካከል ሳይቀር ከሚመጡት ባለሥልጣናት አንዱ እግሩን ሰብሮታል። በወቅቱግን የአስር ተራ ፅለደረሳቸው እነርሱን በመጉዳት መበቀል ሳይሆን በልጠን በመንኝት ከእነርሱ የተሻልን መሆናችንን ማሳየት አለብን ብለን ነው።

ምሽት ላይ አምጥተው ሰላሰገቧቸው የእኛ ልጆች ከአልጋ ወርደው በታቸውን ለአዛውንቶች ለቀው አሰተኗቸው፡የነበራቸውንም ምግብ ሰጧቸው። በማግሰቱ የማረሚያ ቤቱን አሥተዳደር ጠርተን «አነዚሀን ባለሥልጣናት የትላንት ወንጀላቸውን አይታችሁ አትችጉዷቸው። በጣም

ጥሩው ቅጣት ከእነሱ ተሽሎ መገኘት ነው። ትልቁ ቅጣት የኅሊና ነው። ከእነዚህ ባለሥልጣናት መካከል አንዳንዶቹ በዕድሜ የገፉ ስለሆኑ ከመጉዳት መንከባከቡ በፈጣሪ ዘንድም የተወደደ ነውን በማለት አሳመንናቸው።

የእነዚህ ባለሥልጣናት መምጣት ስለ ጦርነቱ ሁኔታ የተሻለ መረጃ እንድናገኝ ረዳን። እኛ እና እነርሱ የታሰርንበት ግቢ የተለያየ በመሆኑ በአካል መገናኘት ባንችልም በደብዳቤ እና በሰው መረጃ በመለዋወጥ ግንዛቤ ለማግኘት ችለናል። አብዛኛቹ ዕድሜያቸው ገፍቶ እና በጦርነቱ ወቅት በረሃ ውስጥ ተጎድተው ስለነበር፡ እኛ ጋር የሚመጡ ሰዎች አስፈላጊውን ምግብ እና ልብስ እንዲያደርሱላቸው አደረግን። እኛ ከየግል ቤታችን በየቀኑ ምግብ እንድንቀበል በፍርድ ቤት ተፈቅደልን ይገባልን ስለነበረ፡ እነሱም ፍርድ ቤቱን ጠይቀው እንዲፈቀድላቸው መከርን። የእስር ቤቱ አሥተዳደር ለእኛ የፈቀዱልንን መብቶች ሁሉ በርሀራሄ እንዲፈቅዱላቸውም ተማጸንን።

መንግሥት በአጭር ጊዜ ውስጥ እንዲያልቅ የፈለገው የትግራይ ጦርነት መቀሌን በመያዝ ብቻ ሊያበቃ አልቻለም። መከላከያ መቀሌን በያዘ በወራት ጊዜ ውስጥ የሽምቅ ውጊያ እየተጠናከረ መጣ። ከፍተኛ ጦርነት እየተካሄደ እንዳለ የመንግሥት ሚዲያዎች ቢደብቁም ከትግራይ እስረኞቾች ቤተሰብ እና በቦታው ኣሉ የእርዳታ ድርጅቶች መረጃ እናገኝ ነበር። አንድ ቀን በእኔ እና 6መጋ/ጭ መካከል መልረጋፔት የሚያመላልሰው ሰው ተመልሶ መጣ። «ትግራይ ፓለትያትን ሁኔታ ታውቃለህ?» ሰለው፡ «አሁን ሰላም ወርዷል ብዙ የሕወሓት ባለሥልጣናት ሞተው አንዳንዶቹም ጠፍተዋል» እዕን፡ ፲ ሯዐፀትና «እኔ ያሰጠነቀኩህ የሽምቅ ውጊያ ተደምጀል። ከዓለም አቀፉ ማኅበረሰብም ጠንካራ ድጋፍ እያገኙ ነው። እዚያ ያለውን የሀገር መከላከያ ሠራዊት አዳክመዋል። በዘ ከተባለ ከሦስት እስከ ሰድሰት ወራት ውስጥ መቀሌን መልሰው መያዝ ይችላሉጋ አልኩት። እሱ ግን «በጭራሽ የሚቻል ነገር አይደለም › ሲለኝ፤ «እሺ አብረን እናያለን› ብዬው ተለያየን። ሰለዚህ ጉዳይ ያወራነው በግንቦት 2013 ዓ.ም መጀመሪያ ላይ ነበር።

የትግራይ ጦር ከገመችኩት ጊዜ ቀደም ብሎ በሰኔ ወር መቀሌን ተቆጣጥሮ፣ ወደ ወሎ እና አፋር ክልሎች ድንበር ዘልቆ ገባ። አሁንም ሰውይው ተመልሶ መጥቶ «አንተ እንዳልከው ሰዎቹ ጠንክረው መጥተዋል። ፊንፊኔን ለመያዝ ይፈልጋሉ። ትላንት ያባረርከው ጠላት እንደገና ተመልሶ ሥልጣን ለመያዝ ሲመጣ እንደት ዝም ትላለህን» አለኝ። «አሁንም ቢሆን መፍትሔው በድርድር ሰላም ማስፈን ነው› አልኩት።

እርሱም «እነርሱ በሰላም መፍታች አይፈልጉም። ቄሮ ተነሰቶ ወደ ሠራዊቱ በመቀላቀል መከላከል አለበት(› ሲል ተናገረ። «የትኛው ቄሮ? የገደላችሁት? ያሰራችሁት ነው? ወይስ ወደ ጫካ ያሰገባችሁት?» በማለት አከታትቶ በጥያቄ መለሰኩለት። አክይም «አሁን በዚህ ጦርነት ውስጥ ቄሮም ሆነ የኦሮሞ ሕዝብ መግባቱ ምንም ፋይዳ የለውም። በሰላም ፍቱት። በሰላም ለመፍታት ዝግጁ ከሆናችሁ በቻልኩት ሁሉ ለመርዳት ዝግጁ ነኝ» ሰለው አቋሜን ሰምቶ መልስ ሳይሰጠኝ ሄደ።

ጦርነቱ እየተባባሰ ሄይ ደሴ ከተማ በትግራይ ኃይሎች ቁጥጥር ሥር ወደቀች። አሁንም ሰውዬው መጥቶ ነገሮች መባባሳቸውን፡ ሥልጣን ከኦሮሞ እጅ ሊወጣ እንደሆነ እና ሀገርም እንደምትፈርስ ተናገረ። «ምን ይሻላል?» ሰለው፡ «መንግሥት ከአሰር ይልቀቅሀ፣ ሥልጣንም

ይሰጡሃል ውጣና አግዝ› አለኝ።

እኔ ደግሞ «መታሰሬ ፈጣሪ በዚሀ ጦርነት እንዳልሳተፍ ሊያተርፈኝ ፈልጎ ነው። አሁንም መሳተፍ አልፈልግም። መፍትሔው በሰላም መፍታት ብቻ ነውጋ አልኩት፣ ብዙ ሊያሳጎምነኝ ቢሞክርም አልሳካ ሲለው ተመልሶ ሄደ።

ጦርነቱ ወደመዲናዋ እየተቃረበ ሲመጣ መንግሥት ብቻ ሳይሆን አንዳንድ የትግራይ አመራር እና የዓለም አቀፍ ማኅበርሰብ (ፓይር52ኻ5520551. ርርመመ 5157) ተወካዮችም በመልዕክተኛ ያወያዩኝ ጀመር። የዓለም አቀፍ ማኅበረሰብ ተወካዮች ጦርነቱ ወዴት ሊያመራ እንደሚችል እና ቀጥሎ ምን ሊከሰት እንደሚችል ጠይቀውን ሐሳቤን አቀረብኩላቸውጸ ነገሩ በድርድር ካልተቋጨ የትኛውም ወንን ቢያሸንፍ የሀገር መፍረዕ አደጋ ሊመጣ እንደሚችል በትንተና አዕደግፌ ገለጽኩላቸው።

ከትግራይ አመራሮች ጋር ባደረኩት የሀሳብ ልውውጥ እና ከሌሎች ምንጮች ከማገኘው መረጃ በመንሳት፤ምንም አንኳን ውጊያው ላይ በአልሀ እና በወታደራዊ ልምዳቸው የበላይነት እያገኙ ቢመጡም፡ የፖለቲካ አቅድ እንደሌላቸው ተረድቻለሁ። ጦርነቱን አሸንፈው ፊንፊኔን ቢይዙ አንኳን ቀጥሎ ማድረግ ባለባቸው ነገር ላይ እንዳላሰቡበት እና እንዳልተዘጋጁበት ተረዳሁ። በ2583 ዓ.ም ደርግን ሲያሸንፉ የተገበሩትን በ2013 ዓ.ም ለመድገም ምኞት ቢኖራቸውም፤ ከ3983ቱ ጋር የሚመጣጠን አቅድ፣ ሰትራቴጂ፣ አደረጃጆች እና አመራር እንደሌላቸው ግልጽ ሆነልኝ። በሌላ አነጋገር አሸንፈው ፊንፊኔ ቢገቡ አንኳን ሀገር አረጋግቶ ለማሰተደዳር የሚያበቃ ቆመና እንደሌላቸው ግልጽ ነበር። :

በ3983 የደርግን መንግሥት መጣል ብቻ ሳይሆን መላ ሀገሪቱን ተቆጣጥሮ ጸጥታ ማሰከበር የሚችል ጠንካራ ሠራዊት ከመገንባት ባለፈ፡ ሥልጣን ከመያዛቸው በፊት ክልላቸውን ጨምሮ ሌሎችንም ለማሥተዳደር ብቃት ያለው ጠንካራ ፓርቲ አደራጅተዋል። በወቅቱ ሲመጡ በመለሰ መሪነት ጠለቅ ያለ አውቀት፡ አንደነት እና ልምድ ያለው ሰትራቴጂክ አመራር ይዘዋል። በአንጻሩ በ2033 ጦርነት ወቅት ግን የትግራይ ኃይሎች ያላቸው ፓርቲ ሕዝቡን ለሀያ ሰባት ዓመታት ያሰለቸ እና አርድቶ ውሰጡ የተበረበረ ነበር። ሠራዊታቸው ተሞክሮ ባለው አመራር እና በተቆጡ አባላት ታግዞ ድል እየተጎናጸፈ ቢመጣም፡ በአንድነት፡ በሥነ-ምግባር አና በበሳል ፖለቲካ እየተመራ አንዳልሆነ ግልጽ ነበር።

ከአንዳንድ የትግራይ አመራሮች ጋር ሳደርግ በነበረው ውይይት ከላይ ያሰቀመጥኩትን ግምት ያጠናከረ ግንዛቤ አገኘሁ። ለምሳሌ «ፊንፊኔ ሰትደርሱ ምን ታደርጋላችሁ?» ለሚለው ጥያቄ አርሰ በአርሰ የማጋጩ እና ተለዋዋጭ መልሶችን ያቀርባሉ። መጀመሪያ «ፊንፊኔ መግባት አንፈልግም› ሲሉ ቆይተው፡ ደሴ ከደረሱ በኋላ «የሽግግር መንግሥት እንመሠርታለን› አሉ። በወቅቱ በውጪ የሚኖሩ ኦሮሞዎች አዘጋጁት የተባለውን የሽግግር መንግሥት ረቂቅ አንድ የትግራይ አመራር ልኮልኝ ሐሳቤን እንድሰጥበት ጠየቀን። እኔ ግን በረቂቁ ላይ አሰተያየት ከመስጠት ይልቅ፣ የሕወሓትን እቅድ እና ምኞች በቀጥታ ማወቅ ሰለፈለኩ፡ ራሳቸው ያዘጋጁት

ረቂቅ ካለ እንዲልኩልኝ ሰጠይቅቅ አንደሌላቸው ነገሩን። ለሽሽግር ወሳኝ የሆኑ ነጥቦችን ያካተተ የሽግግር ረቂቅ አዘጋጅቹ በመላክ የእነርሱን አቋም መገንዘብ ፈለኩኝ።

ባቀረብኳቸው ብዙ ነጥቦች ቢሰማሙም፣ ቀደም ብይ አንደጠረጠርኩት አንዳንድ ጠንከር ያሉ ጉዳዮችን ለመቀበል ፈቃደኛ አልሆኑም። ከአነዚህ ጉዳዮች መካከል አንዱ የሀገር መከላከያ ሠራዊት ጉዳይ ሲሆን፣ አሁን ያለው የሀገር መከላከያ ሠራዊት መጠነኛ ተሃድሶ ተደርጎለት

አንዲቀጥል ሐሳብ ጎቀርብ፣ አነሱ ግን አልተቀበሉትም።

"የጦር ወንጀል የፈጸመ ሠራዊት ሰለሆነ መበተን አለበት" የሚል አቋም አንጸበረቁ። ነባሩን መከላከያ መበተን በሁለት ምክንያቶች በአኛ በኩል ተቀባይነት አንደሌለው ነገርአቸው። የመጀመሪያው፡ የዓመታት ልምድ ያለው ወታደራዊ ተቋም አፍርሶ አዲስ ለመገንባት መሞከር የካበተ ተቋማዊ ልምድ፡ አውቀት አና ድርጅታዊ ባሕልን ማጣክን ነው።

ለምሳሌ ደርግ ሲወድቅ ነባሩ የኢትዮጵያ ጦር ሙሉ በሙሉ በመፍረሱ ከዚያ ተቋም ጋር የሚሰተካከል ወታደራዊ ተቋም ለመገንባት ረጅም ዓመታትን ወሰዷል። የፖለቲካ ለውጥ በማጣ ቁጥር ነባሩን ጦር እያፈረሱ በአዲስ ለመተካት መሞከር የሀገር ግንባታ (25105 ጅህ3141ጮ59) ሂደትን የሚጎትት ሰለሆነ አሁን ያለውን ጦር ከማፍረሰ ማደዕ ይሻላል የሚል ነበር አቋሜ።

ሁለተኛው ምክንያት፡ አሁን ያለውን ሠራዊት አናፈርሳለን ማለት ልክ አንደ 1583 ዓ.ም የአንድ ቡድን ጦር ሀገራዊ አድርጎ ወደማቅረብ ያመራል። ይሀ ደግሞ በብሔሮች መካከል ያለውን የኃይል ሚዛን በማፋለስ፣ በጦሩ ውኃጥ ኋ በፖለቲካው የአንድን ቡድን የበላይነት መልሶ ያመጣል።

ከ1583 ዓ.ም በኋላ አንደተደረገው ነባር መኮንኖች ከተበተኑ በኋላ፣ የይሰሙላ ብዝንሳነትን ለማሳያት ሲባል፡የሕዝብ ውግንናአናየውትድርናልምድ የሌላቸውን ሰዎች ከመሬት አንሰተው ፀፍተኖ ወታደራዊ ባለሥልጣን አድርገው ለመሾም አቅደው ይሆናል ብዬ ጠረጠርኩ።

አሁን ያለው የሀገር መከላከያ ሠራዊት ቢከፋም ቢለማም ከ2038 በኋላ በተደረገው ተሃድሶ በተወሰነ መልኩ ብዝሳነትን ማንፀባረቅ ችሏል። በአንድ ጦር ኃይል ውሰጥ የመካከለኛ ደረጃ መኮንኖች ዐፊ-ጸ35፡ ዐደደቷሪ5ፓ5) ለማብቃት ቢያንሰ ሁለት አሥርት ዓመታትን ይፈጃል። አሁን ያለው ሠራዊት ፈረሰ ማለት፣ ኦሮሞ እና ሌሎች ብሔሮች አንደ ትግራይ የረጅም ጊዜ ልምድ ያካበቱ መኮንኖች ካሏቸው ቡድኖች ጋር ለመመጣጠን ከሀያ ዓመታት በላይ ይፈጅባቸዋል ማለት ነው። በአነዚሀ ዓመታት ውሰጥ ይሀ ወታደራዊ የበላይነት ለሀያ ሰባት ዓመታት ያየነውን የፖለቲካ አና የኢኮኖሚ የበላይነት መልሶ ሊያመጣ ይችላል ብዬ ተከራከርኳቸው። በአነርሱ ወገን ከባድ ወንጀል ያልፈጸሙ መኮንኖችን ማቆየት አንደሚቻል ቢገልጹም ለአኔ አጥጋቢ መልሰ አልነበረም።

በአነዚሀ አና በሌሎች ጉዳዮች ላይ አየተወያየን አያለ የጦር ሜዳው ሁኔታ ተለዋወጠ። የትግራይ ጦር ድል አየቀናው ወደ መዲናዋ አየተጠጋ በሄደ ቁጥር፡ አመራሮቻቸው በሚዲያ የሚያሰተላልፏቸው መልክአዕቶች የአብሪት አና የበቀል ይዘታቸው አየጨመረ ሄደ። "ክማን ጋር ነው የምንደራደረው"፤፤ "ሂሳብ አናወራርዳለን።። ወዘተ የሚሉት አባባሎች፣ ቀንቷቸው መንግሥትን ቢገለብጡ፡ሀገሪቷ ወደባሰ ቀውሰ ልትገባ አንደዎችችል የነበረኝን ሥጋት የበለጠ

አጠናከረው። ይሀንን የአደጋ ሥጋት ለሚመለከታቸው የዓለም አቀፍ ማኅበረሰብ አካላት አሳወኩ።
ከዲፕሎማቶች እና ከትግራይ አመራሮች ጋር አያደረኩ የነበረውን ውይይት በወቅቱ አሜሪካን በመኅብንትላይ ለነበሩትፕሮፌሰር መረራ አያሳወቅኩ ቀጠልኩበት። በተጨማሪም የነበረውን ውይይት ጭብጥ ለተወሰኑ ምሁራን፡ የሲቪል እና ወታደራዊ ባለሥልጣናት በተዘዋዋሪ በማጋራት አዕተያየታቸውን ሰቀበል ነበር። ከኦሮሞ ምሁራን እና አመራሮች የማገኘውን ግብረ መልስ በመጠቀም አየተካሄደ ስላለው ጦርነት እና በድሀረ-ጦርነት ወቅት ሊኖር ሰለሚችል

ፓለቲካዊ ሁኔታ የኦሮሞ አቋም ምን አንደሆነ ለዲፕሎማቶቹ ገለጽኩ።

የትግራይ ጦር ደሴን አልፎ ሸዋ ሮቢትን ሲቆጣጠር፡ የመንግሥት መልዕክተኛው ሰው መጥቶ ነገሮች በፍጥነት አየተበላሹ መሆናቸውን፣ ቢያንሰ ወደ ኦሮሚያ እንዳይገቡ መከላከል እንደሚያፅፈልግ እና ለዚሀም ዝግጅት አየተደረገ መሆኑን ነገረኝ። በተጨማሪም ከአሰር ወጥቼ ከፈለኩ የኦሮሚያ ፕሬዝዳንትነች ወይም በፌደራል ደረጃ የምፈልገውን ሥልጣን ይሄ ሕዝቡን በማነሳሳት ኦሮሚያን በመከላከል አንድሳተፍ ጠየቀኝ። ከበፊቱ አቋሜ ፍንክች አላልኩም። በተጣዮቹ ተናች ሌሎችም መጥተው ይሀንኑ ተማጸኑን። በፌደራል መንግሥት እና በትግራይ ክልል መካከል ያለው የአርዕ በአርዕ ጦርነት በድርድር አንዲቋጭ የበኩሌን ሚና ለመጫወት ዝግጁ መሆንን ገልጬ ከየትኛውም አካል ጎን ቆሜ ሕዝቡን በጦርነት መማገድ አንደማልፈልግ አቅጨን ነገርአቸው። ሰወጣም ከመንግሥት ጋር አብረ በሚነደው አሳት ላይ ጋዝ አንደማላርከፈክፍ ተናገሪ በአቋሜ ጸናሁ።

ይህ በእንዲሀ አንዳለ የትግራይ ጦር ወደኋላ አየተመለሰ እንደሆነ ከደኅንነት እና ከዲፕሎማሲ ምንጮች መረጃ ደረሰኝ። ቀጥሎም ጠቅላይ ሚኒሰትሩ በቴሌቪዥን ቀርቦ ወደ ጦር ሜዳ አንደሚሄድ ተናገረ። የትግራይ ጦር ፊንፊኔን መያዙ ቀርቶ፣ ግጭቱን በድርድር የመፍታት ዕድል ተከፈተ።

# ክፍል አስራ አንድ - ከእስር ቤት መልስ
# 11.1. ከእስር መፈታት

ከታሰርንበት ቀን ጀምሮ በሕይወት ከተረፍን ከምርጫው በኋላ እንደምንፈታ ገምቼ ነበር። የመረጃ ጥንቅራችንም ይሀንኑ ጠቆመን። አንድ ቀን ጠቅላይ ሚኒስትሩ ከፕሮፌሰር መረራ ጉዲና ጋር ሲገናኙ፣ «ከእነ ጀዋር በስተቀር ሁሉንም የፖለቲካ አሰረኞች እንፈታለንን› በማለት ምርጫው ውስጥ እንዲገቡ ለማሳመን ሞከረ። ፕሮፌሰር መረራ ግን እኛ ካልተፈታን ወደ ምርጫ እንደማይገቡ ቁርጡን ተናገረ። ይሀ የጠቅላይ ሚኒስትሩ እና የፕሮፌሰር መረራ የቃለት ልውውጥ ከምርጫው በፊት እንደማንፈታ ጥርጣሪያችንን አረጋገጠልን።

ባለፈው ምዕራፍ ላይ እንደተገለጸው የትግራይ ጦር ተጠናክሮ ወደ ፊንፊኔ በገፋ ቁጥር፣ የመንግሥት ባለሥልጣናት ወጥቼ የምረዳቸው ከሆነ እንደሚፈቱኝ ሲያመለክቱ ነበር። "ከወጣ ይዞርብናል የሚል መክከራከሪያ በማቅረብ የተቃወሙ አንደነበሩ ሁሉ፡ የእኔ መለቀቅ ለመንግሥት እንደሚጠቅም በማውሳት ለከፍተኛ ባለሥልጣናት ተማጽኖ የሚያቀርቡ የገገርው ፓርቲ ደጋፊዎች እንደነበሩም ሰሰማ ነበር። ለመፈታት መቃረቤ መረጃ መሰራጨት ሲጀምር፣ ከዚሀ ቀደም በመታሰሬ ደሰታቸውን ሲገልጹ የነበሩ ሰዎች ሳይቀር፡ አንዳንዶቹ ሊጠይቁኝ ሲመጡ ሌሎቹ ደግሞ መልዕክት በመላክ ያበረታቱኝ ጀመር።

የትግራይ ጦር ወደ ፊንፊኔ አየተቃረበ ሲመጣ አደጋ ይደርሰባችኋል የሚለው ሥጋትም እንዲሁ ጨመረ። ቤተሰቦቻችንን ጨምሮ፣ የውጭ መንግሥታች እና የመንግሥት አካላት ጥርጣሬያቸውን መግለጽ ጀመሩ። በማኅበራዊ ሚዲያ ላይ' ይሀ ወይም ያ ቡድን እነሱን ለማጥቃት አየተዘጋጀ ነው' የሚል ሀሜት ተበራከተ። የትግራይ ኃይሎች ወደ ኤርትራውያን ጣታቸውን ይቀሥራሉ። መንግሥት በበኩሉ ”ወያኔ" እና "ኔ አደጋ ሊያደርሱ ይችላሉ ይላል። እኛም ጥቃቱ ከየትም ይምጣ ተጋላጭነታችንን ለመቀነሰ ፍርድ ቤት ከመቅረብ ታቀብን። ፍርድ ቤት ነገሩን ተረድቶ እኛ በሌለንበት ጉናያችን እንዲታይ ወሰነ። በሕጉ መሠረቻ ተከሳሹ በሌለበት ጉዳዩ አይታይም። እኛ ግን አሰር ቤት ነበርን። አቃቤ ሕግ ይሀን ሕግ በማጣቀስ በግድ ወደ ፍርድ ቤት እንደንቀርብ ችሎቱን ጠየቀ። ጉዳያችንን የሚመለከቱ ዳኞች ግን ሥጋታችንን ተረድተው እንዳንቀርብ ወሰኑ።

ጦርነቱ አየተቃረበ መጥቶ ሸዋ ሮቢት ሰትያዝ፣ በአካባቢው የነበሩት የፌደራል ማረሚያ ቤት እሰረኞች ወደ ሌላ ቦታ መዛወራቸው ተሰማ፡ይሀን ተከትሉ የአሰር ቤቱን ኮሚሽነሮች ጠርተን ሰለደኅንነታችን አወያየናቸው። ሊደርሱብን ሰለሚችሉ የተለያዩ ጥቃቶች የሚወራውን

ገልጸንላቸው፣ በተለይ ጦርነቱ ወደ ፊንፊኔ በተቃረበ ቁጥር የተለያዩ ኃይሎች በእኛ ላይ አደጋ በመጣል ሁኔታዎችን ሊያባብሱ ስለሚችሉ ደኅንነታችንን ለማረጋገጥ ምን ዓይነት ዝግጅት እንዳላቸው ጠየቅን። እነርሱ ግን ጉዳዩን ቀለል አድርገው እንደሚመለከቱት ሰለተረዳን «አንድ ችግር ቢደርስብን ተጠያቂዎቹ እናንተ ፊትለፊታችን የምትገኙት እንደሆናችሁ ሕዝቡ ያውቃል። ይህ ደግሞ ለራሳችሁ ብቻ ሳይሆን ለቤተሰቦቻችሁም አደጋ አለው, በማለት አሰፈራራናቸው። ከዚያ በኋላ ለጉዳዩ ከፍተኛ ትኩረት መሰጠት ጀመሩ። በየጊዜው መረጃ አየተለዋወጥን ምናልባት ጦርነቱ ወደ ከተማ ከቀረበ መወሰድ ባለበት አርምጃ ላይ የጋራ አቅድ አወጣን። ኮሚሽነሮቹ ጥበቃውን ከማጠናከር አልፈው ራሳቸውም ግቢው ውሰጥ ማደር ጀመሩ። በተለይም ድሪባ የሚባል የቃሊቲ ጥበቃ ኃላፊ እና ምክትል ኮሚሽነር ሙላት ቃሊቲ ጠቅልለው በመግባት ጥበቃችንን በቀጥታ ሲያሰተባብሩ ነበር

በእስር ቤቱ አካባቢ የታጠቁ ቡድኖች ቤት አየተከራዩ አንደሆነ ሰንሰማ ጥበቃው የበለጠ ተጠናከረ። በዚህ መሀል አንድ ቀን ማምሻውን አሰረኛው ወደየመኝታ ክፍሉ ገብቶ በር ከተዘጋ በኋላ፣ የፌደራል ፖሊስ ዩኒፎርም የለበሰ ኃይል የማረሚያ ቤቱን አሥተዳደር ሳያሳውቅ አና የቃሊቲ የውጭ በር ለማረሚያ ቤቱ መኪና ሲከፈት ተከትለው ገቡ። ልክ አንደገቡ አነ ጀኖዋር የትነውያሉት?»በማለት ጠይቀውወደነበርንበት ናኛቤት ሲያመሩ፡ጠባቂዎች ሊያሰቆሟቸው ሲሞክሩ ከመኪና ወርደው በአግራቸው መንዝ ቀጠሉ። ሆኖም ወደአኛ ከመድረሳቸው በፊት በኢንሰፔክተር ድሪባ የሚመሩ የማረሚያ ቤቱ ጠባቂዎች አሰቁመው ወደኋላ መልሰው አሰዕወጧቸው። በኋላ ሰናጣራ የመጡት ወታደሮች ከአፌደራል ፖሊሰ አውቅና ውጪ በአንድ የደኅንነት ሹም አንደታዘዙ ደረሰንበት። ይሀንንም ለቤተሰብ ነገረን ሕዝቡ እና ዲፕሎማቶች አንዲሰሙት አደረግን። ወደ ግቢያችን ለመግባት የተደረገው ሙከራ በደኅንነታችን ዙሪያ ያለውን ሥጋት በማጠናከሩ አንድንፈታ ከየአቅጣጫው ግፊት አንዲበረታ አደረገ።

የአሜሪካ መንግሥት ባለሥልጣናትም መንግሥት አንዲፈታን በተደጋጋሚ የሚያደርጉትን ጫና አጠናከሩ። የቀድሞው የኬንያ ፕሬዝዳንት ኡሁሩ ኬንያታ እና የአጋድ ዋና ጸሐፊ ዶ/ር ወርቅነህ ገበየሁ ጠ/ሚኒሰትር ዐቢይን አግኝተው፣ ሰለትግራይ ጦርነት ሲወያዩ አኛ መፈታት አንዳለብን በግልጽ ጠየቁት። ፕሬዝዳንት ኬንያታም ከአሰር ከተፈታሁ ለደኅንነቴ ወደ ኬንያ ሊወሰደኝ አንደሚችል ቃል ገባ። ዶ/ር ወርቅነህም ከእሰር መፈታቴ ሕይወቴን ከማዳን ባለፈ ለሀገሪቱ መረጋጋት እንደሚጠቅም ነገረው። ይሀ ጫና እና ተማጽኖ መጠናከሩ አኛን ለመፍታት አንዲቻኮሉ አደረገ።

አንድ ቀን የእሰር ቤቱ አስተዳዳሪ ወዳለንበት ግቢ መጥቶ ብቻዩን ጠርቶ የመንግሥትን መልዕክት ነገረኝ። ይህም ሊፈቱን አንደወሰኑ እና ተረጋግተን አንድንጠብቅ የሚመክር መልዕክት ነበር። አስከዚያውም በምግብ አንዳንመረዝ አንድንጠነቀቅ ነገረኝ። በመቀጠልም ሁለት ሽማግሌዎች መጥተው የመንግሥት መልዕክት አለን አሉ። «“ወጥተሀ መንግሥትን ካልተቸሀ አንፈታሃለን። ብለዋል» አሉኝ። እኔ ግን «ሰለ ኦሮሞ ጉዳይ አለመናገር አልችልም። በአፌ ዝም ብል አንኳን በሌላ አቅጣጫ ያመልጠኛል። ስለዚሀ ዝም አላለሁ ብዬ በሐሰት ቃል ገብቼ ከምወጣ እስር ቤት ብቆይ አመርጣለሁ› አልኳቸው። ሊያሳምኑኝ ሞክረው ሲያቅታቸው ተመልሰው ሄዱ።

መጨረሻ ላይ ብዙ የሀገር ሽማግሌዎች እና አንጋፋ የፖለቲካ ሰዎች መጡ። አባ ገዳ ጎበና

ሆላ እና ልዑካን ቡድኑን ጨምሮ ከአንጋፋዎቹ መካከል አቶ ገላሳ ዲልቦ፣ ሌንጮ ለታ፣ ዲማ ነጎ፣ ቄስ ኢተፋ ጎበና፣ ሼኽ ሐጂ ኢብራሂም፣ አቶ ዘገየ አስፋው እና ወይዘሮ መኪያ ማሚዩ ነበሩበት። እኛም ወጥተን አነጋገርናቸው። አቶ ዘገየ የልዑካን ቡድኑን ወክሎ የመጡበትን ጉዳይ ነገረን። «መንግሥት ያለ ምንም ቅድመ ሁኔታ ሊለቃችሁ ወስኗል› አለን። የቀሩትም ደም ተከተል ይሀንኑ ደገሙት።

ንግግራቸውን ካዳመጥን በኋላ አቶ በቀለ ተናገረ። ከሽማግሌዎቹ አንዱ ሰትወጡ ከመንግሥት ጋር ትሠራላችሁ ብሎ ሰለነበር፡ በቀለ ተናዶ «እንዴት እጃቸው በደም ከተጨማለቀ ሰዎች ጋር ሥሩ ትሉናላችሁን? ከፈለጉ ይፍቱን፡ አምቢ ካሉም ይተዉት እንጂ አብረን አንሠራም» አለ። እኔም አስከትዬ «መጀመሪያም ያለ ምንም ወንጀል ያሰረን መንግሥት ነው። እኛ እስረኞች ነን፡ ሲመሽ ግቡ ተብለን በር ይዘጋብናል። ጠዋት ውጡ ብለው በሩን ሲከፍቱልን እንወጣለን። ከታሰርን ጀምሮ እንወጣለን፣ እንገባለን።

አሁንም ከእሰር ቤቹ ውጡ ካሉን እንወጣለን። በጋራ መሥራትን በተመለከተ በመንግሥት እና በተቃዋሚ አመራሮች መካከል አብሮ መሥራት ሰላም እንደሚያሰፍን ከድሮም ሰንናገር ነበር። ወደፊት እንዴት እና ከማን ጋር እንሥራ የሚለውን በግለሰብ ደረጃ ሳይሆን ስንወጣ እንደ ፓርቲ ተወያይተን እንወሰናለን› አልኩን። አባ ገዳ ጎበናን «አርስዎ አዚህ መምጣት አልነበረብዎትም። በጅምላ ሰለተጨፈጨፉት የከረዩ አባ ገዳዎች ምንም ሳይናገሩ አዚሀ ምን ያደርጋሉ?» ብይ ተቆጣኋቸው። የከረዩ አባ ገዳዎች ግድያ የተፈጸመው ከጥቂት ሳምንታት በፊት ነበር። ሽማግሌዎቹ የመንግሥትን መልዕክት ነግረውን የእኛንም ተቀብለው ሄዱ። ከዚያ በኋላ ለሁለት ሳምንታት ምንም ሳንሰማ ቆየን። ምናልባት መልሳችን ለመንግሥትስላልተመቸው እኛን የመፍታቱን ሐሳብ ትተውት ይሆናል ብለን ገመትን።

ከሁለት ሳምንት በኋላ ዓርብ ዕለት ከአሥራ አንድ ሰዓት በኋላ የአሰር ቤቱ መኮንኖች መጥተው እቃችሁን ይዛችሁ ተነሱ ትወጣላችሁ አሉን። አሰረኛ የሚለቀቀው በሥራ ሰዓት ነው፡ ነገሩ አጠራጠረን። የሥራ ሰዓት ካለቀ በኋላ በተለይም ዓርብ ቀን ውጡ ማለታቸው ሰላጠራጠረን «ነገ ጠዋት በሥራ ሰዓት እንጂ በማታ አንወጣም›» በማለት አምቢ አልን። ደጋግመው ሊያስፈራሩን ሞከሩ። አሁንም አይሆንም ብለን ገብተን ቤቱን ዘጋነው። መመላለሳቸው እና ለማሰፈራራት መሞከራቸው ጥርጣሪያችንን የበለጠ ጨመረው። ድርጊቱ በመንግሥት እውቅና የሚፈጸም ሊመስለን አልቻለም። ከሁለት ሳምንት በፊት በፌደራል ፖሊስሰ ሰም ያለፈቃድ ሊገቡብን እንደሞከሩት ሁሉ፡ አሁንም በሌላ ስልት ሊመጡ ይችላሉ የሚል ጥርጣሬ ነበረን።ስለዚሀ ቢያንሰ ለመውጣት ፈቃደኛ ባለመሆን በሚከሰተው ግርግር ጉዳዩ የመንግሥት ከፍተኛ አመራር ጋር እንዲደርሰ ፈለግን።

ማታ ፖስት ሰዓት ገደማ ያለንበትን ቤት ሰብረው ገብተው በግድ አስወጡን። ተሸክመውኝ የፌደራል ፖሊሰ መኪና ውስጥ ሊያሰገቡን ሞከሩ። መኪናው ውሰጥ አልገባም ብዬ ከግቢው ወደ ዋናው መንገድ በአግሬ ወጥቼቺቹ ቤቴ ለመሄድ መንገድ ሰደምር፡ ጠባቂዎቹን አሳምነው በጉልበት አንስተው መኪናው ውሰጥ አስገቡኝ። ከመታሰሬ በፊት የነበርኩበት ቤት፣ እኛ ታስረን ብዙም ሳይቆይ ቤተሰቦቼ በመልቀቃቸው የማርፍበትን ቤት ሰላላዘጋጀሁ ወደ ወይዘሮ መኪያ ቤት ወሰዱኝ።

# 11.2.ከተፈታሁ በኋላ

ከተፈታሁብበት ዕለት አንስቶ ሕዝቡ ከሁሉም ዞን ወዳረፍኩበት ቤት መጉረፍጀጀመረ። መንግሥት ሥጋት ውስጥ ገብቶ ትርምዕ እንዳይፈጠር በማሰብ፣ ሕዝቡ በአንድ ጊዜ በብዛት ከመምጣት ይልቅ ቀጠሮ ይዞ ተራ በተራ እንዲመጣ ተደረገ። ከሦስት ወር በላይ ለሚሆን ጊዜ የረመዳን ወር አፅኪደርስስ ድረሰ ሕዝቡ በየቀኑ ከማለዳ ጀምሮ እሰከ ማታ ድረሰ በራ፣ ጠቦት፣ የተለያዩ ምግቦች እና አልባሳት ይዞ አየተፈራረቀ ይጠይቀኛል።

ያረፍኩበት የወይዘሮ መኪያ ቤት ከድሮ ጀምሮ የኦሮሞ ታጋዮች መሰባሰቢያ ነው። በ1983 ዓ.ም ደርግ ወድቆ የሽግግር መንግሥት ሲቋቋም፡ እንደ ገላሳ ዲልቦ፣ ነዲ ገመዳ እና ጄኔራል ዋቆ ጉቱ ያሉ አንጋፋ የኦሮሞ ታጋዮች ያረፉበት የነበረው ሰፊ ግቢ፣ እንደገና እኔ እና ሕዝቡ የምንገናኝበት መናኸሪያ ሆነ። በግዜው ውስጥ ብዙ ሰዎች በሚገኙበት ወቅት በስጦታ ከመጡት ሠንጋዎች ውስጥ መርጠን በማረድ ተሰብስበን እናበላለን። ብዙ ሰው በማይኖርበት ወቅት በሬዎች ተሸጠው ገንዘቡ ለኦፌኮ እንዲውል ይደረጋል። ከአንድ ሺ በላይ በጎች እና ፍየሎች እንደመጡ ጠባቂዎቹ እንደነገሩኝ አስታውሳለሁ። ለእንግዶች ታርደው የተረፉትን ዘመድ እና የሥራ ባልደረቦች እንዲወሰዱት ይደረጋል። እኔ ልፈታ አካባቢ ድምጻዊ ዮሰን ጌታሁን "ቡሎግ" የሚል ዘፈን አውጥቶ ስለነበር፡ ሕዝቡም ዘፈኑ ስለእኔ እንደሆነ በመገንዘብ በቪዲዮው ውስጥ የሚታየውን ዓይነት ፈረስ ከነሙሉ እቃው በስጦታ አበርክቶልኛል።

ብዙ ሰዎች እንደተለቀቅኩ ከመንግሥት ጋር ወደ ሌላ ዙር አተካሮ እና ብጥብጥ የምንገባ መስሏቸው ስለነበር፣ የሀገር ሽማግሌዎች፣ የሀይማኖት አባቶች እና ሴቶች በቡድን ሆነው እየመጡ ስለ እቅድ በስሱ ይጠይቁኛል።

ለምሳሌ፡ በዕውቁ ዓሊም ሼህ አደም ቱላ መሪነት የመጡት ከሃምሳ በላይ የሐረርጌ ዑላማዎች ለጊዜው ከመንግሥት ጋር ግጭት ውስጥ እንዳልገባ እና በትዕግሥት እንድጠብቅ ተማጽነውኛል። እኔ ግን ገና እስር ቤት እያለሁም፡ ከተፈታሁ አተካሮ ውስጥ ላለመግባት ወስኜ ነበር።

ምክንያቱም በወቅቱ ሀገሪቷ ለሁለት ዓመታት የዘለቀው ጦርነት ካስከተለው ከፍተኛ የሕይወት እና የንብረት ውድመት ገና ፋታ ማግኘቷ ነበር። የትግራይ እና የፌደራል ኃይሎች ጊዜያዊ ተኩስ ማቆም ላይ ሰለደረሱ፣ ሁለቱም ወገኖች ለረጅም ጊዜ ያራገቡትን የጦርነት ፕሮፓጋንዳ አለዝበው ሰለሰላም ማውራት ጀመረዋል። በዚያ ሁኔታ ውስጥ እኔ ወጥቼ ፀረ-መንግሥት የሆነ አቋም ባንጸባረቅ አዲስ የፖለቲካ ትኩሳት መፍጠር ይሆናል የሚል አምነት ነበረኝ።

ኦሮሚያ ውሰጥም ሀጫሉ ከተገደለ እና እኛ ከታሰርን በኋላ በኦሮሞ ነጻነት ሠራዊት እና በመንግሥች መካከል ያለው የአርስ በአርሰ ጦርነት ተባብሷል። በጦር ሜዳ ከሚካሄደው ውጊያ በላይ በመንግሥት ደጋፊዎች እና በተቃዋሚዎች መካከል ያለው ጥላቻ በሕብረተሰቡ ውሰጥ ትልቅ መከፋፈልን ፈጥሯል። እንዲህ ባለ ሁነታ ውሰጥ ለሕዝብ እና ለሀገር መልካም

ጥቅም ማስገኘት የምችለው፣ ከአሰር ሰወጣ ምን ዓይነት ሚና ብጫወት ነው ብዬ ብዙ አስቤበታለሁ። እንደወጣሁ መንግሥት ላይ የተቃውሞ ዘመቻ መክፈት የነበረውን ክፍፍል አና የእርሰ በአርስ ጦርነት የበለጠ የሚያባብስ እንደሆነ በመረዳት፣ ያለኝን ተሰሚነት በመጠቀም ሀገራዊ መረጋጋትን ለመመለስ መሞከር የተሻለ ጥቅም አለው የሚል አቋም ያዝኩ። ሰላም የማስፈን ሙከራ በሚዲያ ከመናገር ይልቅ ውሰጥ ለውሰጥ ከሚመለከታቸው አካላት ጋር በመወያየት ተጽዕኖ መፍጠር የተሻለው መንገድ እንደሆነ ወሰንኩ።

በተጨማሪም በአንድ ዓመት ከሰድሰት ወር የእስር ቤት ቆይታዬ ወቅት ብዙ ነገሮች መቀያየራቸውን ተገንዝቤያለሁ። ከመንግሥት ሚዲያዎች አንዲሁም እሰር ቤት ሊጠይቁን ከሚመጡ ሰዎች የተወሰነ መረጃ ብናገኝም በሳል ትንታኔ ለማካሄድ እና አቋም ለመያዝ ግን በቂ አልነበረም። ከአሰር ቤት እንደወጣሁ በቀጥታም ሆነ በመገናኛ ብዙኃን ለሕዝብ ከመናገር በራት የሀገር ውሰጥ እና የውጭ ማኅበረሰብ አካላትን አንዲሁም ተቃዋሚዎች እና የመንግሥት አመራሮችን በማነጋገር አመለካከታቸውን፣አረዳዳቸውን እና አቋማቸውን ማዳመጥ ፈለኩኝ።

ከዚህ በመነሳት ከሁሉም ዘኖች ሊጠይቁኝ የሚመጡ የማኅበረሰብ አባላትን ሰፋ ያለ ጊዜ ወስጄ ሳነጋግር ቆየሁ። ውጭ ሀገር ያሉ ሰዎችን ያግሞ በግለሰብ ኣና በይ. ,) በኢንተርኔት አወያየሁ። በተጨማሪም ሲቪል እና ወታደራዊ የመንግሥት ባለሥልጣናትንም በተለያዩ መንገዶች ኣግኝቺ አነጋግሬያለሁ።

የተለያዩ ፖለታካዊ እና ማኅበራዊ ቡድኖችን በዚህ መልኩ ለወራት ማወያየቴ በየጎራው የነዘረውን ሊኮኖሚያዊ፣ ማኅበራዊ እና ሥነ-ልቦናዊ አቋም በቅጡ እንድንነዘብ ረዳኝ።

በሀገር ደረጃ ያለውን ተጨባጭ ሁኔታ በተመለከተ ጥሩ ግንዛቤ ማግኘት እንድችል ይሀን ውይይት ከኦሮሞ ጋር ብቻ ሳይሆን ከሌሎች ብሔረሰቦችም ጋር አካሄድኩ። ከታሰርኩ በኋላ በጦርንቱ ምክንያት ሌሎች ሀገሮች በኢትዮጵያ ፓለቲካዊ ጉዳዮች ላይ ያላቸው ተጽዕኖ በከፍተኛ ደረጃ ሰለጨመረ የየሀገራቱን አቋም መረዳት ያሰፈልጋል። በአዲስ አበባ የሚኖሩ አምባሳደሮች እና ለጉብኝት የሚመጡ ዲፐሎማቶችን በቤቴ በመቀበል ሰፊ ውይይት አድርንያለሁ። በእነዚሀ ውይይቶች የተለያዩ ሀገራት ያላቸውን አቋም ለመረዳት አንዲሁም በአኛ በኩል ያለውን አመለካከት እና ምኞት ለማሰረዳት ሞክሬያለሁ።

ሌላው ዝዎምታን የመረጥኩበት ምክንያት የጠቅላይ ሚኒስትሩን ሰላም የማሰፈን ዕድል ለማሰፋት ነው። ምናልባት ከኦሮሞ ተቃዋሚዎች የሚመጣ ጫና ከቀነሰ በትግራይ አና በኦሮሚያ ክልል ያለውን ጦርነት በውይይት ለመፍታት ዕድሉን ያሰፋለታል ብዬ አሰበኩ። ስለዚሀ አኔ ወጥቼ መንግሥትን መንቀፍ እና ሕዝቡን ማነሳሳት የበለጠ ጫና አሳድሮበት ልቡን ሊከፋፍል ሰለሚችል ዝም ማለቴ ለሰላም የበለጠ ጠቃሚ ነው የሚል አምነት ነበረኝ።

ከእስር ቤት አንደወጣሁ መጀመሪያ ያገኘሁት የመንግሥች ባለሥልጣን ፊልድ ማርሻል ብርሃኑ ጁላ ነው። ወጥቼቹ በሦስተኛው ቀን አገኘሁት። በቁሮ ትግል ወቅት ከፊልድ ማርሻል ጋር በተደጋጋሚ እንገናኝ ነበር። በትግሉ ወቅት በተለይም በመከላከያ ሥራዊት ውሰጥ ሰላለው ተጨባጭ ሁኔታ በተለያዩ መንገዶች ጠቃሚ መረጃዎችን እና ምክሮችን ከአርሱ አናገኛለን። ለውጡ እንደመጣ ፊልድ ማርሻል ብርሃኑ የመከላከያ ምክትል ኢታማጆር ችም ሆኖ ሰለነበር፡ ኦነግን ወደ ሀገር አሰገብቶ አርቅ የመፈጸምን አሰፈላጊነት ለማሳመን ከሞከርኳቸው ውሰጥ አንዱ እርሱ ነበር። ወደ ሀገር ቤት ከገባሁ በኋላም በኦነግ እና በመንግሥት መካከል ሰላለው

ግጭትና ተያያዥ ጉዳዮች ብዙ ጊዜ ሰንወያይ ቆይተናል።

ረዘም ላለ ጊዜ ካደረግናቸው ውይይቶች በመነሳት ፊልድ ማርሻል ብርሃኑ ለሕዝብ ተቆርቋሪነት ያለውና ሐሳቡን በግልጽ የሚናገር ሰው እንደሆነ ተረድቻለሁ። የኦሮሞ ነጻነት ሠራዊት በሰላም ገብቶ፣ ኦሮሞ አንድ እንዲሆን ከልቡ ሞክሯል። ሌሎች የመንግሥት ባለሥልጣናት ሲያሴሩብን እርሱ ብዙ ረድቶናል። ከመታሰሪ በፊት ባደረግነው የመጨረሻ ውይይት ምርጫ እንዳልወዳደር መክሮኛል። «ከእነዚህ ሰዎች ጋር ትጣላለህ፣ አንተ ወደ ምርጫ ከገባህ ይሸነፋሉ፡ ይህን ስለሚያውቁ እንድትወዳደር አይፈቅዱም። በዚህ የተነሳ ኦሮሚያ ከባድ ትርምስ ውስጥ ትገባለች› ብሎ ሊያሳምነኝ ሞክሯል። «ከእነዚህ ሰዎች ጋር ለመሥራት ምን ያሀል እንደሞከርኩ ታውቃለህ። አሁን ግን ከመንገድ አፈንግጠው ፌደራሊዝምን ለማፍረስ እየሞከሩንነው። በተጨማሪም ሀገሪቷን ሕዝቡ ወደታገለለት ዴሞክራሲያዊ ሥርዓት ከማሸጋገር ይልቅ አዲስ አምባገነናዊ ሥርዓት ሊገነቡ አየጣሩ ነው። ኦሮሞን ይንቃሉ። በግለሰባዊ አና ቡድናዊ ፍላጎት ታውረው ሕዝቡ ከሃምሳ ዓመታት በላይ በፈጀ ትግል እና በከፍተኛ መሥዋእትነት የተጎናጸፈውን ድል ለማጥፋት አየሄዱ ነው። ዓይኔ አያየ የሕዝብን እና የሀገርን ዕድል ሲያበላሹ ዝም አልልም። ስለዚህ ይህ ሕዝብ አማራጭ አመራር (Alternative leadership) ያስፈልገዋል›» በማለት፣ ምርጫ ለመወዳደር የወሰንኩበችን ምክንያት ነግሬው ተለያየን።

ፊልድ ማርሻል ብርሃኑ ከታሰርኩ በኋላም ከእስር አንድፈታ ግፊት ካደረጉ ጥቂች ባለሥልጣናት መካከል አንዱ አንደነበር ሰምቻለሁ። እንደተፈታሁ ሽማግሌዎች መጥተው ፊልድ ማርሻሉን ማናገር አንዳለብኝ ነግረውኝ ወደ ቤቱ ሄደን ሽማግሌዎቹ ብቻችንን ትተውን ሲሄዱ ለረጅም ሰዓት በቁጣ ተናገረኝ። ኦሕዴድን እና ጠቅላይ ሚኒስትሩን አሞጋገሰ። ሰሕተቱ ሁሉ የእኔ አና የተቃዋሚዎች አንደሆነ ተናገረ። ኦሕዴድ የሕወሐትን ሥርዓት ለመጣል የተጫወተውን ሚና አሞካሽቶ የሌሎችን አጣጥሎ ተረከልኝ። ይህን ሁሉ የቁጣ ውርጅብኝ ባለቤቱ በላይ በላዩ በምትቀዳልኝ ቡና አያወራረድኩ ሰዳምጥ ቆየሁ። ከሁለት ሰዓት በላይ ከተቆጣኝ በኋላ ባለቤቱ በተደጋጋሚ የመናገር ዕድል አንዲሰጠኝ ሰትነግረው ነበርና አንደምንም ተራው ደረሰኝ።

ባለፈው ታሪክ ላይ ለመከራከር አልፈለኩም። ሁለታችንም የምናውቀውን ታሪክ ከልሶ ለማቅረብ መሞከሩን አያየሁ ልሞግተው አልቃጣኝም። በእኔ ላይ የደረደረውን ክስ አና ውንጀላ መካድም ሆነ ራሴን መከላከል አሰፈላጊ ሆኖ አልታየኝም።

ሰለዚህም «ዛሬ ሰለ ትላንት ክሰተቶች ለማውራት ሳይሆን ስለ ነገው፡ ለአናንተ አና ለመንግሥታችሁ ያለኝን መልዕክት ለማስተላለፍ ነው የመጣሁት› በማለት መልዕክቶቹን በቅደም ተከተል ነገርኩት።

ሀ. የፊልድ ማርሻል ደረጃ ዕድገት በማግኘትህ ከቀድሞ ግላዊ ቅርርባችን በመነሳት ደሰታዬን ልገልጽልህ እወዳለሁ

ለ. ሀጫሉ ሁንደዴሳ ገድያ ላይ ቤተሰቡም ሆነ ሕዝቡ አሰካሁን አውነቱን አውቆ አርሙን ማውጣት ሰላልቻለ፣በገለልተኛ ወገን ሁሉንም ሊያሳምን የሚችል ምርመራ ተካሂዶ አውነታው ቢታወቅ አስፈላጊ መሆኑን፣

ሐ. በእኔ ላይ በደረሰው ማንኛውም ነገር በመንግሥት ላይ ምንም ዓይነት ቂም እንደሌለኝና

እኔን መጠራጠር እንደማያሰፈልግ ለሌሎች ባለሥልጣናት በአንተ በኩል እንዲያውቁት፣

መ. በየአቅጣጫው በተፈጠረው የእርሰ በአርስ ጦርነት ሀገሪቱ ልትፈርሰ ቋፍ ላይ ነች። የሀገረ-መንግሥት መበታተን ደግሞ ለሀገሪቱ ሕዝቦች ትልቅ ኪሳራ ነው። የዚህች ሀገር መፍረሰ አሁን ሥልጣን ለያዘው ገዢ ቡድን ብቻ ሰይሆን ለመላው የኦሮሞ አመራር ትልቅ ውርደት ነው። ሰለዚህ የዚህችን ሀገር ሰላም መመለስ ቀዳሚ ጉዳይ መሆን አለበት። በዚህ በኩል እኔም ሆንኩ ባልደረቦቼ ከእኛ የሚጠበቀውን ሁሉ ለማገዝ ዝግጁ መሆናችንን ላንተም ለባልደረቦችህም ለማሳወቅ ነው ብይ ውይይታችን በዚሁ ተቋጭቶ ተለያየን።

## 11.3. የሰላም ሰባኪ

ከእስር ቤት ከወጣሁ በኋላ ለአምስት ወራት ያህል የሀገር ውስጥ እና የውጭ መገናኛ ብዙኃን እኔን ለማነጋገር ያደረጉትን ሙከራ አልተቀበልኩም። መጀመሪያ ለመናገር ስወስን ለኡቡንቱ ሚዲያ የመጀመሪያውን የቃለ-መጠይቅ ዕድል ሰጠሁ። ይሀንን ቃለ-ምልልሰ ለመሰጠት የተነሳሳሁት ወደ ውጪ ለሙሄድ በዝግጅት ላይ ስለነበርኩ አቋሜን አሰቀድሜ ለሕዝቡ ለማሰረዳት ሰለፈለኩ ነው። ከተፈታሁ በኋላ ባሉት አምስት ወራት ውሰጥ ከተለያዩ አካላት ጋር ያደረኩቸን ውይይት ጠቅለል አድርጌ አንዲሁም ከንባቤ እና እስር ቤት እያለሁ በጥሞና ራሴን ከማዳመጥ የፈለቁ ሐሳቦችን ጨማምሬተዘጋጀሁ።

በአጠቃላይ በቃለ-ምልልሱ ማሰተላለፍ የፈለኩት መልዕክት ሀገርን ማረጋጋት እና ሰላምን ማስፈን ቀዳሚ ተግባር መሆን አንዳለበት ማስንንዘብ ነበር። ኢትዮጵያን ከውድቀት ማዳን ለኦሮሞም ሆነ ለሌሎች ብሔሮች ወሳኝ ጉዳይ አንደሆነ አደራ አልኩ። ምክንያቱም አሁን ባለው ሁኔታ ኢትዮጵያ ከፈረሰች ነጻ ሀገር ሊመሰርቱ የሚችሉ ክልሎች እንደሌሉና ይልቁንም የኢትዮጵያ መፍረስ፣ ኦሮሚያን ጨምሮ ሁሉንም ክልሎች ለውሰጣዊ መበታተን አንደሚያጋልጣቸው ተናገርኩ። ህሀን ያልኩት በወቅቱ የፌደራል መንግሥት ልክ ዩጎዝላቪያ እንደሆነው ቢፈርስ አንኳን ብሔሮች እና ክልሎች ነጻ ሀገር ሊመሰርቱ ይችላሉ የሚል ሐሳብ ሰለነበር በኢትዮጵያ ተጨባጭ ሁኔታ ይህ የማይቻል መሆኑን ለመጠቆም በመፈለግ ነው።

በተጨማሪም አሁን ባለው ውስጣዊ የአርሰ በአርሰ ግጭት መሸናነፍ አንደማይቻል አበክሬ ተናገርኩ። ምክንያቱ ደግሞ ዛሪ ፅዓለም ላይ ያለው የአርስ በእርስ ጦርነት (civil war ) ሁለቱን ተፋላሚ ወገኖች ብቻ ሳይሆን በርካታ የውጭ አካላትንም የሚያሳትፍ በመሆኑ ነው። ለምሳሌ በቀዝቃዛው ጦርነት (cold war) ወቅት በታዳጊ ሀገሮች ውስጥ ሲደረጉ የነበሩ የእርስ በርስ ጦርነቶች በሁለቱ ኃያላን ሀገሮች ማለትም በአሜሪካ እና ሶቭይት ሕብረት ይታገዛሉ። በአንዲሀ ያለ ሁኔታ የተሻለ አርዳታ ያገኘው ተፋላሚ ቡድን የአርሰ በአርሰ ጦርነቱን የማሸነፍ ዕድል ያገኛል። አንድም መንግሥት አማጺውን ሰብሮ ሀገሪቱን ያረጋጋል፣ አሊያም አማጺው መንግሥትን አሸንፎ ሥልጣን ይጨብጣል፤ ካልሆነም ክልሉን/ግዛቱን ገንጥሎ አዲስ ሀገር ይመሠርታል።

ዓለም በሁለት ኃያላን ብቻ መዘወሯ ካበቃለት ወዲህ ግን በአንድ ሀገር ውሰጥ የአርስ በአርሰ ጦርነት ሲነሳ ብዙ ሀገሮች ይሳተፋሉ። አሁን አሁን መካከለኛ ኢኮኖሚያዊ እና ወታደራዊ አቅም የገነቡ ሀገራች (middle power countries) በብዛት ተፈጥረዋል። አነዚሀ ሀገሪት በአካባቢያቸው ኢኮኖሚያዊ፣ ፖለቲካዊ እና የጸጥታ የበላይነትን ለመቀዳጀት ከፍተኛ ፉክክር ውስጥ ናቸው። ከሚወዳደሩባቸው መንገዶች አንዱ በቀጠናው ባሉ ሀገራት ፖለቲካ ላይ ተጽዕኖ በማሳደር ነው። በአንድ ሀገር ውሰጥ የአርዕ በእርስ ጦርነት ሲቀሰቀስ ተፋላሚ ቡድኖችን ወዲሀ እና ወዲያ ሆነው በመርዳት ግጭቱ እነሱን በሚጠቅም መልኩ እንዲጠናቀቅ ይሞክራሉ።

ይህ ማለት ግጭቱ በሁለቱ የሀገር ውሰጥ ቡድኖች መካከል ብቻ ሳይገደብ በተቀናቃኛቹ ሀገራት መካከልም ይሆናል ማለት ነው። መካከለኛ አቅም ያላቸው ሀገራት መብዛታቸው የሚደረገውን ጦርነት በማወሳሰብ መሸናነፍም ሆነ መታረቅ አሰቸጋሪ እንዲሆን ያደርገዋል። መሸናነፉ ቀርቶ ለእርቅ ጭምር የሁለቱ ተፋላሚ ቡድኖች ፈቃድ ብቻውን በቂ አይሆንም። የሀገሪቱ ሁለት ተፋላሚ ወገኖች ለመታረቅ ፍላጎት ቢኖራቸው አንኳን ክጀርባ የሚረዱት ሀገራት (sponsors) ካልፈቀዱ አርቁን ማሳካት ይከብዳል። አንደ ሶሪያ፣ የመን፣ ሊቢያ አና ሶማሊያ ያሉ ሀገራት ማለቂያ የሌለው ግጭት ውሰጥ አንዲቆዩ ያደረገው አንዱ ምክንያት የመካከለኛ አቅም ያላቸው ሀገራት ፉክክር ነው።

ኢትዮጵያንም የእነዚህ ሀገራት እጣ ፈንታ እንዳይገጥማት ሁሉም በመረባረብ፣ ሰላምን በማምጣት ረገድ የሚጠበቅበትን ሚና እንዲጫወት ተማጸንኩ። በበኩሌ ሁሉንም ተዋጊ ወገኖች በማናገር ማቀራረብ እንደምፈልግና ለአንዱ ቡድን ወግን ሌላውን ቡድን በማግለል ጦርነትን ማበረታታት እንደማልፈግ ገለጸኩ። ፈጣሪ እስርን ሰበብ አድርጎ ባለፉት ሁለት ዓመታት የእርስ በእርስ ጦርነት ውሰጥ እንዳልሳተፍ አድርጎኛል። አሁን ከአስር ቤት ከወጣሁ በኋላም በዚህ ጦርነት መሳተፍ አልፈልግንም በግለት ሐሳቤን አብራራሁ።

በቃለ መጠይቁ ወቅት ሐሳቤን ለስለሰ ባለ እና በተረጋጋ ድምጽ ስላሰተላለፍኩ፣ ሕዝቡ ድሮ በአሰገምጋሚ እና ቁጡ ድምፅ ሰለሚያውቀኝ ግራ ተጋባ። ይህ የተለሳለሰ ድምጽ ሰላም ከሚሰብከው የሐሳቤ ይዘት ጋር ተዳምሮ በሕዝብ ዘንድ ጥያቄ ማሥነሳቱ ግልፅ ነበር። ቃለ-ምልልሱም ዋና የውይይት ርዕስ ሆነ። በኦሮሞ በኩል ክፍተኛ ተቃውሞ አሥነሳ። ጀዋር ወጥቶ ትግሉን ያቀጣጥላል ብሎ ሲጠብቅ የነበረ በተቃራኒው ሰላምን ስሰብክ እና ነገሮችን ለማረጋጋት ሰሞክር በማየቱ ተበሳጨ። ይሀ የጠበኩት ነገር ሰለነበረ ብዙም አልተገረምኩም። ቀጥሎ በቃለ-ምልልሱ ውስጥ ያነሳኋቸውን ሐሳቦች የበለጠ አሰፋፍቼ ሕዝቡን ለማወያየት ወደ ውጭ ሀገር ተጓዝኩ።

## 11.4. ከውጪ ማኅበረሰብ ጋር ያደረኩት ውይይት

በሚዲያ ቃለ-ምልልስ ከሰጠሁ ከአንድ ወር በኋላ የውጭውን ማኅበረሰብ ለማነጋገር "የምስጋና ጉዞ (Imala Galatoomaa) " ብለን የሰየምነውን ዘመቻ ለማካሄድ ወደ አውሮፓ እና ሰሜን አሜሪካ አቀናን። የዚህ ጉዞ ዓላማ ሁለት ነበር። አንደኛው እስር ቤት በነበርንበት ወቅት ለእኛ ሲሉ በረዶ እና ፀሐይ ሳይበግራቸው ውጪ ላይ ውለው በማደር ድምፅ ለሆኑንና ቤተሰቦቻችን እንዳይቸገሩ አስፈላጊውን ድጋፍ ሲያደርጉ የቆዩትን የዲያስፖራ ማኅበረሰብ ለማመስገን ነው።

ሁለተኛው እና ዋነኛው የጉዞው ዓላማ ሰላምን መስበክ ነበር። ባለፈው ምዕራፍ እንደገለጽኩት፡ ከእስር ቤት ስፈታ ሀገሪቱን ወደ ሰላም እና መረጋጋት ለመመለስ የተቻለኝን ሁሉ ለማድረግ ቆርጬለሁ። ሰላም እንዲሰፍን መንግሥት እና በነፍጥ ኃይል የሚዋጉ ቡድኖች ጉዳያቸውን በእርቅ መፍታት አለባቸው። እነዚህ ተፋላሚ ኃይሎች እንዲታረቁ የፖለቲካ ገበያው ከጦረኝነት ወደ ሰላም ወዳድነት መቀየር አለበት።?”

ባለፉት አመታት ተፈጥሮ በነበረው የፖለቲካ ቀውስ ምክንያት እስር ቤት በነበርንበት ወቅት፤ የኦሮሞም ሆነ የተቀረው የኢትዮጵያ ማኅበረሰብ አመለካከት ጦርነትን የማበረታታት ነው። የሕዝቡ አመለካከት ጦርነትን በሚያበረታታበት ሁኔታ ውስጥ የተፋላሚ አመራሮች እርቅ ቢፈልጉ እንኳ ወደ ሰላም የሚያመጣውን እርምጃ ለመውሰድ ይፈራሉ። ደጋፊዎቻቸው ጦርነትን የሚያበረታታ ስሜት ውስጥ ባሉበት ሁኔታ ከጦርነት ይልቅ የሰላምን መንገድ ቢመርጡ እንደ ባንዳ ወይም እንደ ፈሪ በመታየት ድጋፍ አጣለሁ ብለው ይጠራጠራሉ። በመሆኑም የእርሰ በእርስ ጦርነት በውይይት እንዲፈታ ከተፈለገ በቅድሚያ የሕብረተሰቡን አመለካከት ወደ ሰላም ወዳድነት መቀየር ያስፈልጋል። በሁለቱም በኩል ያለው አመራር ለመታረቅ ፈቃደኛ ከሆነ ያለማመንታት እንዲገፋበትያበረታታል። አመራሩ ሰላምን የሚቃወም ከሆነ ግፊት በማድረግ ወደ ድርድር እንዲገቡ ያስገድዳል።

ከዚህ ትንታኔ በመነሳት በውጪ ያለው ማኅበረሰባችንን አመለካከት ጦርነትን ከማበረታታት ወደ ሰላም ወዳድነት ለመቀየር ወሰኼ ሄድኩ። ጦርነትን በሚያበረታታ ማኅበረሰብ ውሰጥ ሰላምን መስበክ ከባድ ነው።

በተለይ ባለፉት ዓመታት ለከባድ ቁጣ፣እልህ እና ፀፀት በተጋለጠው የኦሮሞ ማኅበረሰብ ዘንድ፣ በከፈለው መሥዋዕትነት ሰዎች ሥልጣን ይዘው፣ ወደ ነጻነት እና ዴሞክራሲ ያሸጋግሩኛል ብሎ ሲጠብቅ ከድሮው የበለጠ ስቃይ ሲያመጡበት ሕዝቡን ከፍተኛ ቁጣ ውሰጥ ከቶታል። ብዙኀኑ ከሀጫሉ ግድያ እና ከእኛ መታሰር በኋላ በሰላማዊ ትግል ተሰፋ ቆርጦ የትጥቅ ትግል ለመደገፍ ወስኗል።

ከእስር ቤት ስወጣ ከመንግሥት ጋር መታረቅ ይቅርና ሰለ ሰላማዊ ትግል ለመስማት ፍላጎት የነበረው ሰው በጣም ውስን ነው። በእርቅ እና በሰላማዊ ትግል የሚያምኑትም ቢሆኑ የሕዝብን አስተያየት በመፍራት አይናገሩም። በዚያ ሁኔታ ውሰጥ እርቅ እና ሰላምን ለመስበክ ወደ ውጭ

ስሄድ የሚያጋጥመንን የፖለቲካ አደጋ አላጣሁትም።

ይህን ያደረኩት በኦሮሚያ እና በሰሜን ያለው ጦርነት በእርቅ እንጂ በጦርነት ሊያልቅ እንደማይችል ስለደመደምኩና የትጥቅ ትግልን ሙሉ በሙሉ እየደገፈ ባለ ማኅበረሰብ ውሰጥ የዚህን ሐሳብ ተቃራኒ ለማቅረብ ተቃውሞን እና እርግማንን የመቋቋም ልምድ ማዳበር ስለሚያስፈልግ ነው። በተጨማሪም በሕዝብ የማይወደድ ሐሳብ (unpopular opinion) ለመደመጥ ዕድል የሚያገኘው፣ ሐሳብ አቅራቢው በቂ የፖለቲካ እሴት ካለው ብቻ ነው። እኔ ሁለቱንም መስፈርቶች አሟላለሁ፡ ተቃውሞ እና አርግማን የመቋቋም ልምድን አካብቻለሁ። በቄሮ ትግል ውጤት እና በዓላማዬ ጸንቼ በመታሰር ሕዝቡ ዘንድ ክብር እና አመኔታን አፍርቻለሁ፡ የፖለቲካ እሴት የምንለው ይሀንኑ ነው። ከዚህ በመነሳት ሰላምን ለመስበክ ጉዞዬን ጀመርኩ።

በቀለ ገርባ ለሕክምና ቀድሞ ወደ አሜሪካ ሲሄድ፣ እኔ ደግሞ ሕዝባዊ ስብሰባውን በአውሮፓ ጀመርኩ። የመጀመሪያውን ውይይት የጀመርኩት በጀርመን ኑረንበርግ ከተማ ነበር። ሕዝቡ ግልብጥ ብሎ በመታደም አዳራሹን አጥለቀለቀው። በንግግሬ ግጭቱ በሕዝብ እና በሀገር ላይ የሚያደርሰውን አደጋ ከዘረዘርኩ በኋላ ሁሉም ተፋላሚ አካላት ወደ ድርድር ጠረጴዛ መሄድ እንዳለባቸው ተናገርኩ።

ከኑረንበርግ በመቀጠል ፈረንሳይ ፓሪሰ ከተማ በተደረገው ስብሰባ የኢትዮጵያን ውስጣዊ ሰላም መመለስ፣ ለኦሮሞም ሆነ ለሌሎች ብሔረሰቦች አስፈላጊ መሆኑን ዘርዘር አድርጌ በድጋሚ ተናገርኩ።ከዚያም ወደ ኔዘርላንድ አምስተርዳም ከተማ አመራን። በኑረምበርግ እና በፓሪስ ውይይቶች ላይ ታዳሚው በጣም ብዙ ሰለነበር ከተሳታፊዎች ጋር ጥያቄ እና መልስ ማድረግ አልቻልኩም። ሰለሆነም በአምስተርዳሙ ስብሰባ ንግግር ከማድረግ ይልቅ ተሳታፊዎቹ በጀርመን እና በፈረንሳይ ባደረኳቸው ንግግሮች ላይ ጥያቄዎችን እንዲጠይቁ እና አስተያየት እንዲሰጡ ዕድል ሰጠሁ። የጀርመን እና የፈረንሳይ ውይይቶች በፌስ ቡክ በቀጥታ ሲተላለፉ ስለነበር፣ በዓለም ዙሪያ ያለ ሰው ሊከታተለው ይችላል። እንዲሁም ሳስተላልፋቸው የነበሩት መልዕክቶች ሰፊ መነጋገሪያ ስለነበሩ፣ የአምስተርዳም ስብሰባ ታዳሚዎች ብዙ ጥያቄዎች እንዳላቸው ገምቻለሁ። ተሳታፊዎቹ ሰልፍ ይዘው ጥያቄዎችን፣ ትችቶችን እና አስተያየቶችን አዥጎደጎዱብኝ። እሰኪበቃቸው ድረሰ ዕድል ሰጥቻቸው ወደ መልሱ ተመለስኩ።

አብዛኛዎቹ አስተያየቶች እና ጥያቄዎች በትጥቅ ትግል አስፈላጊነትና ልዩነቶችን በሰላም መፍታት እንደማይቻል በመከራከር ላይ ያተኮሩ ነበሩ። በተጨማሪም የኢትዮጵያ ኢምፓየር ካልፈረሰች እና ነጻ ኦሮሚያ ካልተመሠረተች ኦሮሞ ሰላሙን እና መብቱን መጎናጸፍ አይችልም የሚሉ ናቸው። እነዚህ ጉዳዮች አብዛኛው የኦሮሞ ፖለቲካ መሪዎች ሕዝቡን በመፍራት ሲሸፋፍኗቸው የነበሩ ስለሆኑ ግልጽልጽ አድርጌ ለመናገር ወሰንኩ። በተለይ በሁለት ነጥቦች ላይ ያለኝን አቋም አስረግጬ ተናገርኩ።

1. እኔም ሆንኩ ኦፌኮ የእርስ በእርሰ ጦርነት በሀገሪቱ ውስጥ ላለው የፖለቲካ ግጭት መፍትሔ ይሆናል ብለን እንደምናምን እየተደረጉ ያሉት ጦርነቶች ቆመው የፓለቲካ ችግሮች በውይይት እንዲፈቱ የምንታገል መሆኑን በመግለጽ ለፓለቲካዊ ችግሮች ፖለቲካዊ መፍትሔ መፈለግ ጦርነትን ከመምረጥ የተሻለ መሆኑን አሰመርኩበት።

2. እኔም ሆንኩ ኦፌኮ የኦሮሞ ጥቅም እና መብት የሚከበረው ኦሮሚያን በመገንጠል ሳይሆን ኢትዮጵያ ውስጥ ፌደራላዊ እና ዴሞክራሲያዊ የሆነ ሥርዓት በመገንባት፣ ሁሉም የየራሱን ክልል በማሥተዳደር፡ በፌደራል ደረጃ ሥልጣንን በፍትኃዊነት ተጋርቶ የጋራ ሀገር በመንንባት እንደሆነ ገለጽኩ።

ቀጥሎ በኖርዌይ፣ በሰዊድን እና በእንግሊዝ ሀገራት በዚሁ መልኩ የጋለ ክርክር የተሰተዋለባቸውን ውይይቶች አደረግን። የአውሮፓ ጉዞዬ ከሕዝባዊ ውይይቱ በተጨማሪ የዲፕሎማሲ ሥራ የማጠናከር ዓላማም ነበረው። ከእስር ከተፈታሁ ጀምሮ በኦሮሞ ነጻነት ሠራዊት እና በመንግስት መካከል የሚካሄደው የእርስ በእርስ ውጊያ በሕዝቡ ላይ እያደረሰ ያለው ጉዳት ትኩረት ሊሰጠው እንደሚገባ በፊንፊኔ ላሉ እና ለሥራ ለሚመጡ ዲፕሎማቶች በመንገር ሰላም እንዲወርድ ጫና በማድረገ እንዲረዱን ስማጸን ነበር። በአውሮፓ ጉዞይም በኦሮሚያ ሰላምን ማሰፈን ለኢትዮጵያ እና ለአፍሪካ ቀንድ መረጋጋት ያለውን ጠቀማታ ለማሰረዳት በጎበኘኋቸው ሀገራት የውጭ ጉዳይ ሚኒስትሮችን እና ሌሎች የመንግሥት አካላትን አነጋግሬያለሁ። በዚህ የዲፕሎማሲ ሥራ ጥሩ ሰኬት ተገኝቷል።

የአውሮፓውን ውይይት ከጨረሰኩ በኋላ ወደ ጣሊያን ሄጄ የቀድሞውን የኦሮሚያ ክልል ፕሬዝዳንት ለማ መገርሳን አነጋገርኩት። ገና ከሀገር ስወጣ ጊዜ ካገኘሁ ላናግረው እቅድ ነበረኝ። አውሮፓ ከደረሰኩ በኋላ ሰለእርሱ በውግዘት መልክ አንድ መድረክ ላይ ጥያቄ ሲነሳ፡ «ለማ የሚችለውን ለሕዝቡ አድርጓል። ለኦሮሞ ሕዝብ ባለውለታ ነው። አሁንም ቢሆን ሕዝቡን ከቀድሞ ባልደረቦቹ ጋር ከመበደል ይልቅ ሁሉን ትቶ የግል ኑሮውን መኖር ከመረጠ ሊመሰገን እንጂ ሊወገዝ አይገባም› ብዬ መልሻለሁ።

ያን ቀን አመሻሽ ላይ አንድ ለመንግሥት ቅርብ የሆነ ሰው ደውሎ ለማን ማወደሴ ስሕተት እንደሆነ እና በአካል አግኝቼ እንዳላናግረው መከረኝ። ለማን ማናገር ጠ/ሚኒሰትር ዐቢይን እንደሚያሰቀይምም አከለበት። «ለማን ይቅርና ማንንም ሰው ለማናገር የመንግሥት ፈቃድ አያስፈልገኝም። ለማን በማናገሬ የሚናደድ ሰው ካለ የራሱ ችግር ነውን አልኩት። "አታናግረው" መባሌ የበለጠ እልሀ ውስጥ ሰለከተተኝ ወደ ሮም፣ ጣሊያን ላገኘው ሄደኩ። አንድ ምሽት እራት አብረን በልተን ብዙ ነገር አወራን። በማግሰቱ ሁለታችንም የጣሊያንን የውጭ ጉዳይ ሚኒስቴር አመራሮችን ካነጋገርን በኋላ ተለያየን።

የአውሮፓ ጉዞዬን ከጨረሰኩ በኋላ ወደ ሰሜን አሜሪካ ተሻገርኩ። በመጀመሪያ ወደ ኒውዮርክ ከተማ በማቅናት ከተለያዩ የተባበሩት መንግሥታት ድርጅት(United National) ባለሥልጣናት ጋር ስለ ኢትዮጵያ ሁኔታና በኦሮሚያ ያለውን የእርስ በእርሰ ጦርነት እንዴት ማስቆም እንደሚቻል የሁለት ቀናት ውይይት አደረግን። ከዚያ ተነስቼ ወደ ሚኒሶታ ስሄድ ብዙ ሕዝብ ወጥቶ ከአውሮፕላን ማረፊያ ተቀበለኝ። በማግሰቱ በሺዎች የሚቆጠሩ ሰዎች በተገኙበት ከበቀለ ጋር በመሆን ሕዝቡን አወያየን። ሚኒሶታ ላይ ባደረኩት ንግግር በሐሳብ ብዙ ዓመታትን ወደኋላ ነጎድኩ። ለረጅም ጊዜ ከምንተዋወቅ እና አብረን ከሠራን ወዳጆች ጋር በመተያየቴ ዓይኖቼ እንባ አቀረሩ። በንግግሬም

የወጣቶች ማኅበርን ከመሠረትንበት ጊዜ ጀምሮ በከተማዋ ስናከናውን የነበረውን ሥራ አወሳሁ። ,OMNን ማቋቋም ጨምሮ ሌሎች ፕሮጀክቶችን ስንሠራም የሚኒሶታ ማኅበረሰብ ከመጀመሪያው ከጎኔ ሰለነበሩ አመሰገንኩ። በተለይ አርፋሴ ገመዳ ባልታወኩበት ጊዜ ጥረቴን ቀድመው ተቀብለው ከጎነ ከቆሙት መካከል ግንበር ቀደሚ እንደሆነች ተናገርኩ። ከዚያ በኋላ ትዳር መሥርተን፣ ግላዊ እና ሕዝባዊ ትግልን ተጋግዘን ሰናኣኬድ እንደነበር መሰከርኩ። ልጃችን ኦሮሞ ከተወለደ በኋላም በትግሉ ተጠምጄ ሰለነበር ብቻዋን ማሰደዷን አነሳሁ። ከታሰርኩ በኋላም ትዳራችን የገጠመው ችግር ሳያግታት ለኔ መፈታት ሰታደርግ ለነበረው ያላሳለሰ ጥረት አመሰገንኳት።

ከሚኒሶታ በኋላ በሰሜን አሜሪካ ወደ አሥራ አምስት ከተሞች ሄደን ሕዝቡን አነጋገርን። በዋነኛነት ያተኮርነው ሰላም በማውረድ አስፈላጊነት ላይ ነው። የተለያዩ ሰዎች እና ቡድኖች እኛን በመቃረን ከፍተኛ የስም ማጥፋት ዘመቻ ከፈቱ። ምናልባት በዚህ ዘመቻ ተጽዕኖ ከበቀለ ጋር ሐሳባችን መለያየት ጀመረ። አውሮፓ እያለሁ "እወዛጋቢ ጉዳዮችን ማንሳትህ ተቃውሞ አያሥነሳ ሰለሆነ ብንተወው" የሚል ሐሳብ አቅርቦልኝ ነበር። እኔ ግን የምናምንበት እና በፓርቲ ደረጃም ወስነን የመጣነው ስለሆነ ተቃውሞ አጋጠመን ብለን መተው የለብንም በሚል ሐሳብ ጸናሁ። በጋራ በተናገርንባቸው መድረኮች ላይ ልዩነታችን የበለጠ ግልጽ እየሆነ መጥቶ ወደ መቃረን ተሸጋገርን። ይህም ግንኙነታችን ላይ ጫና ፈጠረ።

ሕዝባዊ ስብሰባውን ባወያየን ቁጥር እኛን የሚቃረኑ ተቃውሞዎች እና ዘመቻዎች እየቀነሱ መጡ። እቅዴም ይሄ ነበር። በመጀመሪያ አከራካሪ ጉዳዮችን በማንሳት የሕዝቡን ሰሜት ኮርኩሮ ቁጣው እንዲወጣለት በማድረግ ቀጥሎ ወደፊት ልንከተለው የሚገባንን ስልት መጠቀም ነበር።

በዚህም መሠረት በአውሮፓ እና በአሜሪካ ሰሜታዊ ውይይቶችን ካደረኩ በኋላ ካናዳ እንደደረስኩ አሰቀድሜ ሀገር ቤት ባዘጋጀሁት ጽሑፍ ላይ በመመሥረት ትግሉ ሰላለፈበት ሁኔታ፣ አሁን ያለበትን ደረጃ እና ቀጣዩን ምዕራፍ የሚጠቁም ማብራሪያ ማቅረብ ጀመርኩ። ያንን "Haala Kesessa Jirruu Fi Boqonnaa Qabsoo Itti Aannnu (ያለንበት ሁኔታ እና ቀጣዩ የትግል ምዕራፍ) "" በሚል ርዕስ የተዘጋጀውን ጽሑፍ በOSA ዓመታዊ ስብሰባ ላይ ለማቅረብ አስቤ ነበር። ሆኖም እንደ ዋና ተናጋሪ (Keynote Speaker) መጋበዜ በተወሰኑ የኦነግ ደጋፊዎች ዘንድ ከፍተኛ ተቃውሞ ስለፈጠረ ላለመሳተፍ ወሰንኩ።

ጽሑፉንም ከቶሮንቶ፣ካናዳ ማኅበረሰብ ጋር ባደረኩት ውይይት ላይ ሳቀርብ ትግሉ ያለፈባቸውን ምዕራፎች ዘርዝሬ፡ እሰካሁን የተጎናጸፍናቸውን ድሎች በማሰጠበቅ ወደሚቀጥለው ምዕራፍ መሸጋገር እንደሚያሰፈልግ አሰረዳሁ። በካልጋሪ ከተማ ደግሞ በ2018 ትግላችን ነባሩን አገዛዝ አስወግዶ በኦሮሞ ቡድን ከተተካ በኋላ የኦሮሞ ፖለቲካ ለሁለት መክፈሉን ገልጬ፤ እነሱም ሥልጣን የያዙት እና ወደ ትግሉ የተመለሱት መሆናቸውን አመላከትኩ። የሕዝብ እና የሀገር ሰላምን ለማሰጠበቅ ሁለቱን ኃይሎች ማቀራረብ እንደሚያሰፈልግ እና ይህን ለማሳካት ትርክት ማሰተካከል እንዳለብን ተናገርኩ። በኤድመንተን ከተማ፡ አንድ የብሔር ትግል ተሳክቶለት ሥልጣን ሲቆናጠጥ ውስጣዊ ክፍፍል ሰለሚባባስ ብዝኅነትን ማሰተናገድ የሚያሰችል የፖለቲካ ሥራ አስፈላጊ ሰለመሆኑ የሚያትተውን የጽሑፉን ክፍል አቀረብኩ።

በዚያ የዲያስፖራ ጉዞዬ ወቅት ከኦሮሞ ማህበርሰብ ጋር ከማደርገው ሰብሰባዎች ጎን ለጎን ከአማራ፣ ትግራይ፣ ሶማሌ እንዲሁም ኤርትራ ምሁራኖች እና አንቂዎች ጋርም በመገናኘት

ሁሉም ጦርነቶች ቆሞ ሰላም እንዲሰፍን የድርጃቸውን ሚና እንዲጫወቱ አወያያቸው ነበር። በተለይ ከትግራይ ምሁራን እና አመራሮች ጋር ባደረኳቸው ውይይቶች ለጊዜው ቆሞ የነበረው ጦርነት ዳግም የመፈንዳች አዝማሚያ ላይ ሰለነበር እንዲያሰቆሙ ወተወትኩ። ላሳምናቸው የቻልኩ አልመሰለኝም፡ ጦርነቱም እንደፈራሁት ነሀሴ 2022 አገርሾቶ በክልሉ ሀዝብ ላይ ተጨማሪ ወድመች አሰከተለ።

በዚህ መልኩ የውጪውን ማኅበረሰብ ውይይት አጠናቀቅኩ። በርግጥ ያ ጉዞ ትልቅ ማህበራዊ አና ፖሊቲካዊ ዋጋ አሰከፍሉኛል። ረጅም ጊዜ አብረን ከሠራን ንደኞች እና ባልደረቦች ጋር ቢያቃቅረንም፡ የፓለቲካ ገበያውን ከጦርነት ወደ ሰላም ለመቀየር የያዝኩትን ዓላማ ማሳካት ችያለሁ። ብዙም ሳይቆይ የትግራይ ጦርነት በፕሪቶሪያው ሰምምነት ቆመ። የኦሮሚያ መንግሥት እና የኦሮሞ ነጻነት ሠራዊትም ለድርድር ታንዛኒያ ተገናኙ። ያነ ሰለ ሰላም ሰዕሰብክ ከሃዲ አድርገው የፈረጁኝ ግንባር ቀደም የሰላም አርበኛ ሆነው ብቅ አሉ።



2013 ሃጫሉ ከባልደረቦቹ ጋር ለኦሮሚያ ቲያ ኮንሰርት አሜርካ በመጣ ወቅት፣ በኦሃዮ ግዛት ኮለምበስ ከተማ ተገናኘን። አብሮን ያለዉ የሁለታችንም ጋደኛ ፈይሳ ፋጂ ነዉ።



ሀገር በገባሁ በማግስቱ አምቦ ስሄድ ሃጫሉ ቀድሞኝ ደርሶ ሲቀበለኝ።



ወደ ሀገር ከተመለስኩ በኃላ ሃጫሉ ባረፍኩበት ኢሊሊ ሆቴል ሊጠይቀኝ በመጣበት ወቅት ስንቀላለድ።



ከንቲባ ታከለ ኡማ እና ሌሎች የመንግስት ኃላፊዎች ጋር በኦሮሞ ባህል ማዕከል ተገናኝተን በሀጫሉ አስከሩን ሽኝት ጉዳይ ላይ ስንወያይ። በእለቱ መጥተዉ የከበቡን የመከላከያ አባላት‹‹ከንቲባ ታከለን አግታችኃል ተበለን ነዉ የተላክነዉ›› ቢሉንም፣ ከታሰርኩ በኃላ መንግሥት ከንቲባ ታከለም ሆነ ባለስልጣን በቦታዉ እንዳልነበሩ ፍርድ ቤት ቀርቦ። ፎቶ ግን አይዋሽም።





የሀጫሉን አስክሬን በኦሮሞ ባህል ማዕከል ስሰናበት።



በመከላከያ እና ፖሊስ ወታደሮች መካከልየተፈጠረዉን ፍጥጫ ማረገብ በሚቻልበት ዘዴ ላይ በቦታዉ ከነበረዉ የኦሮሚያ ፖሊስ ኮማደር ጋር ስንወያይ።





እኔ ተይዤ ከቦታው ስወሰድ እራሱን የገደለው የፖሊስ አባል መገርሳ ጌቱ፣ ትውልዱ ሆሮ ጉዱሩ ወለጋ ዞን፣ ጉዱሩ ወረዳ ኮምቦልቻ ከተማ ነው።



የኛ መታሰር በቦታዉ የነበሩ የኦሮሚያ ፖሊሶችን መሣሪያቸዉን በመጣል እና የደንብ ልብሳቸዉን በማዉለቅ ተቃዉሞዎውኑን ከበለጹት የፖሊስ አባላት ክፉኛ አስቆጥቶ ነበር።

መካከል ሳጅን እያሱ ታምራት



የፌደራል ፖሊስ መጀመሪያ ወደ ፍርድ ቤት የወሰደኝ እለት ለሚቀጥሉት ወራት መመላለሻዬ ወደ ሆነችዉ ብረትለበስ መኪና ስገባ።




ቃሊቲ እስርቤት አቀባበል ያደረጉልን በረሮዎች። ቃሊቲ የምግብ ማብሰል ተራዬ እለት።



ሊጠይቀን የሚመጣዉን ሕዝብ የምናነጋግርበት ቦታ




በእስር ክፍላችን የነበረችዉ ጠረጴዛ በምጽሐፍ እና ይህን መጽሐፍ የማርቀቁ ሥራ እንደጉድ የሚረዝመዉን መድኃኒት የተሞላች ስለነበር ላይበረሩ
እና ፋርማሲ የእስር ቤት ጊዜ ለመቃቃም ረድቶኛል። በአንድ የተጣመሩ ይመስል ነበር።



የቃሊቲ እስር ቤት ዉጫዊ እና ዉስጣዊ ገጽታ።



በትግሉ ወቅት በማኅበራዊ ሚዲያ እየቀረበ በሚዲያ ከሚሰሙት የተፋነነ ወሬ ስጋት እና ፍርሀት የሚያዩንን ሊገድለኝ ሲዝት የነበሩ ቴዲ ማንጁስ
ታስሮ የእስር ቤት ጠባቂ ፖሊሶች በማረጋጋት እና በማግባባት ቃሊቲ ስለጠበቀኝ፣ የቀድሞ ጠላትነታችን ግንኙነታችን ቤተሰባዊ መልክ
እንዲይዝ እናደርግ ነበር። ቀርቶ የጸጉር አስተካካዬ ሆነ።






ከበቀለ እና ሀምዛ ጋር ወደ ፍረድ ቤት ለመሄድ ዩኒፎርም ለብሰን ልጄ ኦሮሞ ከእናቱ አርፋሴ ጋር በመሆን ቢጫ ስዝንዘጋጅ። ቃሊቲ እስር ቤት
የተፈረደባቸዉ ሰዎች ቀይ፣ በክስ ሂደት ለብሶ እኔ አንድፈታ የሚጠይቅ መፈክር ይዞ። ላይ ያሉ ደግሞ ቢጫ ዩኒፎርም ይለብሳሉ።






በረሃብ አድማ ላይ በነበርንበት ወቅት ደጋፊዎቻችን ቢጫ ንቅናቄ የሚባል ተቃዉሞ ያካሂዱ ነበር። እኛ ተከሳሾች የምንለብሰዉ ዩኒፎርም ቀለሙ ቢጫ
ስለነበር፣ እነሱም ቢጫ እየለበሱ ችሎት መታደም ጀመሩ። ፍርድ ቤቱ ድርጊቱን ሲያግድ የመንግስ ኃይሎፍ ብዙዎችን አፍሰዉ አሰሩ።



በረሀብ አድማው ወቅት እንደወትሮው ቆመን ጠያቂ ማናገር አቅቶን ቤተሰብ እና የሀገር ሽማግሌዎች በተኛንበት ያናግሩን ነበር።



የረሃብ አድማው ከመጠን በላይ ወፍሮ የነበረውን አካሌን አመንምኖት።



በረሃብ አድማ ላይ በነበርንበት ወቅት እየተመላለሱ እኛን እና መንግስትን ሲማጸኑ የነበሩ የሀገር ሽማግሌዎች።





የረሃብ አድማው ከውፍረት ከገላገለኝ በኋላ ዳግም ላለመወፈር ጣሳዎችን በአፈር ሞልተን ባዘጋጀነው ክብደት ስፖርት መስራትን እንዲሁም ከፖሊሶች ጋር መረብ ኳስ መጫወትን አዘወተርኩ።



አትሌት ደራርቱ ቱሉ የረሃብ አድማውን ያስቆመችን ቀን ለብሳው የመጣችው ቀሚስ



በእስር ወቅት ሲረዱን ከነበሩ ጠበቆች እና ሀኪሞች ጋር።





እስር ላይ ሳለሁ አርቲስት ዮሰን ጌታሁን ቡሎ የሚል ዘፈን እኔን በፈረስ
አስመስሎ ዘፍኖ ስለነበር፣ ስለቀቅ ሕዝቡ ብዙ ፈረሶችን በስጦታ
አበርክቶልኝ ነበር።



ከተፈታሁ በኋላ በእስር ቤት በከረዩ ስታይል አሳድጌው
የነበረውን ጸጉር ከባህሉ ልብስ ጋር ፎቶ ተነስቼበት
በዚያው ሰሞን ለተገደሉት የከረዩ አባገዳዎች
መታሰቢያ አደረኩት።





ሊጠይቁኝ ከመጡት ውስጥ በምዕራብ አርሲ አጄ አካባቢ የአጋዚ ጦር ሕዝቡን በፈጀበት
ወቅት የተጋፈጡት ጀግኖቹ ደራራ ጉዬ እና አደም ጉቶ ይገኙበታል።




ከእስር መፈታቴ እንደተሰማ በየቀኑ መቶዎች ስጦታ ይዘም እየመጡ ደስታቸውን ይግለጹ ነበር።




ከእስር ቤት ከወጣሁ ከወራት በኋላ የኢትዮጵያን ዜግነት ዳግም ለመውሰድ ቃለ መሃላ ፈፅሜ
የሁለት ዓመታት "ሀገር አልባነቴም/Statelessness" አበቃለት።



የኢትዮጵያ ሀገር ሽማግሌዎች ማኅበር አመራሮች ወደቤቴ መጥተው በሀገራችን ሰላም ማስፈን የሚቻልበት ሁኔታ ላይ በተወያየንበት ወቅት።



የጎሮ ትምህርት ቤት አስተማሪዬን እና በስኮላርሺፕ የላከኝን መምህር አበራን ዳግም አገኘሁት።



በስታንፎርድ ዩኒቨርሲቲ አማካሪዬ የነበሩትን ፕሮፌሰር ላሪ ዳይመንድ ከበቀለ ገርባ ጋር በጎበኘንበት ወቅት።



በኮሎምቢያ ዩኒቨሲቲ የPhD አማካሪዬ የነበሩትን ፕሮፌሰር ማህሙድ ማምዳኒን
ከእስር ከተፈታሁ በኋላ ነው ኒው ዮርክ ሄጄ አገኘኋቸው።



ከእስር ቤት እንደወጣሁ ከእባዬ (እናቴ) ጋር



በእስር ቤት በነበርኩበት ወቅት ሥራዋን አቁማ በየቀኑ ምግብ ስታመላልስልኝ ከነበረችው ታላቅ እህቴ ራቢያ ጋር



ከእስር ቤት ስፈታ ያረፍኩበትን ቤት ካዋሱኝ ታዋቂዋ ባለሀብት እና እንጋፋ ታጋይ ማኪያ ማሚዮ (ኡሚ) ጋር



ከእስር በኋላ ከዶ/ር ኢሊሊ ጋር ተጋብተን ፈጣሪን ለማመስገን ወደ መካ እቀናን።




ከሬድዋን አማን (ማጂክ) እና ዩሱፍ በሺር ጋር ከእስር እንደተፈታሁ የተነሳነው ፎቶ። ሁለቱ ወጣቶች በውጭ ሀገር ሳደርግ የነበረውን ትግል ሲያግዙኝ ቆይተው ወደ ሀገር አብረውኝ ከመጡ በኋላ አብረውኝ ታሰሩ። ቀድመውኝ ሲፈቱ ወደ አሜሪካ ከመመለስ ይልቅ ኢትዮጵያ ቆይተው ቤተሰቤን መንከባከብን መረጡ።



ከእስር በኋላ ወደ አሜርካ ተጉዤ የመጀመሪያ ልጄን ኦሮሞን አገኘሁት



ከልጆቼ ቁሮ እና ቀብሶ ጋር የአባቶችን ቀን ስናከበር

## እንደ መውጫ

በዚህ መጽሐፍ ውስጥ ከልጅነቴ ጀምሮ አመለካከቴን በመቅረጽ ረገድ ሚና የነበራቸውን ማኅበራዊ፣ ኢኮኖሚያዊ እና ፖለቲካዊ ሁነቶች፣ በትምህርት ቆይታ የቀሰምኩትን እውቀት እና በዓለም ዙሪያ ባደረኩት ጉዞ ያዳበርኩትን ልምድ በማጣመር ኋላ ላይ የተሳተፍኩበትን፣ ብሎም የመሪነት ሚናን ተጫውቼ ፈር ማስያዝ የቻልኩትን የትግል ሂደት ዳስሻለሁ። ያለፍኩባቸውን ሁሉንም ክስተቶች ዘርዝሬ ለመጻፍ ጊዜውም፣ወረቀቱም ስለማይበቃ ለአንባቢ ቢደርሱ ይጠቅማሉ ያልኳቸውን ለመምረጥ ተገድጃለሁ። አንባቢ እንደሚረዳው፡ ጽሁፉ የእኔን፣ የሕይወት ጉዞም ሆነ የቄሮ ትግል ታሪክ በተሟላ ሁኔታ የሸፈነ ሳይሆን፣ በሁለቱም ላይ ቅንጭብጫቢ ትውስታዎቼ የስፈሩበት ነው። መጽሐፉ የሚተርከውን የ36 ዓመታት (1985-2022) የሕይወት ጉዞዬን ስፋት፣ ብዛት እና ውስብስብነት መለስ ብዬ ሳስበው ለራሴም ይገርመኛል። አሁን መጽሐፉ በሚታተምበት ወቅት 38 ዓመቴ ሲሆን ኦሮሞ፣ ቄሮ እና ቀብሶ ብዬ ስም ያወጣሁላቸው የሦስት ወንድ ልጆች አባት ነኝ።

ይህን መጽሐፍ ማርቀቅ እና መልሶ ማንበብ ያለፍኩበትን የፓለቲካ ሕይወት መለስ ብዬ እንድዳስስ እና በጥሞና እንዳጤን ዕድል ስጥቶኛል። በፓለቲካ ጉዞዬ ላይ ካደረኩት ግምገማ በመነሳትም ርዕሱ "አልፀፀትም" እንዲሆን መረጥኩ። ከጠዋቱ በተጠናወተኝ የትግል መንፈስ ኃይል ተነሳስቼ የተወለድኩበትን ሕዝብ ከጭቆና የማውጣት ዓላማን ለማሳካት በመትጋት ሂደት ውስጥ በተደጋጋሚ ሕይወቴን ከጫፍ ላደረሱ አደጋዎች ተጋልጫለሁ። ለቅስም ሰባሪ የስም ማጥፋት ዘመቻዎች ተዳርጌያለሁ። በቀስምኩት ትምህርት እና ሙያ የግል ሕይወቴን እና የቤተሰቤን ኑሮ ለማሻሻል የነበረኝን እድል ወደ ጎን ትቻለሁ። ሆኖም፣ ማንኛውም የከፈልኩት መስዋዕትነት ትክክለኛነቱ ላመንኩበት ዓላማ የተከፈለ፣ ተከፍሎም ውጤት ያስገኘ ስለሆነ አልቆጭም። ለዚህም ነው የመጽሐፉን ርዕስ “አልፀፀትም” ያልኩት።

ይህ ማለት ግን የፖለቲካ ሥራዬን መለስ ብዬ ስዳስስ ምንም ስሕተት አላገኘሁም ለማለት አይደለም። እንዲያዉም አሁን በደረስኩበት አመለካከት እንዲሁም በዕድሜ እና ልምድ ኮሚገኝ ግንዛቤ ላይ ቆሜ ወደኃላ ስመለከት ብዙ ለየት ባለ መልኩ መሰራት የነበርባቸው ጉዳዮች ይታዩኛል። ሆኖም እነዚያ ስህተቶች የተከስቱት ለስኬት ከነበረኝ ጉጉት እንዲሁም በከፍተኛ ጫና ሥር፣ በአነስተኛ ልምድ፣ በቂ ባልሆነ ቁሳዊ እና ስብዓዊ ግብዓት እቅርቦት ሁኔታ ውስጥ በተወስዱ እርምጃዎች የተፈጸሙ በመሆናቸው ነው። ከግለስቦች እና ቡድኖች ጋር ግጭት ውስጥ ስገባ የነበረውም ትግሉን በፍጥነት ለማሳካት በማሰብ በወሰድኳቸው እርምጃዎች እና ውሳኔዎች እንጂ ማንንም ለመጉዳት አስቤ አልነበረም።

የተወለደኩበት ሕዝብ ላይ የሚደርስውን ጭቆና የተወሰነውን በገዛ ዓይኔ አይቼ፡ ሌላውን ከታላላቆቼ ሰምቼ፡ በቀደምት ታጋዮች ታሪክ ተማርኬ፡ በልምድ እና በትምህርት ባገኘሁት ግንዛቤ ተመርቼ ሕዝቤን ከመድሏዊ አገዛዝ ነጻ የማውጣት ሕልሜን ለማሳካት ብዙ ጥሬያለሁ።

ሕዝባችንን በፈጣን ልማት ከድህነት አረንቋ የሚያወጣ ዴሞክራሲያዊ ሥርዓት ለመገንበት የነበረን ምኞት እስካሁን ከዳር ባይደርስም፡ ያደግንበትን የጭቆና ሥርዓት ተመጣጣኝ በሆነ መሥዋዕትነት በስትራቴጂ ተመርተን መገርስሳችን ያኮራኛል። የቀረውን ከዳር ለማድረስ በተረፈው ዕድሜያችን እንለፋለን፣ ያልቻልነውን ጀኔራል ዋቆ ጉቱ እንዳለው የሚቀጥለው ትውልድ እንዲያሳካ እንቀርጻለን። የትግል ትውሳታዎቼን በመጽሐፍ መልክ ለማጠናቀር ያነሳሳኝም ይሄው ነው።

ተደጋጋሚ ችችት የሚቀርብባቸውን ዋና ዋና የፓለቲካ ውሳኔዎችን መለስ ብዬ ለመገምገም ሞክሬያለሁ። አንዱ እና ዋነኛው ትችት የብሔር ፖለቲካ ማራመዴ ነው። በተለይ ከለውጡ በኋላ ከተባባሰው የብሔር ክፍፍል እና ግጭት እንጻር ይህንን ጉዳይ ደግሜ ደጋግሜ ሳስብበት ከርሜያለሁ። የትችቱን መነሻ ብረዳውም 'ሌላ ምርጫ ነበረኝ ወይ?' የሚል ጥያቄ ያጭርብኛል። እኔን ወደ ፓለቲካ ያስገባኝን እና በዚህ መጽሐፍ ውስጥ ያስፈርኩትን ከውልደት እስከ ጉልምስና ያለፍኩበትን ነባራዊ ሁኔታ ስገመግም 'አማራጭ አልነበረኝም' ወደሚል መደምደሚያ ያደርሰኛል። በገዛ ቀዬው ለኢኮኖሚያዊ ብዝበዛ፣ ብሔር-ተኮር የማንነት መደፍጠጥ፣ ንቀት እና መዋረድ ከተጋለጠ ሕዝብ ተወልጀ፣ የብሔር ጭቆናን ለማስወገድ ሲታገል ከነበረ ቤተሰብ እሳቱ የሚንቀለቀል የትግል ችቦ ወራሽ ሆኛለሁ። በተጨማሪም ብሔርን መሠረት ያደረገ ግጭት እና ፕሮፓጋንዳ በተጧጧፈበት የፓለቲካ ምህዳር ውስጥ አድጌ፣ ሕዝቤን ከችግር ለማላቀቅ የብሔርተኝነት ፖለቲካን ከማራመድ ውጪ ሊያስኪድ የሚችል መንገድ የነበረ አይመስለኝም። በተለይ ደግሞ ከፍ ያለ የፓለቲካ ተሳትፎ የጀመርኩት የኦሮሞ ትግል በመዳከሙ ምክንያት "ኦሮሞ ለሃምሳ ዓመት ታግሎ ምንም ለውጥ አላመጣም፣ 50ሚሊዮን ሆኖ ከ2 ሚሊዮን በወጣ አገዛዝ ይረገጣል" በሚሉ ከግራ እና ቀኝ በሚስነዘሩ የንቀት ንግግሮች ሕዝባችን ለሞራል ስብራት የተጋለጠበት ጊዜ ነበር። እናም ባለኝ አቅም ሁሉ ትግሉን ውጤታማ ለማድረግ ይህን ሕዝብ ከንቀት እና ከሞራል ስብራት ማስወጣት አለብኝ የሚል አልህ ውስጥ አስገባኝ። ተሳክቶልንም ዛሬ እነዚያን የንቀት አባባሎች የማንስማበት ደረጃ ላይ ለመድረስ በቅተናል።

እንዳንዶች እንደሚከሱኝ የብሔር ፖለቲካን ሳራምድ የነበረው ሌላውን ማኅበረሰብ በመጥላት ወይም ለመጉዳት በማሰብ አይደለም። ማንኛውም ብሔር በግል ያደረሰብኝ ጉዳት ስለሌለ ለጥላቻም ሆነ ለበቀል ሊያነሳሳ የሚችል ግላዊ ምክንያት አልነበረኝም፤ የለኝምም። እንዳንድ ግለሰቦች ወይንም ቡድኖች ማንነቴ ላይ ያተኮሩ ተደጋጋሚ ነቀፋዎችን ሲሰነዝሩብኝ የቆዩ ቢሆንም እነዚህን ክስተቶች ዛሬም ቢሆን የፖለቲካ ትኩሳቱ ውጤት እንጂ እንደየትኛውም ሕዝብ ነፀብራቅ አድርጌ አልመለከታቸውም። ሕልሜ የኦሮሞ ሕዝብ በማንነቱ ከሚደርስበት ጭቆና ተላቆ ከሌላው ማኅበረሰብ ጋር በፍትሃዊ እኩልነት ለመኖር የሚያስችለውን ፓለቲካዊ አቅም መገንባት ስለነበር፡ ሕዝባችን ከጎንዮሽ ሽኩቻ ይልቅ የጭቆና ሥርዓቱ ላይ እንዲያነጣጠር ሳልታክት ሰርቻለሁ። በዚህም ተሳክቶልን በአራት ዓመቱ የቄሮ ትግል ወቅት፣ በትግራይ ማኅበረሰብ ስም ሥልጣን በተቆናጠጠው የሕወሓት አገዛዝ ላይ ያነጣጠረ ትግል ስናደርግ በኦሮሚያ የሚኖሩ የብሔሩ ተወላጆች ጥቃት ሳይደርስባቸው ለውጥ ማምጣት ችለናል። አገዛዙ ሊፈጥራቸው ሲሞክር የነበሩትን የጎንዮሽ ግጭቶች በማክሸፍ ኦሮሚያ ውስጥ ይከስታል ተብሎ ሲፈራ የነበረውን የብሔር ገጭት በማስቀረት ረገድ ተሳክቶልናል። በአጠቃላይ እንድን ስው ወደ ማንነት ፖለቲካ የሚያስገባው ዋናው ምክንያት በማንነት ላይ

የተመሠረተ ጭቆና እና መድሎ የሚፈጽም አገዛዝ ነው። ይሁን እንጂ ማንነትን መሰረት ያደረገን ጭቆና በማንነት ተደራጅቶ መታገል ግድ ቢሆንም የሚደረገው ፖለቲካዊ ትግል በጨቋኙ አገዛዝ ላይ እንጂ በማኅበረሰብ ላይ እንዳያነጣጥር መጠንቀቅ አስፈላጊ ነው። ይህ ጥንቃቄ የሚያዕፈልገው ለሌላው ማኅበረሰብ ከማሰብ እንጻር ብቻ ሳይሆን የትግሉን እቅም በጎንዮሽ ፣ኩታ ማጣክን የአገዛዙን ዕድሜ ስለሚያራዝም ነው። ብሔርተኝነት (nationalism) ከፍተኛ የፖለቲካ ማታገያ ኃይል መሆኑ እሙን ቢሆንም በጥንቃቄ እና በብልሃት ካልተያዘ ሊያደርስ የሚችለውን እደጋ መንንዘብ አስፈላጊ ነው። የራስን ወገን በመውደድ እና ሌላውን በመጥላት መካከል ያለው መስመር በጣም ቀጭን ከመሆኑ የተነሳ እንድ ብሔርተኛ በራስ ወገን ላይ የሚደርስን ጭቆና ሲቃወም ከርሞ፣ በገልባጩ በሌላው ወገን ላይ የሚፈጸመውን በደል ወደ መደገፍ ሊሻገር ይችላል።

ኢትዮጵያን እስከዛሬ ያስተዳደሩ አገዛዞች ሁሉ በአምባገነናዊ ሥልጣናቸው ለመቆየት ሲሉ መድሎን ሲፈጽሙ ቆይተዋል። የመድሎው ገፈት ቀማሾች ደግሞ በብሔር ተደራጅተው በመታገል አገዛዞቹን ለመቀየር ችለዋል። እንዱ እምባገነን ወርዶ ሌለው ሲመጣ ግን የተበዳይ ቦታ መለዋወጥ ካልሆነ በስተቀር፣ ታጋዮች የተዋደቁለት ሁሉንም ሕዝቦች ፍትሃዊ እኩልነት ያጎናጸፈ የፖለቲካ ሥርዓት እስካሁን መገንባት እልተቻለም። አገዛዞቹ በስሙ ሥልጣን የሚቆናጠጡት ማኅበረሰብም ምናልባት ከባሕል እና ከቋንቋ ጋር የተቆራኘ የሥነ- ልቦና የበላይነት ያገኝ ይሆናል እንጂ፣ በነጻነት የመኖርን እና በልማት ከድህነት የመላቀቀ ዕድል እላገኘም። ይህን በመረዳት የሁሉንም ዜጎች እና የማኅበረሰብ ቡድኖች መብት እና ጥቅም ፍትሃዊ በሆነ መልኩ የሚያስከብሩ እንዲሁም ዴሞክራሲያዊ ሥርዓት ለመገንባት የሚያስችሉ በጋራ ሲደረጉ የነበሩ ሙከራዎች እስካሁን እልተሳኩም። ዛሬ ላይ ሁሉም ወገን ጭቆና እና መድሎን በየተራ ስለቀመስ፡ ለጋራ ትግለ የተሻለ ግንዛቤ ያለ ይመስላል። ከዚያ ውጪዉ የሀገራችን ሕዝቦች እሁን ከደረሱበት የብሔር ንቃት እንጻር እንደድሮው እንዱን ጨቁኖ በሥልጣን ለመቆየት የሚስችል ሁኔታ ዘመን አልፎበታል። ይህንን መሞከር ለከፋ የእርስ በእርስ ጦርነት እና ሀገራዊ ውድቀት እንደሚዳርግ በተጨባጭ እያየነው ስለሆነ ያልተሞከረውን ዴሞክራሲያዊ መንገድ መሞከር ይሻለናል።

ሁለተኛው ትችት የኢሕአዴግን አገዛዝ ሙሉ በሙሉ ገልብጠን ሥር-ነቀል ለውጥ ከማካሄድ ይልቅ በሥርዓቱ ውስጥ ያሉ ለውጥ ፈላጊዎች ሥልጣን እንዲይዙ መወሰናችን ነው። በዚህ መጽሐፍ ውስጥ ደጋግሜ እንደጠቀስኩት ይህንን መንገድ የመረጥንበት ምክንያት የአረብ ሀገራት የገጠማቸውን ዓይነት ለእርስ በእርስ ጦርነት የመጋለጥ እደጋ ለመቀነስ እና ወደ ዴሞክራሲ የመሻገር ዕድላችንን ለማስፋት ነበር። የተከተልነው መንገድ በአነስተኛ መስዋዕትነት እና በተሻለ ፍጥነት ለውጥ ለማምጣት ያስቻለን ቢሆንም የፈራነውን የእርስ በእርስ ጦርነት ማስቀረት ወይም ወደ ተመኘነው ዴሞክራሲ ሊያሸጋግረን አልቻለም። ከዚህ በመነሳት ስልታችን የተሳሳተ እንደሆነ ይተቻል። ይህን ጉዳይ መለስ ብዬ ደጋግሜ በእትኩሮትእጥንቼዋለሁ።

ሥርዓቱን ከመገልበጥ መቀየር የሚለው ስልታችን እስከ ለውጡ ዋዜማ ድረስ ባቀድነው መልኩ ስርቶልናል። ከአብዮታዊ ይልቅ ጥገናዊ ለውጥን ያለመ ስልት መከተላችን ሀገረ-መንግሥቱን ሊበታትን የሚችል የከፋ ግጭት እና ውድመት ሳይደርስ እንዲሁም ሀገራዊ ተቋማት ሳይፈራርሱ ወደ ሽግግር ጎዳና ለመግባት እስችሏል። ያልተሳካው የእቅዳችን ቀጣይ

ምዕራፍ የሆነው ህገሪቷን ወደ ዴሞክራሲያዊ ሥርዓት ማሸጋገር ነው። ለሽግግሩ መጨናገፍ ዋናው ምክንያት እቅድበምንነድፍበት ወቅት ለመገመት አዳጋች የሆኑ ሁነቶች ስላጋጠሙ ነው። ለምሳሌ፡ ከተቃዋሚ ይልቅ ከኢሕአደግ ውስጥ ለውጥ ፈላጊ አመራር ሥልጣን ቢይዝ የግጭት ዕድልን ለመቀነስ ይረዳል የሚል ተስፋ ነበረን። ምክንያቱም ከኢሕአደግ ድርጅት አብራክ የወጣ መሪ ሥልጣን ቢይዝ ከተቃዋሚው የበለጠ ከሕወሓት ጋር ይቃረናል ብለን ልንገምት እንችልም ነበር። እንዲሁም በሥርዓቱ ውስጥ ያደገ ሰው ኋላ እንዳየነው ከኢሕአዴግ ብዙ የራቀ ርዕየተ-ዓለም ይኖረዋል ብሎ መተንበይ ይከብዳል። ይህ ደግሞ የእኛ ብቻ ሳይሆን የሕወሓት አመራሮችም ግምገማ ነበር።

ጠ/ሚ ዐቢይ ግን የኢሕአዴግ መሠረታዊ አቋሞች የሚባሉትን እንደ ፌደራሊዝም ያሉትን የሚጻረር ብቻ ሳይሆን እኛ በጥድፊያ ቢፈርስ ህገራዊ አደጋ ያስከትላል ብለን ጥገናዊ ለወጥ የመረጥንለትን ኢሕአዴግን ለማፈራረስ ያቀደ መሪ ሆኖ ብቅ አለ። የግራ ዘመም ፓሊቲካ አራማጅ በሆነ ድርጅት ውስጥ አድጎ የቀኝ ዘመም አይዲዮሎጂ አቀንቃኝ ሆኖ ተከሰተ። ከሕወሐት መሪዎች ጋርም ከተቃዋሚ አመራሮች የበለጠ ግለሰባዊ ተቃርኖ ያለው ሆኖ ተገኘ። በሕዝባዊ አመጽ ወደ ሥልጣን የመጣ አመራር ኢሕአዴግን ለውድቀት ከዳረገው አምባገነናዊነት በመማር ወደ ደዴሞክራሷያዊ ሥርዓት መሸጋገርን ይመርጣል ብለን ተስፋ ያደረግን ቢሆንም ጠ/ሚ ዐቢይ ግን በአንድ ፓርቲ ሲመራ የነበረን አገዛዝ በአንድ ግለሰብ በሚመራ አምባገነናዊነት የመተካት እቅድ እንግቦ ተከሰተ። ይሄም ልናስቀረው ላሰብነው የእርስ በእርስ ጦርነት ተጋላጭ አደረገን።

ሦስተኛው ትችት ደግሞ ከዐቢይ ጋር የነበረኝ ግንኙነት ለሽግግሩ አለመሳካት ጉልህ አስተዋጽኦ አለው የሚል ነው። በአንድ ወገን ዐቢይን ከመጀመሪያው መቃወሜ ቂም እና አለመተማመንን በመፍጠር አብሮ በመሥራት ሽግግሩን ለማሳካት የነበረንን ዕድል አክሽፏል የሚሉ አሉ። በሌላ ወገን ደግሞ መጀመሪያ በያዝኩት ተቃውሞ ከመቀጠል ይልቅ አቋሜን ቀይሬ ሕዝቡ የለውጡን አመራር እንዲደግፍ መምከሬ፣ ቄሮን ከትግል ስሜት በማስወጣት ዐቢይ ያለከልካይ ሥልጣኑን እንዲያደላድል አስችሎታል የሚል ነው። ይሁን እንጂ በዐቢይ አመራር ሥር ሽግግሩ ሊገጥመው የሚችለውን አደጋ አስቀድሜ መርምሬ ከደመደምኩ በኋላ፣ የእሱን መሸም ባልቃወም ኖሮ ዛሬ ሕዝቡ ምን ይለኝ ነበር? ህሊናዬ ዕረፍት ያገኝ ይሆን? አስቀድሜ ከማስጠንቀቅ ይልቅ ካለፈ በኋላ ብናገር ጥቅሙ ምንድነው?

ዐቢይ ሥልጣን ከያዘ በኋላ ተቃውሞዬን አቁሜ ልዩነቴን እንደያዝኩ ከመደገፍ ይልቅ በተቃውሞ መቀጠልም አስቸጋሪ ነበር። በተጋጋለ የድል እና የለውጥ ስሜት ውስጥ የነበረው ሕዝብ የተቃውሞዬን ምክንያት ለመረዳት በሚያመች ሁኔታ ውስጥ አልነበረም። ከ50ዓመታት ትግል በኋላ የተገኘ ድል ልታጨናግፍ ነው፤ የመጀመሪያውን የኦሮሞ መሪ ማደናቀፍ ተገቢ አይደለም፤ ማንም ይሁን ማን ከወያኔ አይብስም !" በሚሉ እና በመሳሰሉ ሐሳቦች ከቅርብም ከሩቅም ይወተውቱኝ ነበር። ሀገሪቷ ወደ መረጋጋት እንድትመለስ በመመኘት እና በሌሎች ምክንያቶች የተነሳሱ የሌላ ሀገር አመራሮች ጭምር ሕጋዊ፣ ፖለቲካዊ እና አካላዊ ጫና ሲያደርጉብኝ ነበር። ይህን ሁሉ ውትወታ ተቋቁሜ ተቃውሞዬን መቀጠል ግብዝነት ሆኖ ስለታየኝ፣ ተቃውሞውን ትቼ ሽግግሩን ለጣሳካት ለአንድ ዓመት ተኩል ያክል ባለኝ አቅም ሁሉ ድጋፌን በቅንነት ለግሻለሁ።

ሽግግሩን ሊያደናቅፉ የሚችሉ ድርጊቶች እና ጉድለቶችን ስመለከት ትችት እና ምክረ-ሐሳብ በቃልም በጽሑፍም ለአመራሩ በቀጥታ በማቅረብ እርምት እንዲደረግ በተደጋጋሚ ወትውቻለሁ። የሀገሪቷ የፖለቲካ ልሂቃን የተስማሙበት የሽግግር ፍኖተ-ካርታ እንዲዘጋጅ፣ በትጥቅ ትግል የነበሩ ኃይሎች በአግባቡ ወደ ሰላማዊ ፖለቲካ እንዲገቡ፣ እኩርፈው እና ፈርተው የተገለሉ የቀድሞ አመራሮች ታርቀው ወደ ማዕከላዊ የፖለቲካ ምህዳር እንዲቀላቀሉ፣ ከጎረቤት ሀገራት ጋር የምናደርገው ግንኙነት ግለሰባዊ ሳይሆን ተቋማዊ እንዲሆን ለማሳመንም የተቻለኝን ሁሉ ሞክሬያለሁ። አመራሩ ግን ውትወታዬን ቢያዳምጥም ተጨባጭ የእርምት እርምጃ መውሰድ አልፈለገም። በመቀጠል ትችቶቹን በግልጽ በሚዲያ በማቅረብ ሕዝባዊ ጫና ለመፍጠር ሞከርኩ። ይህም ሳይሳካ ሲቀርና ሽግግሩ ወደ መቀልበስ፣ ሀገሪቷም ወደ ክፉ አደጋ እየገሰገሰች መሆኑን ስረዳ፣ ወደ ተቃዋሚ ጎራ በመቀላቀል ታቅዶ በነበረው ምርጫ ላይ አማራጭ ሐሳብ እና አመራር ለሕዝብ ለማቅረብ ወሰንኩ። የምርጫውን በኮሮና ወረርሽኝ ምክንያት መራዘም እንደ ዕድል ተጠቅመን አደገኛ ደረጃ ላይ ደርሶ የነበረውን የፖለቲካ ውጥረት እንድናረግብ የመጨረሻ ተማጽኖ ብናቀርብም ሰሚ ሳይገኝ ለእስር ተዳርጌ ከፖለቲካው መድረክ ተወገድኩ።

ከልጅነቴ ጀምሮ እስከ ትግሉ ወቅት ብዙ ፈተናዎችን ያስተናገድኩ ቢሆንም ወደ ኢትዮጵያ ከተመለስኩበት እስከ ታሰርኩበት ዕለት የነበሩት ሁለት ዓመታት በሕይወቴ ውስጥ ለከፍተኛ የአእምሮ ጭንቀት የተጋለጥኩበት ነበር። በትግሉ ወቅት ብዙ ችግሮች ቢገጥሙኝም ለችግሮቹ መፍትሔ የማምጣት ኃላፊነት በእጄ ነበር። በለውጡ ማግስት ግን የመሪነቱን ሚና ሌላ አካል ስለተረከበ፣ ስሕተቶች እና ችግሮችን ስመለከት ከመጮህ ባለፈ ለማረም አልቻልኩም። የነበርኩበትን ሁኔታ አውቶቡስን እንደ ምሳሌ በመወሰድ ላስረዳ፣ በትግሉ ወቅት አውቶቡሱ ከመንገድ ከወጣ መሪውን ጠምዝዞ መመለስ፣ ነዳጅ ከጎደለ መሙላት እና ተሳፋሪውከተስላቸ በተለያየ መልኩ ማነቃቃት እችል ነበር። በሽግግሩ ወቅት የአውቶቡሱ ሹፌርነት በሌላ ሰው እጅ ስለሆነ የረዳትነት ሚናን ወስጄ ልደግፍ ሞከርኩ። አውቶቡሱ ግን መንገድ እየሳተ፣ ነዳጅ እያፈሰሰ፣ በአደገኛ ፍጥነት እየተጓዘ መሆኑን ብጮህም ሾፌሩ ብቻ ሳይሆን በለውጥ እና በደል ስሜት ተውጦ ሲጨፍር የነበረው ተሳፋሪ ሊሰማኝ አልቻለም ነበር። ሁኔታው በእንቅልፍ ልባችን አስፈሪ ሕልም እያየን ብንጮህም የሚሰማንም ሆነ የሚደርስልን ሰው ስናጣ የሚሰማን ዓይነት የጭንቀት ስሜት ነበር፤ አውቶቡሱ ወደ ገደል እየገሰገሰ እያየ ማስቆም እንዳልቻለ ረዳት ሁሉ፡ በሕዝባችን ላይ እየመጣ ያለው ከፍተኛ አደጋ ወለል ብሎ እየታየኝ ምንም ማድረግ አለመቻሌ ከጊዜ ወደ ጊዜ የባሰ ጭንቀት ውስጥ ከተተኝ። መታሰሬ ከፖለቲካ ምህዳሩ አስወጥቶ በየቀኑ የሚከሰቱ ስሕተቶችን ያለ እንዳች መፍትሔ ከመታዘብ ገላገለኝ። ለረጅም ጊዜ ርቆኝ ከነበረው እንቅልፍም ታርቄ ጭልጥ ብቆ እንድተኛ ዕድል ስጠኝ።

በነገራችን ላይ በሕዝባዊ ንቅናቄ የሥርዓት ለውጥ ከመጣ በኃላ የታለመለት ዴሞክራሲያዊ ሽግግር ሳይሳካ የቀረው በሀገራችን ብቻ አይደለም። ቪንስንት በቪንስ (Vincen Bevins)የተባለ ጋዜጠኛ በቅርቡ ባሳተመው መጽሐፍ ውስጥ የቄሮ ትግል ሲካሄድ በነበረበት ዘመናት በብዙ ሀገራት ውስጥ ከወትሮው የበለጠ ተመሳሳይ ሕዝባዊ አመጾች የተካሄዱበት እንደነበር ያሳያል። ጥናቱ የሸፈነውን እ.አ.አ ከ2010 እስከ 2020 ዘመን የሕዝባዊ አመጽ የተፋፋመበት ነገር ግን አብዮታዊ ለውጥ ያልመጣበት አሥርት ዓመታት እንደሆነ ተንትኗል። በአረብ ስፕሪንግ፣ በደቡብ አሜሪካ፣ በኤዥያ እንዲሁም በአፍሪካ ብዙ ሀገራትን የናጡ እና

አገዛዞችን የገረሰሱ ሕዝባዊ ተቃውሞዎች ሲካሄዱ የነበሩ ቢሆንም በለውጥ ማግስት ሕዝቡ የተመኘውን ነጻነት፡ ፍትሕ እና ዴሞክራሲ መጎናጸፍ እንዳልቻሉ፣ እንዲያውም ከሐዝባዊ ትግሉ ዓላማ በተቃራኒው በቆሙ ኃይሎች ተጠልፈው የባሰ ጭቆና እና መከራ እንዳስከተሉ በቪንስ በግርምት ታዝቧል።

በአሥርት ዓመታቱ ወቅት ለእመጸቹ መፋፋም የማኅበራዊ ሚዲያ ተደራሽነትች መስፋፋትን እንደ አንድ ምክንያት አቅርቧል። ለታስበው ሥርነቀል ለውጥ እጦት ደግሞ አንዱ እና ዋነኛው ምክንያት ሕዝባዊ ንቅናቄቂዎች እንድን ጨቋን አገዛዝ ሲገረስሱ የሚፈጠረውን የሥልጣን ክፍተት ለመሙላት የሚያስችል የእስተሳስብ፣ የአመራርም ሆነ የአደረኛደት ቅድመ ዝግችት አለመኖሩ እንደሆነ ያትታል። ከዚህም የተነሳ የሽገግር ወቅት ፖለቲካን የለውጥ ንቅናቄውን ራእይ የማይጋሩ ምናልባትም የሚዳረሩ ኃይሎች እንዲጠልፉት አስችሏል ይላል።

በእኛ በኩል ይህንን የለውጥ መጠለፍ አደጋ አስቀደመን የተረዳን ሲሆን ለመቅረፍም የተለያዩ እርምጃዎች ለመውስድ ሞክረናል። ለአብነትም ጸረ-ለውጥ የሆኑ እና እምባገነናዊ አገዛዝ እንዲቀጥል ፍላጎት ይኖራቸዋል ብለን የገመትናቸውን ባለስልጣናት እንዲንለሉ ስርተን ነበር። በትግሉወቅት ኦሕዴድንከሕወሓት በመነጠል አገዛዙንለማዳከም እንደስራነው ሁሉ፣በለወጡ ዋዜማ ኦሕዴደን እራሱ ጸረ-ለውጡን “እሮጌው ኦሕደዴድ”፣ ለውጥ እራማጁን ደግሞ “ቲም ለማ" በሚል ከፋፈልነው። ዓላማችን ጸረ-ለውጡን ከሥልጣን በማራቅ ሽግግሩን የመጥለፍ ዕድሉን ማጥበብ፣ ለውጥ ፈላጊውን ደገሞ ለሕዝብ እንዲወግን እና የለውጥ እንቅስቃሴው አጋር እንዲሆን ለማድረግ ነበር። እሳቤው ከገዢው ፓርቲ የወጣው ኃይል ሥልጣን ይዞ ሲቀጥል ለውጡን ለመቀልበስ ቢፈልግ እንኳን አቅም እንዳይኖረው ለማድረግ ነበር።

ለለውጥ ጠለፋ ያለውን ዕድል የበለጠ ለማጥበብ ለማ ሥልጣን ከያዘ ጀምሮ ጸረ-ለውጥ እንደሆኑ የሚገመቱ ነባር የኦሕዴድ አመራሮች ከሥልጣን ተወግደው፣ አዳዲስ ወጣቶች ወደ ሥልጣን መጡ። ዐቢይ ግን የጠቅላይ ሚኒስትርነቱን ሥልጣን በያዘ በወራት ውስጥ፣ ለማ የጀመረውን እሮጌውን ኦሕዴድ በአዳዲስ ለውጥ እራማጆች የመተካት ሥራ መቀልበስ ጀመረ። ድሮውንም ለጊዜው በአማካሪነት ፅም ከሕዝብ እይታ ዞወር ተደርገው የነበሩ ነባር የኦሕዴድ አመራሮች ቀስ በቀስፅ ወደ ሥልጣን ሲመለሱ አዲስ ተሹመው የነበሩት ወጣቶች መገፋት ጀመሩ። ይህ ተሃድሶን የመቀልበስ ሂደት፣ ለማ ከኦሮሚያ ፕሬዝዳንትነት ከተነሳ
ወዲህ በስፊው ተጧጧፈ። የተወስኑ አዲስ ገቢዎች ከመቀነስ የተረፉ ቢሆንም፣ ጸረ-ለውጥ አቋም ተቀብለው መገንባት ለጀመረው እምባገነናዊ አገዛዝ ግንባር ቀደም ጋሻ ጃግረ ሆኑ፡ እነሱም ቢሆኑ አገዛዙ እየተደላደለ ሲሄድ አንድ በአንድ ከመወገድ አልዳኑም።

በአጠቃላይ ለታለመው የዴሞክራሲ ጀግግር አለመሳካት እኔ ከጠቀስኳቸው በተጨማሪ ብዙ ፓለቲካዊ እና ማኅበራዊ ምክንያቶች ሚና ኑረቸው ይሆናል። እነዚህን ምክንያቶች ምሁራኖች በጥልቀት በማጥናት የተሟላ ትንተና እንደሚስጡ ተስፋ አደርጋለሁ። ይህ የእኔ የተሳታፊ-ታዛቢ (Participant Observer )ትውስታም ለጥናታቸው እንደ አንድ ግብዓት ይጠቅማል።

ዛሬ ላይ የኦሮሞ ሕዝብ በልጆቹ መሥዋዕትነት ለአሥርት ዓመታት ሲታገላቸው ከነበረው ጨቋኝ አገዛዞች መገላገል ቢችልም፡ ከራሱ አብራክ በወጣ እምባገነናዊ ሥርዓት ስር መውደቁ ግን "ላም እሳት ወለደች። እንደሚባለው ሆኖበታል። በአንድ ወገን ትናንት ሌሎች ላይ

እንዳደረገው አምፆ እንዳያስወግደው ትንሸሻም ብትሆን ያገኘኋትን ለውጥ እጥቼ ወደ ትናንቱ መድሏዊ አገዛዝ እመለሳለሁ ብሎ ይሥጋል። በሌላ ጎን ደግሞ ልጆቹ ሥልጣን ይዘዋልና መከራዩ እብቅቶለታል ብሎ ተደላድሎሎ እንዳይቀመጥ በመንግሥት የሚደርስበት በደል እና ዕፅቃይ ቀዋሉበታል። ከዚህ በመነሳት ባለፉት ስድስት ዓመታት በኦሮሞ ውስጥ ሁለት ተቃራኒ ሐሳቦች ተፈጥረዋል።

በአንድ ወንን የቀድሞው አገዛዝ ተወግዶ አሁን በሥልጣን ላይ በሚገኘው የኦሮሞ እንጃ መተካቱ ትልቅ ድል እንደሆነና እሱ ላይ ማመጽ በረዥም እና እልህ አስጨራሽ ትግል የተገኘውን ሀገር የመምራት ዕድል ያሳጣል የሚሉ አሉ። ይህንን ሐሳብ የሚያራምዱት የኦህዴድ አባላት ብቻ ሳይሆኑትላንት ለረዥም ዓመታት በተቃውሞ ሲታገሉ እና መስዋዕትነት ሲክፍሉ የነበሩ ይገኙበታል። በሌላ ወገን ደግሞ ምንም እንኳን በብሔር ኦሮሞ የሆኑ ግለሰቦችና ቡድኖች ሥልጣን ቢይዙም፣ ድሮ በሕዝባችን ላይ ሲደርስ የነበረው መንግሥታዊ በደል አሁንም ተባብሶ ቀጥሏል። ይህን በደል ትላንት ትዕዛዝ ተቀብሉ ሲያስፈጽም የነበረው፣ ዛሬ ደግሞ በራሱ ተነሳሽነት ያስቀጠለው አሁን ሥልጣን ለይ ያለው ስብስብ ስለሆነ ምንም ለውጥ የለም፣ ዕለዚህም ልክ እንደ ቀደሙት አገዛዞች በትግል ማስወገድ አለብን የሚል ነው። በዚህ አመለካከት በመነሳት በሺዎች የሚቆጠሩ ወጣቶች ነፍጥ እንግበው በትጥቅ ትግል ላይ ተስማርተዋል።

ይህን የሐሳብ ክፍፍል የኦሮሞ ፖለቲካ ከዚህ በፊት አስተናግዶት ስለማያውቅ በሕዝቡ ውስጥ ስፊ ብዥታን ፈጥሯል። ትልቅ ቁጥር ያላቸው የኦሮሞ ልሂቃን ከዚህ በፊት የነበሩትን አገዛዞች ሲያገለግሉ የነበረ ቢሆንም፣ “እኔ መንግሥት ነው። የሚል ሐሳብ በኦሮሞ የፖለቲካ ትርክት ውስጥ አልነበረም። ዛሬ ግን ይህ ሐሳብ በገሚሱ የኦሮሞ ልሂቃን እና ማኅበረሰብ ክፍል ይንጸባረቃል። ኦሮሞ ያልሆኑ የፖለቲካ ቡድኖች አገዛዙን "የኦሮሞ መንግሥት" በማለት የሚያራምዱት የጅምላ ፍረጃም በመጠቃትና እራስን ከመከላከል ስሜት የተነሳ ብዙው ኦሮሞ ይህን አመለካከት ወደመቀበል እንዲያዘነብል እየገፋፋ ይገኛል። በተቃውሞ የቀጠለው የኦሮሞ ልሂቅ ደግሞ፣ አገዛዙ የኦሮሞ አለመሆኑን ለማሳመን ሲጥር ይታያል። እንደ ማሳመኛም ገዢው ቡድን የትላንቱ አምባገነናዊ አገሃዛዝ አካል የሆነ፣ከጅምሩም የኦሮሞን ሕዝብ ለመጨቆኛ የተቋቋመ መሆኑን ይከራከራል። አንዳንዶች እንዲያውም የአገዛዙን ባላሥልጣነት ኦሮሞነት ጥያቄ ውስጥ እስከማስገባት ይሄዳሉ።

እንደኔ አመለካከት ለአገዛዙ ደጋፊዎችም ሆኑ ተቃዋሚዎች “የኦሮሞ መንግሥት"የሚባለውን ጉዳይ በጥንቃቄ ማጤን ያስፈልጋል። በተጨባጭ አሁን ያለው አገዛዝ ከአንድ ብሔር ቡድናዊ አስራር ይልቅ በአንድ ግለስብ አመለካከትና ፍላጎት የበላይነት የሚመራ ስለሆነ፣ እንዳንዶች የሚጠቀሙት ዐቢይ መንግሥት" የሚለው ምናለባት የተሻለ ይገልፀዋል። ስለሆነም የእዝዙ ቁንጮ የኦሮሞ ብሔር ተወላጅ ስለሆነ ብቻ "የኦሮሞን ሥልጣን ማስጠበቅ" በሚል ስበብ አምጣነናዊ ሥርዓትን ለማስቀጠል መሞከር፣ ምንም ያህል ቢዘገይ ከባድ ኪሳራ ያመጣል። በሌላ በኩል ይህ አገዛዝ እንደ ትናንቱ ሥርዓቶች ሁሉ፣ ኦሮሞ ላይ ጉዳት እያደረስ ስላለ ከራዕ እርቆ በዓድ ለማድረግ (alienating) ሲባል የመሪዎቹን የብሔር ማንነት ጥያቄ ውስጥ መክተትም ብዙ ርቀት አያስኬድም። እንዲህ አይነት አካሄድ “የኦሮሞ ክፉ የለውም” ወደሚል ግብዝነት ያመራል። የኦሮሞነት ስጪ እና ነሺነት ሚና ለመጫወት መሞከር ከዚህ በፊትም ትግሉን የጎዳ፣ ወደፊትም ሕዝቡን የሚከፋፍል አመለካከት ነው።

በተጨመሪም የዚህ አገዛዝ መሪ ኦሮሞ መሆኑና ወደ ሥልጣን የመጣውም በኦሮሞ ሕዝብ የትግል ማዕበል ስለሆነ፡ የሀገሪቷ ብሔሮችም ሆኑ የዓለም ማኅበረሰብ ሥርዓቱን እንደ"ኦሮሞ-መር መንግሥት" ይመለከቱታል። እንዳንድ የአገዛዙ ተቀናቃኞች ከሚገባው በላይ እጋንነው "የኦሮሞ መንግሥት" በማለት ለጅምላ ፍረጃ እያዋሉት ቢሆንም፣ ከቀደሞ ሥርዓቶች ጋር ሲነጻጸር የኦሮሞ ብሔር ተወላጅ የሆኑ ግለስቦች በመንግሥት ላእላይ መዋቅር ውስጥ የተሻለ ቁጥር እና ተጽዕኖ እላቸው። እንዲሁም ልክ የቀድሞዎቹ አገዛዞች የፈለቁበትን የእማራን ወይም የትግራይን ማኅበረስብ መሸሸጊያ ሲያደርጉ እንደነበረው፣ የዛሬዎቹም ኦሮሞን የሥልጣናቸው መከታ ለማድረግ ሲሞክሩ ይታያል። እነዚህን ፖሊቲካዊ እውነታዎች የመሪዎቹን ኦሮሞነት በመካድ ለንገላገላቸው እንችልም።

በሌላ በኩል ሥርዓቱን በደፈናው "የኦሮሞ መንግሥት" ብሎ መግለጽም አገዛዙ የኦሮሞን ሕዝብ ለብቻ ተጠቃሚ እድርጓል የሚል እንድምታ ይኖረዋል፣ እለፍ ሲልም በእምባገነናዊ ሥርዓቱ ውስጥ የሌላ ብሔር ተወላጆችን ተሳትፎ፣ ተጽዕኖ እና ተጠቃሚነት መካድ ይሆናል። በተጨማሪም ይህ እካሄድ ለሚፈጸሙ መንግሥታዊ በደሎች ተጠያቂነትን ከእንድ ብሔር ጋር የማስተሳሰር እዝማሚያ እንዳያስከትል በጥንቃቄ ሊጤን ይገባዋል። አንድ አገዛዝ እከሌ የሚባል ሕዝብ መንግሥት ነው ለማለት የሚቻለው፣ ያ ሕዝብ በደሞክራሲያዊ ምርጫ ውክልና ከስጠው ብቻ ነው። ስለሆነም የባለሥልጣናቱን ኦሮሞነት መካድ እንደማያስኬደው ሁሉ የሕዝብ ይሁንታ ያላቸው እድርጎ ማቅረብም ተገቢ እይሆንም። ይልቁንም ቡድኑ የሕዝብ ውክልና እንደሌለውና፣ ድርጊቱም የኦሮሞን ፍላጎት እንደማያንጸባርቅ በመግለጽ መታገል ይሻላል።

ሁለቱን ተቃራኒ ሐሳቦች የሚያስታርቀው ደሞክራሲያዊ ሥርዓት መገንባት ነው። እንደ ኦሮሞ እስካሁን የተገኘውን ድል ለማስጠበቅም ሆነ፣ በስሙ ሥልጣን ላይ ባለው ቡድን የሚደርስበትን በደል ለማስቆም ዴሞክራሲ ወሳኝ ነው። በዴሞክራሲ ውስጥ እምባንነንነትን የሚመኙግለስቦች እናቡድኖች ካልሆኑበስተቀር እንደ ኦሮሞ ያለ ስፊሕዝብ የሚያጣው ነገር የለም። የገዳ ሥርዓት እለኝ ብሎ የሚኩራራ፡ ትናንት በሌሎች ብሔሮች ስም በደል ሲያደርሱ የነበሩ እምባገነኖችን ሲኮንን የነበረ ሕዝብ፡ ዛሬ ከእብራኩ የወጡ ጨቋኞችን የሚያወድስ ከሆን የትግል ዓላማው ተዓማኒነት ጥያቄ ውስጥ ይገባል።

በተጨማሪም የኦሮሞ ሕዝብ እብላጫ ቁጥር ያለውና በሀገሪቷ እምብርት ላይ በስፊውስፍሮ ከመገኘቱ እንጻር፡ ለራሱ ጥቅም ብቻ ሳይሆን ለሁሉም የሀገሪቷ ብሔሮች መብት፣ሰላም እና ልማት ማረጋገጥ ረገድ ትልቅ ኃላፊነት እለበት። ይህን ኃላፊነት ከዳር ማድረስ የሚችለው ደግሞ የኦሮሞ ፖለቲካ ዲሞከራሲያዊ ሥርዓት መገንባትን ግብ እድርጎ ያለማወላወል መታገሉን ከቀጠለበት ነው። ብሔሮች እራሳቸውን በራሳቸው፤ ሀገሪቷን ደግሞ በጋራ የሚያስተዳድሩበትን ደሞክራሲያዊ ፌደራላዊ ሥርዓት የመገንባት ትግል ውስጥ ግንባር ቀደም ሚና መጫወቱን ከገፋበት፡የራሱን ጥቅም እስከብሮ በሌሎች ብሔሮችም ዘንድ ክብርን
ይገናጸፋል።

የፖለቲቲካ ሥልጣን አስፈላጊነት የሚካድ ጉዳይ እይደለም። ነገር ግን በአተገባብሩ ላይ ተመስስርቶ፣ ሥልጣን ጠቃሚ (asset) ውይም ጎጂ (liability) ሊሆን እንደሚችል መገንዘብ ያስፈልጋል። በብልሃት እና በተጠያቂነት መንፈስ ከተጠቀምነው፡ የህብረተስባችንን

መብትና ጥቅም ለማስጠበቅ ብሎም ከሌሎች የሚቃጣን ጥቃት ለመመከት ይረዳል። በተቃራኒው፣ መንግሥታዊ ሥልጣንን የግለሰብን ወይም የውስን ቡድንን ፍላጎት ብቻ ለማስጠበቅ ሲባል ሌሎች ማኅበረሰቦችን ባገለለ መልኩ ከተጠቀምነው፣ ውሎ ቢያድርም ለከፋ ጉዳት መጋለጥን ማስከተሉ አይቀሬ ነው።

ስለዚህ "ሥልጣንን ለማስጠበቅ" በሚል ሰበብ የአንድን ቡድን አምባገነናዊ ሥርዓት ለማስተጠል መሞክር፤ አገዛዙ በራሱ በኦሮሞ ሕዝብ ላይ ከሚያደርሰው በደል በተጨማሪ በሌሎች ብሔሮች ውስጥ የጥርጣሬ እና የጥላቻ አመለካካት እንዲጠናከር ያደርጋል። ይህንን ደግሞ፣ ከዚህ በፊት የነበሩ አገዛዞች ትተውት ካለፉት ብቻ ሳይሆን፣ በአሁኑ ዘመንም ባለፉት ጥቂት ዓመታት ውስጥ እየሆነ ያለውን እያየን እንገኛለን። ሥልጣን ላይ ባለ ቡድን የሚፈጸሙ ጥፋቶች፣ የብሔሩን ስም በጠቅላላው ለማጠልሸት ግብዓት እየሆኑ ነው። ኦሮሞ ከውስጡ በወጣ አምባገነናዊ ሥርዓት በደልን በቀጥታ ማስተናገድ ሳይበቃው፣ ሥርዓቱ ሌሎች ብሔሮች ላይ ለሚያደርሰው ጥፋት ተጠርጣሪ በመሆን በሁለት መልኩ እየተጎዳ ይገኛል። ከዚህ አስከፊ ጉዳት ለማምለጥ በዴሞክራሲ ሥርዓት ግንባታ ላይ ማተኮር ያዋጣል።

በአንድ ማኅበረሰብ ስም የሚንቀሳቀስ የፖለቲካ ቡድን ድክመትና ጥፋት ያንን ሕዝብ ለወል የሞራል ውድቀት (collective moral failure) ያጋልጣል። በመጽሐፉ ውስጥ እንደጠቀስኩት፣ በኦነግ ድርጅት ውስጥ በነበረው ችግር ምክንያት ትግሉ መዳተቱ የኦሮሞን ሕዝብ ለጥልቅ ሞራላዊ ስብራት ዳርጎት በራስ መተማመንን ነፍጎት ነበር። በቄሮ ትግል ወቅት የተገኙ ድሎች ይህንን የወል ሞራላዊ ስብራት ለመጠገን አስችለው ነበር። እሁን በኦሮሞ ስም ሥልጣን ላይ ያለው ቡድን የሚፈጽማቸው ጥፋቶች እና የሚንጸባረቁ ድክመቶች ሕዝቡን ለአዲስ የወል ሞራል ስብራት እየዳረጉት ይገኛሉ። ትላንት "ኦሮሞ ሃምሳ ሚሊዮን ሆኖ ሃምሳ ዓመት ታግሎ ምንም አላመጣም" ሲባል የነበረውን የሥነልቦና ጥቃት (psychological warfare) በቄሮ ውጤታማ ትግል ካፈረስነው በኋላ፣ ዛሬ ደግሞ በአገዛዙ ድከመቶች የተነሳ "ኦሮሞ ሀገር ማስተዳደር አልቻለም" በሚል የጅምላ ፍረጃ ዘመቻ ይስተዋላል። ዛሬ አገዛዙን የሚመሩት ግለሰቦች ትላንት ሕወሓት መራሹ ኢሕአዴግ ችሎታን (meritocracy) ሳይሆን፣ ታማኝነትን እንደ መስፈርት በመጠቀም፣ የአመራር ብቃትም ሆነ ማኅበራዊ ተቀባይነት እንደሌላቸው በማረጋገጥ የመለመላቸው ናቸው። ዐቢይም ይህንን ከሕወሓት የወረሰውን የሰው ኃይል ይዞ መቀጠል ብቻ ሳይሆን፣ ከብቃት ይልቅ ታማኝነት የምልመላ እና ሹመት ብቸኛ መስፈርት ሆኖ እንዲቀጥ አድርጓል። ይህ ስለሆነም፣ አገዛዙ የኦሮሞ ልሂቃን ብታት መለኪያ ሊሆን እንደማይችል የዘመቻው አራማጆችም የሚጠፋቸው ሃቅ አይደለም።

ይህንን የጅምላ ፍረጃ ማክሸፍ የሚቻለው የአገዛዙን ድክመት በመካድ፣ ሌለው ላይ ጣት በመቀሰር እና በፕሮፖጋንዳ እንካ ሰላንቲያ ሳይሆን፣ ልክ በትግል ወቅት እንደተደረገው በእውቀት ላይ በተመሰረተ ስትራቴጂ "ሀገርን መምራት" እንደሚቻል በተጨባጭ በማሳየት ነው። ለዚህ መነሻችን መሆን ያለበት ከግለሰባዊ ምኞት እና ቡድናዊ ፍላጎት የዘለለ አካታች ሀገራዊ ራእይ ማንገብ ነው። ኢትዮጵያ አሁን በደረሰችበት ነባራዊ እውነታ፣ አንድ ግለሰብ የሚነግስበት ወይም የተወሰነ ቡድን ብቻ የሚጠቀምበት ፖለቲካዊ ሥርዓት እንደማያዛልቅ አምኖ መቀበል ያስፈልጋል። ስለሆነም የኦሮሞን ሕዝብ መብትና ጥቅም ዘላቂነት ባለው እና አስተማማኝ በሆነ መሰረት ላይ ለማቆም፣ የሁሉንም ዜጎች እና ቡድኖች መብትና ጥቅም አመዛዝኖና ኢቻችሎ ሊያቅፍ የሚችል ፖለቲካዊ ሥርዓት መገንባት የማያወላዳ አቋማችን ሊሆን ይገባል።

የኦሮሞ ሕዝብ በኢትዮጵያ ዴሞክራሲያዊ ሥርዓትን በማስፈን ትግል ውስጥ የሚጠበቅበትን ከፍተኛ ኃላፊነት መወጣት የሚችለው ከተቀረው የሀገራችን ሕዝቦች ጋራ ተባብሮ እና ተናብቦ በመስራት ነው። ለዚህደግሞትላንት ለትግል የረዳው የኦሮሞ ብሔርተኝነት ዛሬ ላይ አምባገነናዊ ሥርዓትን ለማደላደል መጠቀሚያ እንዳይሆን ጥንቃቄ ማድረግ ያስፈልጋል። አምባገነኖች ከሌሎች ብሔሮች አመጽ ሲነሳባቸው ራሳቸውን ለማዳን የሚሞክሩት የወጡበትን ሕዝ ብሔርተኝነት በማቀንቀን ነው። ይህ ደግሞ ሁሉንም ሕዝብ በጋራ የሚጎዳውን የአምባገነና አገዛዝ ዕድሜ ከማራዘም አልፎ፣ ሕዝቡ ከሌሎች ብሔሮች ጋር ያለውን ማኅበራዊ ትስስ በማሻከር ከሥርዓቱ ውድቀት በኋላ ለሚቆይ የተራዘመ የእርስ በእርስ ጦርነት ሊያጋልጠወ ይችላል። ስለዚህ የትኛውም አምባገነን ብሔርተኝነትን እንደ ሽፋን ተጠቅሞ ሌሎች ብሔሮች እንዳይጎዳ የኦሮሞ ሕዝብ በንቃት መጠበቅ አለበት።

እትዮጵያን አሁን ከገባችበት ቀውስ አውጥቶ ወደ ዴሞክራሲ የሚያሸጋግር ጎዳና የመመለ ኃላፊነት ለኦሮሞ ብቻ የሚተው አይደለም። የአሁኑ አገዛዝ በኦሮሞ ትግል ወደ ሥልጣን የወጣ ቢሆንም፣ ሽግግሩን ቀልብሶ ሥልጣኑን እንዲያደላድል የሁሉም ማኅበረሰብ ልሂቃን ሚ ነበረበት። ለሽግግሩ ከሃዲድ መውጣት ዋናውን ሚና የተጫወተው ሹፌሩ ቢሆንም፣ በለው ማግስት የሀገሪቷ የፖለቲካ ማኅበረሰብ በተቀናጀ መልኩ ቢረባረብ ኖሮ የለውጥ ቅልበሳው በመከላከል ዴሞክራሲያዊ ሽግግሩን የማሳካት ዕድል ይኖር ነበር። በወቅቱ የተለያዩ የልሂቃ ቡድኖች የነበራቸውን አቋም መለስ ብዬ ሳይ ዕድሉ እንዲያመልጠን ሚና እንደተጫወ ይታየኛል።

ለምሳሌ ለ27 ዓመታት የፌደራል ሥልጣን በበላይነት ተቆጣጥሮ የነበረው የትግራ ልሂቅ የፖለቲካ ማዕከሉን ሙሉ በሙሉ ለቆ ወደ መቀሌ በመገለል የሩቅ-ተቺ ሆነ ትችቱን እያከረረ በሄደ ቁጥር፣ ማዕከላዊውን ሥልጣን የተቆጣጠረው ቡድን፣ ሕወሓት ከፖለቲካ ተቀናቃኝነት ይልቅ የጸጥታ ሥጋት እንደሆነ በመፈረጅ የጦረኝነት ፖለቲካ (securitized politics) በማስፈን የፖሊቲካ ምህዳሩን ለማጥበብ እንደምክንያ ተጠቀመበት። የኦሮሞው ልሂቅ በበኩሉ አብዛኛው በድል አድራጊነት ደስታ ተውጦ ገሚ ደግሞ ለውጥ መምጣቱን ራሱ ባለማመን፣ ከትግል ሥነልቦና ወደ አሥተዳደራዊ ኃላፊነ በፍጥነት መሸጋገር ባለመቻሉ፣ ሥልጣን ላይ ያወጣውን ቡድን ልጓም ይዞ ሽግግሩን ፈ ለማስያዝ የነበረውን ዕድል አባከነ። በተለይ ከረዥም ዓመታት እና ሰፊ መስዋዕትነት በኃ የተገኘን ሥልጣን ላለማጣት በመሳሳት፣ ለዘላቂ ለውጥ ከሌሎች ወገኖች ጋር የመተባበር አስፈላጊነት ዘንግቶ ሀገሪቷን ወደ ዴሞክራሲ ለማሸጋገር የነበረው ዕድል እንዲባክን ሆነ እንዲያውም የተወሰነው ልሂቅ "የኦሮሞን ሥልጣን ማስጠበቅ" በሚል አስተሳሰብ አፍጥ፡ እየመጣ ለነበረው አዲስ አምባገነናዊ ሂደት አስቻይ ሆኖ ተሰለፈ። የአማራው ወገን ደግሞ የብሔር ፖለቲካን በሚኮንን እና የቀድሞ ዘመን ከፍታን እንመልሳለን በሚለው ዲስኩር ተ አድርጎ ከአዲሱ አገዛዝ ጋር ቆመ። በተለይ ለሕወሓት እና ኦነግ ከነበረው የረዥም ጊዜ ጥሃ በመነሳት፣ አዲሱ አገዛዝ በሁለቱ ኃይሎች ላይ የጀመረውን ዘመቻ ከመደገፍ አልፎ የሁለ ክልሎች የፖለቲካ ልሂቃን እንዲወገዱ አበክሮ ሰራ፤ ለፖለቲካ ምህዳሩ መጥበብ ኋላ ላይ ለእርስ በእርስ ጦርነቱ መነሳት ቀጥተኛ ሚና ተጫወተ።

ዛሬ ላይ ቆመን መለስ ብለን ስናይ፣ የትግራይ ልሂቅ እንዳሰበው መቀሌን እንደምሽግ ተጠቅፃ እራሱን መከላከል አልቻለም፣ ክልሉን እና ሕዝቡን ለከፋ እልቂት እና ውድመት አጋለጠው።

የኦሮሞው ልሂቅም የሳሳለትን ሥልጣን ማደላደል ቀርቶ ወደ አርስ በእርስ ጦርነት ገብቶ ኦሮሚያን በቀደምት አገዛዝ ወቅት እንኳ ታይቶ ለማይታወቅ እልቂት ዳረገ። የአማራው ልሂቅም እንዲሁ ቃል የተገባለት የብሔር ፖለቲካን በማጥፋት የቀድሞዋን ታላቋን አሃዳዊት ኢትዮጵያ እውን የማድረግ ሕልም ከሽፎ፣ ትላንት ሲጸየፈው የነበረውን ብሔርተኝነት አንግቦ ሥልጣኑን ባደላደለለት አገዛዝ ላይ እምጿል። ክልሉም ወደ አሳዛኝ ጦርነት እና ሥርዓት አልበኝነት ገብቷል። እነዚህ ሦስት የልሂቃን ቡድኖች ቀድሞ የነበራቸውን ቁርሾ ረገብ አድርገው፣ ጊዜያዊ የአሸናፊ ተሸናፊ ሥነ ልቦናዎችን ተቋቁመው፣ ሀገሪቷን ወደ ዴሞክራሲ ለማሸጋገር ቢተባበሩ ኖሮ፣ አዲስ ሥልጣን የያዘው አገዛዝ ምንም ያህል አምባገነን የመሆን ፍላጎት እና እቅድ ቢኖረውም ሊሳካለት እንደማይችል አስባለሁ። ሆኖም ግን ከሁሉም ወገን የነበርን ልሂቃን የዴሞክራሲ ሽግግርን ለማሳካት በእውቀት፣ በልምድ፣ በድርጅታዊ መዋቅር እንዲሁም በሥነልቦና ዝግጁ ስላልነበርን ዕድሉን መጠቀም አልቻልንም።

ባለፉት ዓመታት በሁሉም ወገን የተፈጸሙ ስሕተቶች ከከተቱን ፖለቲካዊ እና ኢኮኖሚያዊ ቀውስ እንጻር ኢትዮጵያ እስካሁን እንደሀገር መቀጠሏ ተዓምር ያስብላል። ጎረቤታችን ሱዳን ከእኛ በብዙ መልኩ ባነሰ ቀውስ ምክንያት ምስቅልቅሏ መውጣቱን ላየ እድለኛ መሆናችንን ይረዳል።፣ ሀገረ-መንግሥት አንዴ ከፈረሰ መልሶ መገንባት ምን ያህል አዳጋች እንደሆነ በቅርባችን ከተከስቱት ሶማሊያ፣ ሊቢያ፣ የመን እና ሱዳን መማር አስፈላጊ ነው። የትግራይ ጦርነት ቆሞ ካንዣበበው ደመና ተንፈስ ብንልም፣ አሁንም ቢሆን ከመፍረስ አደጋ አልወጣንም። እየተካሄዱ ያሉ ግጭቶች ቆመው፡ በፖለቲካችን ላይ ሀገራዊ መስማማት ተደርሶ፣ ኢኮኖሚው እንዲያገግም ካልተደረገ ሀገረ-መንግሥቱ እየተዳከመ መሄዱን ይቀጥላል።

“ያልገደለህ መርዝ መድኃኒት ይሆንሃል” እንደሚባለው ሁሉ፣ ባለፉት ዓመታት ከፈጸምናቸው ስሕተቶች በአግባቡ ከተማርን፣ ለሚቀጥለው ዘመን ፖለቲካችንን ለማቃናት ጥሩ ልምድ ሊሆኑን ይችላሉ። አብይ ልሂቃን ቡድኖች እንወክለዋለን የሚሉትን ቡድን ጥቅም ለማስጠበቅ በተናጠል የሚያደርጉት እንቅስቃሴ ጊዜያዊ ድል ቢያጎናጽፍም ዘላቂ መፍትሔ እንዳለመጣ አምነን መቀበል ነው። አሁን የኢትዮጵያ ሕዝቦች ከደረሱበት የፖለቲካ በተለይም የብሔር ንቃተ ኅሊና አንጻር የማንኛውንም ቡድን የበላይነት አስፍና ሊቀጥል የሚችል አገዛዝ ፈጽሞ ሊቀበል አይችልም። የማዕከሉ ፖለቲካ ሳይስተካከል ክልሎች የተረጋጋ ፖለቲካ ሊኖራቸው እንደማይችል ከጦርነት በኋላ ትግራይ ውስጥ እየተስተዋለ ያለው የክልሉ ልሂቃን ሽኩቻ ጥሩ ማሳያ ነው። የማዕከሉን ፖለቲካ ማስተካከል የሚቻለው ደግሞ በአንድ ግለሰብ ወይም ቡድን ራእይ እና በጎነት ሳይሆን፣ ሁሉን አካታች በሆነ ድርድር እና ምክክር ብቻ እንደሆነ ከዐቢይ የስድስት ዓመታት ሙከራ እና ካስከተለው ቀውስ መረዳት እንችላለን።

የኢትዮጵያ ሀገረ-መንግሥት የተመሰረተበት ሂደት እና አሁንም የሚመራበት መንገድ እልቂት: መድሎ እና ጭቆና የነበረበት መሆኑ የሚካድ ባይሆንም፣ የማዕከሉን ፖለቲካ በማስተካከል ሥርዓተ መንግሥቱን ከማስቀጠል የተሻለ አማራጭ እንደሌለ ባለፉት አሥርት ዓመታት እንደ መፍትሔ ከተተገበሩ ሙከራዎች መማር አለበን። በዘመናዊ የኢትዮጵያ ሀገረ-መንግሥት ምስረታ ጦርነቶች መጨረሻ ላይ የበላይነት ያገኘው የአማራ ልሂቅ፣ ተሸናፊ የነበሩ ብሔሮችን በመጨፍለቅ፣ በራሱ ማንነት የተሳለ ውህድ እና እሃዳዊ ሥርዓት ለመገንባት ያደረገው ጥረት፣ ከታለመው በተቃራኒ የብሔር መነቃቃትን ወልዶ፣ የሀገረ-መንግሥት ግንባታ ሂደቱን ወደ ቀውስ መርቶታል።

በአሃዳዊው የኢትዮጵያ ማዕከላዊ አገዛዝ የተከፉ ቡድኖች አንዳንዶቹ በመገንጠል፣ ሌሎቹ ደግሞ ማዕከሉን በበላይነት መቆጣጠር እንወክለዋለን የሚሉትን ሕዝብ ለአንዴና ለመጨረሻ ጊዜ ከችግር ለመገላገል ሞክረዋል። ለምሳሌ የኤርትራ ኃይሎች የኢትዮጵያ ማዕከላዊ መንግሥት አካሄድን በመቃወም ከረዥም እና ደም አፋሳሽ ጦርነት በኋላ ነጻ ሀገር መሰረቱ። ሆኖም ከሠላሳ ዓመታት በኋላም ለቀጠለው ኢኮኖሚያዊ መቀጨጭ እና የደህንነት አደጋ የኢትዮጵያን ማዕከላዊ መንግሥት ሲወቅሱ እናያለን። በሌላ ወገን ደግሞ ሕወሓት የደርግን አገዛዝ ገርስሶ የማዕከላዊ መንግሥት ሥልጣንን በበላይነት መቆጣጠርን ለትግራይ ሕዝና ችግር እንደመፍትሔ ለማቅረብ ቢሞክርም፣ ከ27 ዓመት በኋላ ኢትዮጵያንም የትግራይ ሕዝብንም ወደከፋ ሁኔታ የከተተ ነው። አሁን ሥልጣን ላይ ያለው አገዛዝ በሕወሓት ዘመን የነበረውን በአንድ ፓርቲ የበላይነት የሚመራ አምባገነንነት በግለሰብ የበላይነት በመተካት ለመቀጠል ያደረገው ሙከራም በስሙ ሥልጣን የያዘውን የኦሮሞ ሕዝብም ሆነ ኢትዮጵያን ወደ ባሰ ቀውስ ያስገባ ነው።

መገንጠልም ሆነ ማዕከሉን በበላይነት ለመያዝ መሞከር መፍትሔ ያልሆነው፣ ከኢትዮጵያ ሀገረ-መንግሥት አመሰራረት እና አድገት ከመነጨ ሁለት ባሕሪያት የተነሳ ነው። አንደኛው ባሕሪይ የሀገረመንግሥቱ ግንባታ ሂደት ከፍተኛ ሃብትና ጉልበት በማዕከል እንዲከማች ያደረገ መሆኑ ነው። ከዚህ የተነሳ ተበደልኩ ያለ አንድ የሀገሪቱ ክፍል ቢገነጠልም እንኳ በማዕከሉ ቁጥጥር ሥር በተከማቸው መዋዕለ-ንዋይ እና ገበያ ላይ ተለጣፊ (dependent) ከመሆን ስለማይላቀቅ፣ ፖለቲካዊ እንጂ ኢኮኖሚያዊ ሉዓላዊነት መጎናጸፍ አይችልም። ለዚህ ጥሩ ምሳሌ የኤርትራ ጉዳይ ሲሆን፣ የሕወሓት ቡድን ማዕከላዊ ሥልጣንን ለቆ ወደ መቀሌ ከሄደ በኋላ የገጠመው ፈተናም ሌላ ማሳያ ነው። ሁለተኛው ደግሞ፣ የኢትዮጵያ ሀገረ- መንግሥት ቁጥራቸው ትልልቅ ከሆነ እና ማንነታዊ ንቃተ-ኅሊናቸው ከጊዜ ወደጊዜ እየዳበረ ከሄደ ሕዝቦች የተገነባ በመሆኑ አንድ ወገን ማዕከላዊ ሥልጣንን በበላይነት በመያዝ ሌላውን አፍኖ ለማስተዳደር በሞክረ ቁጥር፣ መገለል የተሰማቸው ቡድኖች በማደራጀት እና በማሳመጽ የአገዛዙን ዕድሜ ማሳጠር የሚያስችል አመቺ ሁኔታ ስላለ ነው።

እስካሁን የተሞከሩት ከኢትዮጵያ ማዕከላዊ መንግሥት መገንጠል ወይም በበላይነት በመያዝ የአንድን ወገን ጥቅም በዘላቂነት ማሰጠበቅ እንደማይቻል ከተረዳን፣ ያልተሞከረውን ብንሞክር አይሻልምን? ያልተሞከረው የሁሉንም ሕዝቦች መብትና ጥቅም የሚያስከብር ዴሞክራሲያው ሥርዓት መገንባት ነው። እኔም በተቀረው ዕድሜዬ ፍትሃዊ እኩልነትን ከተፋጠነ ልማት አጣምሮ ሊያስኬድ የሚችል የፖለቲካ ሥርዓት በሀገራችን እንዲመሰረት ባለኝ እውቀ ጉልበትና ተሰሚነት እተጋለሁ።